# አማርኛ ፡ ቅኔ ፡

## ከነመፍቻው ።

ተሻሽሎና ፡ ታክሎበት ፡ የተሰናዳ ።

(ሁለተኛ ፡ እትም) ፡



ከባላምባራስ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ፡ ወልደ ፡ መስቀል ፡

ለትምህርት ፡ እንዲያገለግል ፡

ተዘጋጀ ።

አዲስ ፡ አበባ ፡ በ፲፱፻፶፰ ፡ ዓመተ ፡ ምሕረት ፡

በብርሃንና ሰላም ማተሚያ ቤት ታተመ

ተኀትመ ፡ ዝንቱ ፡ መጽሐፍ ፡ አመ ፡ ፴ ፡ ወ ፫
ዓመተ ፡ መንግሥቱ ፡ ለቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡
ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ።



ግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡
ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ዘኢትዮጵያ ።

# መግለጫ ።

«አማርኛ ፡ ቅኔ» ፡ የተባሉትን ፡ መጽሐፎቼን ፡ ለማዘጋጀት ፡ ያሳሰበኝና ፡ ያነሣሣኝ ፡ ምክንያት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዐላማውን ፡ ጭ ምር ፡ ዘርዝሬ ፡ በሰፊው ፡ በየመግቢያቸው ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ገለጥሁ ፡ አሁን ፡ ደግሞ ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ከዚህ ፡ በፊት ፡ የተባለውን ፡ መ ልሶ ፡ ማግባት ፡ አስፈላጊ ፡ መስሎ ፡ ስላልታየኝ ፡ በመግቢያ ፡ ስም ፡ የሚጻፈውን ፡ ትቼዋለሁ ። ስለዚህም ፡ ቀጥዬ ፡ ልናገር ፡ የምፈልገው ፡ ስለ ፡ መፍቻው ፡ አገላለጥ ፡ ያለኝን ፡ ሐሳብ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ይህነንም ፡ ካስገነዘብኩ ፡ በኋላ ፡ ባንደኛውና ፡ በሁለተኛው ፡ እትም ፡ ያማርኛ ፡ ቅኔ ፡ መጻሕፍት ፡ መግቢያ ፡ ላይ ፡ ሰጥቼ ፡ በነበ ረው ፡ ቃል ፡ መሠረት ፡ ለምስጢሩ ፡ መፍቻ ፡ የሆነውን ፡ መጽሐፍ ፡ አዘጋጅቼ ፡ እንሆ ፡ አቅርቢያለሁ ።

ይህ ፡ ያማርኛ ፡ ቅኔ ፡ መፍቻ ፡ በቶሎ ፡ ተጠናቆ ፡ ባገልግሎት ፡ ላይ ፡ እንዲውል ፡ ለማድረግ ፡ ሐሳቤ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፤ በጊዜ ፡ ማጣት ፡ ምክ ንያት ፡ እስካሁን ፡ በመዘግየቱ ፡ አዝናለሁ ።

የሰው ፡ ሥራ ፡ ከስሕተት ፡ የራቀ ፡ ባይሆንም ፡ ቅሉ ፥ በበኩሌ ፡ የተቻለኝን ፡ ያኽል ፡ ደክሜ ፡ ጎሊናዬ ፡ እንደማይወቅሠኝ ፡ አድርጌ ፡ አዘጋጅቻለሁ ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ ስለ ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ከአንባቢዎች ፡ በየጊዜው ፡ ይደርሰኝ ፡ የነበረው ፡ ጥያቄ ፡ መፍቻው ፡ ተጠናቆ ፡ ባለመድረሱና ፡ አጥጋቢ ፡ መልስ ፡ ለመስጠት ፡ ባለመቻሌ ፡ መንፈሴን ፡ ያስጨንቀው ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ ልገልጸው ፡ እወዳለሁ ። እንዲሁም ፡ አንዳንድ ፡ ተማሪ ዎች ፡ መፍቻው ፡ ፈጥኖ ፡ ቢወጣ ፡ ኖሮ ፡ አናስቸግርም ፡ ነበር ፡ በማ ለት ፡ እየመጡ ፡ ማብራሪያ ፡ እንድሰጣቸው ፡ የጠየቁኝም ፡ እንደ ፡ ነበሩ ፡ አስታውሳለሁ ።

የሁሉም ፡ ችግር ፡ አንድ ፡ ዐይነት ፡ መሆኑን ፡ በጥያቄያቸው ፡ ለመረዳት ፡ ችያለሁ ። ይህነንም ፡ የሚፈጥረው ፡ በግጥሙ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ኅብረ ፡ ቃል ፡ ባገርና ፡ በሰው ፡ ስም ፤ እንዲሁም ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ ድርጊት ፡ ውስጥ ፡ ተሸፍኖ ፡ ምስጢሩ ፡ ተሰውሮና ፡ ተሸንቅሮ ፡ በመገኘቱ ፡ ነው ። እውነትም ፡ የያንዳንዱ ፡ ግጥም ፡ የኅብር ፡ ስሜት ፤ ባልተለመደና ፡ እንግዳ ፡ በሆነ ፡ ቃል ፡ ላይ ፡ ሲመሠረት ፥ ምስጢሩን ፡ ከደራሲውና ፡ ታሪኩን ፡ ቀደም ፡ ብለው ፡ ከሚያውቁት ፡ በቀር ፡ ማ

ንም ፡ ሰው ፡ በቀላሉ ፡ ሊረዳውና ፡ ሊፈታው ፡ አይችልም ። ነገሩ ፡ ይጠናል ፤ ፍቺውንም ፡ ማግኘት ፡ ያስቸግራል ።

ለምሳሌ ፤ 1 ኰሉን ፡ ተኳኰለን ፡ አልዋልን ፡ እቤታችን ፤
በምን ፡ አማራቸው ፡ ዐቢራው ፡ መልካችን ።

ሠ ፡ ዐቢራ ፡ የለበሰው ፡ የተጐሳቈለው ፡ መልካችን ፡ በምን ፡ አማራቸው ።

ወ ፡ ዐቢራ ፡ መልካ ፡ የሚባለውን ፡ መሬታችንን ፡ ምን ፡ ቢያስቡ ፡ ሊነጥቁን ፡ ተመኙ ።

2 ምነው ፡ ትፈራለህ ፡ ወንዱ ፡ ልጅ ፡ በሌቱ ፡
አለፋና ፡ ስሄድ ፡ እኔ ፡ እንኳ ፡ ሴቲቱ ።

ሠ ፡ አለፋና ፡ አለመብራት ፡ እኔ ፡ እንኳ ፡ ሴቷ ፡ በጨለማ ፡ ስሄድ ፡ አንተ ፡ ወንዱ ፡ እንዴት ፡ ትፈራለህ ።

ወ ፡ አለፋ ፡ እሚባለው ፡ ቦታ ፡ ስሄድ ፡ ና ፡ ተከተለኝ ፡ እዚያ ፡ ድረስ ፡ እንገናኝ ።

3 አይሮፕላናችን ፡ ከሄደ ፡ ዘገየ ፤
የያዘውን ፡ ዕቃ ፡ ጥሎስ ፡ እንደሁ ፡ ማየ ።

ሠ ፡ ማ ፡ አየ ፡ ወይም ፡ ማን ፡ አየ ፡ ብሎ ፡ ጥያቄ ፡ ማቅረብ ።

ወ ፡ ማየ ፡ (Maillet) የሰው ፡ ስም ።

4 ምንም ፡ ብንጐመዥ ፡ ለመቍረጥ ፡ ብንጓጓ ።
እንዴት ፡ ይጣፍጣል ፡ ያላዋዜ ፡ ሥጋ ።

ሠ ፡ ያለአዋዜ ፡ ያለድልኽ ፡ ያለድቍስ ፡ ያለአፍርንጅ ፡ ሥጋን ፡ መብላት ፡ ምን ፡ ያስደስታል ።

ወ ፡ አልዋዜ ፤ (Aloisi) የሚባለውን ፡ ጠላት ፡ ሰውነቱን ፡ ሥጋውን ፡ በመቈራረጥ ፡ መግደል ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።

5 ቈስን ፡ ናት ፡ ወይ ፡ ዲያቆን ፡ የኛ ፡ እመቤታችን ፡
ባርካ ፡ ተናኘ ፡ ወርቅ ፡ ይኸው ፡ አሳየችን ።

ሠ ፡ በመስቀል ፡ አማትባ ፡ ባርካ ፡ አሳየችን ።

ወ ፡ ጠላት ፡ በጣና ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ያሰጠመውን ፡ ባርካ ፡ (Barca) ጀልባ ፡ አስወጥታ ፡ አሳየችን ።

እያንዳንዱ ፡ ቅኔ ፡ የተወሳሰበና ፡ የተጠላለፈ ፡ አስደናቂ ፡ ምስጢርን ፡ የያዘ ፡ ሆኖ ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ መልክ ፡ የቀረበ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ፍችውን ፡ ስሰጥ ፡ በደራስያኑ ፡ አእምሮ ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ ትክክለኛውን ፡ ስሜትና ፡ ሐሳብ ፡ ለይቶ ፡ ዐውቆ ፡ ይኸ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ ለመናገር ፡ አስቸጋሪ ፡ ቢሆንም ፡ በመጽሐፉ ፡ ውስጥ ፡ የሚገኙትን ፡ ግጥሞች ፡ ሁሉ ፡ በጠቅላላው ፡ ሠምና ፡ ወርቅ ፡ በማለት ፡ እየለየሁ ፡ በሁለት ፡ መደብ ፡ ከፍዬ ፡ አንባቢዎች ፡ በቀላሉ ፡ ለመረዳት ፡ እንዲችሉ ፡ አድርጊያለሁ ።

እንደ ፡ እውነቱ ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ ስለያንዳንዱ ፡ አማርኛ ፡ ግጥም ፡ ዝርዝር ፡ ሁናቴውን ፡ በበለጠ ፡ ጠልቆ ፡ ለመረዳት ፡ በዘርፎቹና ፡ በቅርንጫፎቹ ፡ ቍጥር ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ መልክ ፡ ምስጢሮቹ ፡ ተሸፍነውና ፡ ተሰውረው ፡ የሚገኙበትን ፡ የስልቶቹን ፡ ብዛት ፡ መግለጡ ፡ ጠቃሚ ፡ በሆነ ፡ ነበር ። ዳሩ ፡ ግን ፡ ሥራ ፡ ስለሚያበዛና ፡ ሐተታ ፡ ስለሚጨምር ፡ አልፈዋለሁ ። መቼም ፡ ሠምና ፡ ወርቅ ፡ ሲባል ፡ በአማርኛም ፡ ሆነ ፡ በግእዝ ፡ ቅኔ ፡ ብዙ ፡ መንገድ ፡ እንዳለው ፡ የታወቀ ፡ ነው ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ግን ፡ ጥቂት ፡ የሠምና ፡ ወርቅ ፡ መንገድ ፡ ሲገኝበት ፡ የሚበዛው ፡ ኅብር ፡ ቅኔ ፡ ነው ።

የሆነ ፡ ሆኖ ፡ አሁን ፡ ሠም ፡ የምንለው ፡ ቃል ፡ የደረሰው ፡ እውነተኛ ፡ ሐሳብና ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ ተሸፍኖበት ፡ የምስጢሩ ፡ መጋረጃ ፡ ሆኖ ፡ በመገርመሪያ ፡ ለአእምሯችን ፡ የሚሰማው ፡ ፍች ፡ ሲሆን ፡ ወርቅ ፡ ተብሎ ፡ የሚጠራው ፡ ደግሞ ፡ አንድ ፡ ቃልን ፡ በማጥበቅ ፡ ወይም ፡ በማላላት ፡ አጠገቡ ፡ ካለው ፡ ከሌላው ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ በማያያዝ ፡ በላንቃ ፡ በድምፅና ፡ በንግግር ፡ ዜማ ፡ ያለውን ፡ ስልት ፡ በመመርመር ፡ የሚገኘው ፡ ሁለተኛው ፡ ምስጢር ፡ ነው ።

ለማስረጃም ፡ ያኽል ፡ ቀጥሎ ፡ ያለውን ፡ ምሳሌ ፡ መመልከት ፡ ይረዳል ።

1 አገውን ፡ በቍርበት ፡ ጐገርምን ፡ በከብት ፡ (በማጥበቅና ፡ በማላላት ፡
በመላ ፡ ፈጃቸው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሳይሞት ። ሁለት ፡ ፍች ፡ የሚሰጥ) ።

2 አዳራሹ ፡ ሰፊ ፡ በሩ ፡ አልጠበባችሁ ፡
በተራ ፡ በተራ ፡ (በተራበ ፡ ተራ) ፡ ምነው ፡ (አንዱን ፡ ቃል ፡ ካንዱ ፡ በማያ
መግባታችሁ ። ያዝ ፡ ሁለት ፡ ፍች ፡ የሚሰጥ) ።

3 በታንኳ ፡ በመርከብ ፡ ሲገቡ ፡ ብታይ ፡ (በላንቃ ፡ ልዩ ፡ አነባበብና ፡ ድምፅ ፡
እረ ፡ አባይን ፡ በግር ፡ ትገባለህ ፡ ወይ ። በመስጠት ፡ ሁለት ፡ ፍች ፡ ያለው) ።

አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ደግሞ ፡ ታሪኩ ፡ ካልታወቀ ፡ በቀር ፡ በማውጣት ፡ በማውረድ ፡ በመመርመር ፡ ብቻ ፡ ግጥሞቹ ፡ ሊፈቱ ፡ ባለመቻላቸው ፡ ነገሩ ፡ ለተመልካች ፡ በጣም ፡ ረቆ ፡ እንዳያስቸግር ፡ በማሰብ ፡ አስፈላጊ ፡ መስሎ ፡ በታየኝ ፡ ቦታ ፡ በየገጹ ፡ ግርጌ ፡ አጫጭር ፡ መግለጫዎች ፡ እንዲገኙ ፡ አድርጊያለሁ ።

በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ ጣም ፡ ያላቸው ፡ ጥልቅ ፡ የሆኑ ፡ ስሜትንና ፡ ምስጢርን ፡ የያዙ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መንፈሳዊና ፡ ሥጋዊ ፡ ምክሮች ፡ ይገኛሉ ። አንባቢ ፡ ማንኛውንም ፡ ገጽ ፡ ገለጥ ፡ አድርጎ ፡ በተመለከተው ፡ ቍጥር ፡ ከሐዘን ፡ የሚያጽናና ፡ ከብስጭት ፡ የሚመ

ልስ ፣ ትዕግሥትን ፡ የሚሰጥ ፡ የሰውን ፡ ግብዝነትና ፡ ከንቱነት ፡ የሚያስረዳ ፣ ነገረ ፡ ሠሪነት ፡ የሚጐዳ ፡ እንጂ ፡ የሚጠቅም ፡ ባሕርይ ፡ አለመሆኑን ፣ ነገር ፡ ማዋሸክ ፣ ወሬ ፡ መለቃቀም ፡ በስብቀትና ፡ በሐሜት ፡ ሰውን ፡ መጕዳት ፡ ተንኰል ፡ መሥራት ፡ ለዕለት ፡ ደስ ፡ ቢል ፡ ውሎ ፡ አድሮ ፡ ኅሊናን ፡ መውቀሡ ፡ የማይቀር ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሚያስገነዝብ ፣ ለክብር ፡ መቸኰልና ፡ የያዙትን ፡ በጅ ፡ ያለውን ፡ ማቃለል ፡ የማይገባ ፡ መሆኑን ፡ የሚያስረዳ ፣ ሰውን ፡ የሚያነሣውና ፡ የሚጥለው ፡ ጊዜ ፡ መሆኑን ፡ የሚገልጥ ፣ አንድ ፡ ቀን ፡ የተደሰቱ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ ሐዘንተኞች ፡ መሆናቸውን ፡ የሚያሳውቅ ፣ እግዚአብሔርን ፡ አለመፍራትና ፡ ለበላይ ፡ አለመታዘዝ ፡ በምድርም ፡ ሆነ ፡ በሰማይ ፡ ፍርድንና ፡ ቅጣትን ፡ እንደሚያስከትል ፡ አጕልቶ ፡ የሚያሳይ ፣ በሰው ፡ ላይ ፡ ስለሚደርሰው ፡ ጕዳት ፡ በደልና ፡ ግፍ ፡ የሚናገር ፡ ያየውን ፡ ተድላና ፡ ደስታ ፡ የሠራውን ፡ ዠግንነትና ፡ ዠብዱ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያደረገለትን ፡ ቸርነት ፡ ሁሉ ፡ ጥልቅ ፡ በሆነ ፡ በኅብረ ፡ ቃል ፡ ውስጥ ፡ ተሸፍኖ ፡ ያገኛል ።

የያንዳንዱንም ፡ የግጥም ፡ ትርጉም ፡ ትክ ፡ ብለን ፡ በዐይነ ፡ ልቡና ፡ ስንመለከተው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ሊደርስ ፡ የሚችለውን ፡ ማንኛውንም ፡ ከልደት ፡ እስከ ፡ መቃብር ፡ ያለውን ፣ ለምሳሌ ፡ ማግኘት ፡ ማጣትን ፣ መከበር ፡ መዋረድን ፣ መሾም ፡ መሻርን ፣ መታመም ፡ መሞትን ፣ በጠቅላላው ፡ በዕድሜ ፡ ላይ ፡ እየተከታተሉ ፡ የሚደርሱትን ፡ ማናቸውንም ፡ መለዋወጥ ፡ የያዘ ፡ መሆኑን ፡ ለመረዳት ፡ ይቻላል ።

የቅኔው ፡ ስልት ፡ ኅሊናን ፡ በሚነካ ፡ ሁኔታ ፡ ባንድና ፡ በሁለት ፡ ቃል ፡ ብቻ ፡ አጠቃሎ ፡ ረቂቅ ፡ የሆነ ፡ ምስጢርን ፡ አዝሎ ፡ ሲታይ ፣ አባቶቻችን ፡ በአእምሮ ፡ የበሰሉ ፡ ከመሆናቸው ፡ የተነሣ ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ የማሰብ ፡ ኀይል ፡ እንደ ፡ ነበራቸው ፡ እንደ ፡ ዋዛ ፣ እንደ ፡ ዘበት ፣ ጣል ፡ አድርገው ፡ በሂዱት ፡ ቃል ፡ ለመገንዘብ ፡ እንችላለን ።

አገራችን ፡ ታላቅ ፡ ሞያ ፡ አላት ፤ አባቶቻችንም ፡ ያተረፉልንና ፡ ያቈዩልን ፡ የባህል ፡ ቅርስ ፡ እኛን ፡ ልጆቻቸውን ፡ የሚያኰራ ፡ ነው ። ይህነንም ፡ ሲወርድ ፡ ሲዋረድ ፡ መጥቶ ፡ ከእጃችን ፡ የገባውን ፡ የከበረ ፡ ባህል ፡ ጠብቆና ፡ አክብሮ ፡ ማኖር ፡ እንዲሁም ፡ ለትውልድ ፡ እንዲተላለፍ ፡ ማድረግ ፡ የኛ ፡ የወራሾቹ ፡ ፈንታ ፡ ነው ።

ያንድ ፡ አገር ፡ ሕዝብ ፡ ታላቅነትና ፡ ጠቅላላ ፡ ሁናቴ ፡ የሚታወቀው ፡ የሚገመተውና ፡ የሚመዘነው ፡ በታሪኩ ፣ በሐውልቱ ፣ በሥነ ፡ ጽሑፉ ፣ ባስተዳደሩ ፣ በባህሉና ፡ ካባት ፡ ሲያያዝ ፡ በመጣው ፡ የትውልድ ፡ ቅርሱ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፣ በታሪካችን ፡ መጽሐፍ ፡ አንደኛው ፡ ምዕራፍ ፡ አማርኛ ፡ ቅኔያችን ፡ ሊሆን ፡ ይገባል ።

ይሁን ፡ እንጂ ፡ ያንድ ፡ አገርን ፡ ትክክለኛ ፡ ሁናቴ ፡ የሕዝቡን ፡ የተፈጥሮ ፡ ስሜትና ፡ ዝንባሌ ፡ ለማወቅና ፡ ለመረዳት ፡ ታሪኩን ፡ በሚገባ ፡ መርምሮ ፡ መገንዘብ ፡ ከሁሉ ፡ የበለጠ ፡ ጠቃሚ ፡ ነገር ፡ መሆኑን ፡ መረዳት ፡ አለብን ።

ስለዚህ ፡ ማንኛውም ፡ ባለአፈ ፡ ታሪክ ፡ ለሚናገረው ፡ ሁሉ ፡ ዋጋ ፡ ሳይሰጡ ፡ ዝክረ ፡ ነገሩን ፡ ቅኔውን ፡ ተረቶቹንና ፡ ልምዶቹን ፡ መመርመርና ፡ ጠልቆ ፡ መረዳት ፡ ያለፈውን ፡ ጊዜ ፡ በመስተዋት ፡ እንደ ፡ መመልከት ፡ በፎቶግራፍ ፡ አንሥቶ ፡ ሥዕሉን ፡ እንደ ፡ ማየት ፡ ያኸል ፡ ይቈጠራል ።

በኛ ፡ በኩል ፡ ያለውን ፡ ስንመለከተው ፡ ያማርኛም ፡ ሆነ ፡ የግእዝ ፡ ቅኔዎቻችን ፡ እንዲሁም ፡ ተረቶቻችን ፡ በቀላሉ ፡ ስለማይተረጐሙ ፡ እንኳንስ ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ ባስተርጓሚ ፡ አማካይነት ፡ ይቅርና ፡ የኛም ፡ ተወላጆች ፡ ቢሆኑ ፡ ቅሉ ፡ ሁሉም ፡ በትክክል ፡ ስሜቱን ፡ በቀላሉ ፡ ለመያዝ ፡ ይችላሉ ፡ ማለት ፡ አስቸጋሪ ፡ ነው ። ምክንያቱም ፡ ከመማር ፡ ይልቅ ፡ ልዩ ፡ ስጦታን ፡ የአእምሮ ፡ ንቃትንና ፡ አስተዋይነትን ፡ የሚጠይቅ ፡ በመሆኑ ፡ ነው ።

በውጭ ፡ አገር ፡ ቋንቋ ፡ ለመተርጐም ፡ ቢሞከርም ፡ ከነወዙ ፡ ከነለዛው ፡ ስሜቱን ፡ መቶ ፡ በመቶ ፡ የሚገልጽ ፡ ሰው ፡ ይገኝ ፡ አይመስለኝም ። የሆነ ፡ ሆኖ ፡ አሁን ፡ በትምህርት ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ የሚገኙት ፡ ወጣቶቻችን ፡ የበለጠ ፡ ዕድል ፡ ስላላቸውና ፡ አማርኛ ፡ ቅኔዎቻችንና ፡ ያባቶች ፡ ቅርሶቻችንን ፡ ትክክለኛ ፡ ትርጉም ፡ ለታሪክ ፡ ጸሓፊዎች ፡ ለመግለጽ ፡ ፈቃድም ፡ ችሎታም ፡ ስለማይጐድላቸው ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የውጭ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ በሀገራችን ፡ ላይ ፡ የሚጽፏቸው ፡ ታሪክና ፡ ባህል ፡ ቀመስ ፡ የሆኑት ፡ ድርሰቶች ፡ ሁሉ ፡ የተሻሉና ፡ የታመኑ ፡ እንደሚሆኑ ፡ ጥርጥር ፡ የለውም ።

እያንዳንዱ ፡ ግጥም ፡ ሐተታ ፡ ቢጨመርበትና ፡ የግል ፡ አስተያየት ፡ ሰፋ ፡ ብሎ ፡ ቢታከልበት ፡ ኖሮ ፡ ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ አሁን ፡ ካለው ፡ ቅጽ ፡ የላቀና ፡ የጐላ ፡ በሆነ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ይህን ፡ ማድረጉ ፡ የሚቻል ፡ ሲሆን ፡ የቅኔውን ፡ ሐተታ ፡ በበለጠ ፡ ማብራራትና ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ አፍታቶ ፡ ማስረዳት ፡ የመምህራኑና ፡ ያባቶች ፡ ድርሻ ፡ እንዲሆን ፡ ትቼዋለሁ ።

እነሱም ፡ ተደብቆና ፡ ተሸፍኖ ፡ የቀረውንና ፡ ከተማሪዎቹ ፡ አእምሮ ፡ የተሰወረውን ፡ ምስጢር ፡ አጕልተው ፡ ቢያሳዩዋቸውና ፡ በቀላል ፡ መንገድ ፡ ቢገልጹላቸው ፡ በልጆቹ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስ ፡ እንደሚያገኙበት ፡ ግልጥ ፡ ነው ።

ባንደኛውም ፡ ሆነ ፡ በሁለተኛው ፡ እትም ፡ ያማርኛ ፡ ቅኔ ፡ መጻሕፍት ፡ ውስጥ ፡ ያሉት ፡ ግጥሞች ፡ በጥያቄና ፡ በመልስ ፡ መልክ ፡ የተነገሩ ፡ በምስጢር ፡ የተያዙና ፡ በንግግር ፡ የሚጠቃቀሱ ፡ ሲሆኑ ፡ የፊደልን ፡ ተራ ፡ ለመከተልና ፡ የግጥሙን ፡ ስንኝ ፡ ለመጠበቅ ፡ ሲባል ፡ ተራርቀውና ፡ ቅደም ፡ ተከተላቸው ፡ ተዘዋውሮ ፡ እንደ ፡ ተዘጋጁ ፡ የሚታወስ ፡ ነው ። ስለዚህም ፡ «አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ከነመፍቻው» ፡ ተብሎ ፡ በተሰየመው ፡ በዚህ ፡ መጽሐፍ ፡ ውስጥ ፡ አንዳንዶቹን ፡ አስፈላጊ ፡ ይሆናሉ ፡ ብለን ፡ የገመትናቸውን ፡ ብቻ ፡ በቍጥር ፡ እንዲያያዙና ፡ እንዲገናኙ ፡ አድርገናል ። ይህም ፡ አቀራረብ ፡ ግጥሞቹን ፡ የተሻሉ ፡ ከማድረጉ ፡ በላይ ፡ አንባቢዎቹንም ፡ ሆነ ፡ መምህራኑን ፡ በበለጠ ፡ እንደሚረዳና ፡ አጥጋቢ ፡ ስሜትን ፡ እንደሚሰጥ ፡ ተስፋ ፡ አደርጋለሁ ።

ይህ ፡ «አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ከነመፍቻው» ፡ የተባለ ፡ መጽሐፍ ፡ እንዲዘጋጅ ፡ ታስቦ ፡ የነበረው ፡ ካሁን ፡ በፊት ፡ በወጡት ፡ መጻሕፍት ፡ ውስጥ ፡ ለግጥሞቹ ፡ በየምዕራፉ ፡ የተሰጠውን ፡ የተራ ፡ ቍጥር ፡ በመከተል ፡ ትርጉሙን ፡ ለመስጠት ፡ ነበር ። ዳሩ ፡ ግን ፡ መገምገሪያውም ፡ ሆነ ፡ ሁለተኛው ፡ እትም ፡ የወጡት ፡ ካ፳ ፡ ፯ ፡ ዓመት ፡ በፊት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ መጽሐፎቹም ፡ አሁን ፡ ባለንበት ፡ ሰዓት ፡ በገበያ ፡ ላይ ፡ ስለ ፡ ታጡ ፡ መፍቻው ፡ ለብቻው ፡ ቢታተም ፡ ለማስተያየት ፡ የሚረዳው ፡ ዋናው ፡ መጽሐፍ ፡ ከሌለ ፡ ችግሩ ፡ የባሰ ፡ እንደሚሆን ፡ ስለ ፡ ተረዳሁትና ፡ ይልቁንም ፡ በሁለተኛው ፡ እትም ፡ ውስጥ ፡ የሌሉ ፡ ፪፻ ፡ የሚሆኑ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ ግጥሞች ፡ ስለ ፡ ሰበሰብኩና ፡ ስላከልኩበት ፡ ሁሉንም ፡ ባንድነት ፡ አጠቃሎ ፡ ለግጥሞቹ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ አዲስ ፡ ተራ ፡ ቍጥር ፡ እየሰጡ ፡ ማዘጋጀት ፡ ግድ ፡ ሆነብኝ ፤ ይህም ፡ የተሻለ ፡ ሆኖ ፡ አገኘቼዋለሁ ።

አንደኛውን ፡ ወይም ፡ ሁለተኛውን ፡ እትም ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ መጽሐፍ ፡ ይዞ ፡ የቅኔዎቹን ፡ ትርጉም ፡ ለማወቅ ፡ የሚሻ ፡ ሰው ፡ ቢኖር ፡ ግን ፡ በቍጥሩ ፡ ሳይሆን ፡ በፊደል ፡ ተራቸው ፡ እየፈለገ ፡ ምስጢሩን ፡ ለማግኘት ፡ አያዳግተውም ።

ምንም ፡ እንኳ ፡ የግጥሞቹ ፡ ስልት ፡ ያነጋገሩ ፡ ሁኔታ ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ መልክን ፡ የያዘ ፡ ቢሆን ፤ ዋናው ፡ ዐላማ ፡ የሰውን ፡ ልቡና ፡ ከክፉ ፡ አሳብ ፡ ለመመለስና ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መንገድ ፡ ለመምራት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፤ እምብዛም ፡ ከመጽሐፍ ፡ ውጭ ፡ የሆነ ፡ ቃል ፡ ባማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ውስጥ ፡ የሚገኝበት ፡ አይመስልም ፤ ይህነንም ፡ የሚያሳየንና ፡ የሚያስረዳን ፡ ልማዳችን ፡ ባህላችንና ፡ መንፈሳችን ፡ በቅዱሳት ፡ መጻሕፍት ፡ ላይ ፡ የተመሠረቱና ፡ ከሃይማኖታችን ፡ ጋራ ፡ በጥብቅ ፡ የተሳ

ሰሩ ፡ መሆናቸው ፡ ነው ። ለዚህም ፡ ማስረጃ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ ለም ሳሌ ፡ ያኸል ፡ ከመጽሐፍ ፡ ቃል ፡ ጋራ ፡ ግንኙነት ፡ ያለውን ፡ ከው ስጡ ፡ ለቅሜ ፡ አንባቢዎች ፡ እንዲመለከቱት ፡ አድርጊያለሁ ።

1 ገድሎ ፡ ማዳኑን ፡ አየነው ፤
ለወልድ ፡ አብነት ፡ አለው ። (ምስጢረ ፡ ሥላሴ) ።

2 እረ ፡ ርዳኝ ፡ እባካህ ፡
አንተ ፡ ሰው ፡ በናትህ ። (ምስጢረ ፡ ሥጋዌ) ።

3 የዛሬ ፡ ሳምንት ፡ ዐርብ ፡ ቀን ፡
ትልቅ ፡ ነጭ ፡ በግ ፡ አርደን ፡
የታመሙ ፡ ሁሉ ፡ መላው ፡ ዳኑ ፡
በሥጋና ፡ በደሙ ። (ምስጢረ ፡ ቍርባን) ።

4 ዛሬ ፡ አላዝንብህም ፡ ባታድለኝ ፡ ጠጅ ፤
ኋላ ፡ በትንሣኤ ፡ አትበድለኝ ፡ እንጂ ። (ምስጢረ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን) ።

5 ትናንት ፡ ተኝተው ፡ ሌሊት ፡
አንቀዣበረኝ ፡ ያሉት ፡
ሐሰትም ፡ አይደል ፡ እውነት ፡
ይህ ፡ ሁሉ ፡ ያለሙት ። (ምስጢረ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን) ።

6 አማቾችህ ፡ መጡ ፡ ተሸሸግ ፡ የለህም ፤
እንዲሁም ፡ ማፈሩ ፡ አያዛልቅህም ። (ምስጢረ ፡ ትንሣኤ ፡ ሙታን) ።

ሠሙም ፡ ሆነ ፡ ወርቁ ፡ በየስሜቱ ፡ ሲገለጽ ፡ በተቻለ ፡ መጠን ፡ እውነተኛውን ፡ ትርጉም ፡ እንዲይዝና ፡ ምስጢሩን ፡ እንዳይለቅ ፡ ለማ ድረግ ፡ ተደክሞበታል ።

ምናልባት ፡ የደራሲውን ፡ ትክክለኛ ፡ ሐሳብ ፡ ሳልከተል ፡ ቀርቼ ፡ ሌላ ፡ ትርጉም ፡ ሰጥቼ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ካደረግሁት ፡ ጥንቃቄ ፡ ያመለጠ ፡ ሳይሆን ፡ አይቀርምና ፡ እንደማያስወቅሠኝ ፡ ተስፋ ፡ አደር ጋለሁ ።

በዋናው ፡ መጽሐፍ ፡ መቅድም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ገለጽሁት ፡ ሁሉ ፡ ወላጆች ፡ ለልጆቻቸው ፡ በየጊዜው ፡ አንዳንድ ፡ ግጥም ፡ እየሰጡ ፡ ሠምና ፡ ወርቁን ፡ እንዲለዩ ፡ በውስጡ ፡ ተሸፍኖ ፡ የሚገኘውን ፡ ድርብ ፡ ምስጢር ፡ መርምረው ፡ ተጨንቀውና ፡ ተጠበው ፡ እንዲያወጡና ፡ እን ዲያስፋፉትም ፡ ቢያደርጓቸው ፡ የሚገኘው ፡ ፍሬ ፡ አስደሳች ፡ ይሆ ናል ።

ወጣቶቹ ፡ የሚሰለቹ ፡ ቢሆን ፡ እንኳ ፡ ኮሶ ፡ እየመረረ ፡ ካልተ
ዋጠ ፡ ፈውስን ፡ አይሰጥምና ፡ እየተከታተሉ ፡ ማሠራቱ ፡ ዋጋ ፡ አለው ፡
ይጠቅማልም ። እኔም ፡ ለልጆቼ ፡ ያደረግሁትን ፡ በሁለተኛው ፡ እትም ፡
ውስጥ ፡ ያለውን ፡ መልመጃ ፡ ለሌሎች ፡ ምሳሌ ፡ እንዲሆን ፡ በማለት ፡
ከዚህ ፡ ቀጥዬ ፡ አግብቼዋለሁ ።

ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ ሳዘጋጅ ፡ በመሰብሰብም ፡ ሆነ ፡ ምስጢሩን ፡
በመጠበቅ ፡ የረዱኝን ፡ ሁሉ ፡ ከልብ ፡ አመሰግናለሁ ። ስማቸውንም ፡
ለመግለጥ ፡ ሐሳቤ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ እነሱ ፡ ባለመፍቀዳቸው ፡ ትቼዋለሁ ።

በትምህርት ፡ ገበታ ፡ ላይ ፡ ለሚገኙት ፡ ወጣቶች ፡ የአእምሮ ፡
ማጐልመሻ ፡ እንዲሆን ፡ በማሰብ ፡ የትምህርትና ፡ የሥነ ፡ ጥበብ ፡ ሚኒ
ስቴር ፡ ይህነን ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ደጋግሞ ፡ በማሳተምና ፡ እንዲሁም ፡
መፍቻው ፡ ለመምህራኑ ፡ አገልግሎት ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ እንዲዘጋጅ ፡
ስላበረታታኝ ፡ ከልብ ፡ አመሰግናለሁ ።

ባላምባራስ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ፡ ወልደ ፡ መስቀል ።

# ማፍታቻ ።

## ልጆች ፡ ከፈቷቸው ፡ ቅኔዎች ፡ ውስጥ ፡ ለምሳሌ ፡ ያኽል ፡ ተመርጠው ፡ የቀረቡ ።

### አንደኛ ።

አ ባባ ፤

የላክልኝን ፡ ያማርኛ ፡ ቅኔ ፡ መጽሐፍ ፡ ስመለከተው ፡ በውነቱ ፡ በውስጡ ፡ የሚገኘውን ፡ ድርብ ፡ አማርኛ ፡ ለመተርጐምና ፡ ምስጢሩን ፡ ጠልቆ ፡ ለማወቅ ፡ በሰፊው ፡ ማሰብና ፡ መመርመር ፡ ያስፈልጋል ። ይልቁንም ፡ በዚህ ፡ በባዕድ ፡ አገር ፡ ብዙ ፡ የቅርብ ፡ ጓደኛና ፡ የዘመድ ፡ ቤተ ፡ ሰብ ፡ በሌለበት ፡ ይኸን ፡ መጽሐፍ ፡ ሳነበው ፡ ከሐዘኔ ፡ የሚያጽናና ፡ ከድካሜ ፡ የሚያበረታታ ፡ ምክር ፡ አግኝቼበታለሁ ። ይህ ፡ መጽሐፍ ፡ ያለፈውን ፡ አስታዋሽ ፡ የወደ ፡ ፊቱን ፡ ሐዘን ፡ አስታጋሽ ፡ ነው ፡ ለማለት ፡ በሙሉ ፡ እንደበቴ ፡ ደፍሬ፡ ለመናገር ፡ ችያለሁ ።

በዚህም ፡ ላይ ፡ ከተነገሩት ፡ አማርኞች ፡ አብዛኞቹ ፡ የትካዜና ፡ የሐዘን ፡ እንጕርጕሮዎች ፡ ናቸው ፤ ይልቁንም ፡ የሐዘኑ ፡ የሚገኘው ፡ ከሴቶች ፡ አልቃሾች ፡ ስለ፡ ሆነ ፡ ሴቶች ፡ ያገራችንን ፡ ትምህርት ፡ እንኳ ፡ ሳይማሩ ፡ እንዲያው ፡ በራሳቸው ፡ ዕውቀት ፡ ብቻ ፡ ይኸን ፡ የመሰለ ፡ ምስጢር ፡ ያለው ፡ አማርኛ ፡ በግጥም ፡ ማሰማታቸው ፡ በጣም ፡ ያስደንቃል ። ታዲያ ፡ እነኝህ ፡ ሴቶች ፡ ትምህርት ፡ ቢኖራቸው ፡ የቱን ፡ ያኽል ፡ ዕውቀት ፡ ባስፋፉ ፡ ነበር ። አሁን ፡ ከነዚህ ፡ ከሰማኋቸው ፡ ግጥሞች ፡ የሁለቱን ፡ ብቻ ፡ ፍች ፡ በመሰለኝ ፡ ጽፌ ፡ ስልክልህ ፡ አባባ ፡ እኔ ፡ በሐሳቤ ፡ ለግጥሙ ፡ የሰጠሁት ፡ ፍች ፡ ትክክለኛም ፡ ባይሆን ፡ የተቻለኝን ፡ ያኽል ፡ አስቤና ፡ መርምሬ ፡ የተረጐምኩት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሳትቀበለኝ ፡ ትቀራለህ ፡ ብዬ ፡ አልጠራጠርም ።

በሬዬ ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ስፈልግ ፡ ስባጅ ፤
እውነት ፡ ተጠፋማ ፡ አምላክ ፡ ይፍረድ ፡ እንጅ ።

እውነት ፡ በሬዬ ፡ ከጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይፍረድ ፡ ብሎ ፡ ማማረር ። እውነት ፡ ነገር ፡ (የሐሰት ፡ ተቃዋሚ) ፡ ከጠፋ ፡ እግዚአብሔር ፡ የዳኝነቱን ፡ ይሥራ ፡ ማለት ፡ ነው ።

በችግር ፡ ላይ ፡ ሲኖር ፡ በዝቶ ፡ ድኽነቱ ፡
መቼ ፡ ከበረና ፡ ዠማ ፡ ሆነ ፡ ቤቱ ።

ከብሮ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ የበዛ ፡ ሀብት ፡ ያለው ፡ ቤት ፡ ሆነ ። ዠማ ፡ የሚባለው ፡ የትልቁ ፡ ወንዝ ፡ ውሃ ፡ ወሰደው ፤ ሞቶ ፡ ቤቱ ፡ ዠማ ፡ ውስጥ ፡ ሆነ ፡ ማለት ፡ ነው ።

ጧት ፡ ማታ ፡ የምታስብህ ፡ ልጅህ ፡
ናርዶስ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ።
ALLGEMEINS, KRANKENHAUS,
ALLEE ALTONA. HAMBURG,
W. GERMANY,

## ሁለተኛ ።

በጣም ፡ ለማፈቅርህና ፡ ለምወድህ ፡ አባቴ ፡

ባላምባራስ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ።

እንደ ፡ ምን ፡ ሰንብተሃል ፤ እኔ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይመስገን ፡ ደኅና ፡ ነኝ ።

የላክልኝ ፡ መጽሐፍ ፡ «አማርኛ ፡ ቅኔ» ፡ ደረሰኝ ። ደስ ፡ የሚያሰኝ ፡ የማይሰለች፡ ጥሩ ፡ መጽሐፍ ፡ ነው ። ቀን ፡ ከትምህርት ፡ ቤት ፡ ስመለስ ፡ ማታ ፡ ማታም ፡ እቤቴ ፡ ሳርፍ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ እንኳ ፡ አልፎ ፡ አልፎ ፡ ሳላነበው ፡ ቀርቼ፡ አላውቅም ። ቢያንስ፡ ቢያ ንስ ፡ ካራት ፡ ጊዜ ፡ ያላነሰ ፡ ዘልቄ ፡ አንብቤዋለሁ ፤ ግን ፡ ምንም፡ የማይሰለች፡ አእምሮ ፡ የሚሰበስብ ፡ ትካዜን ፡ የሚቀሰቅስ ፡ በመሆኑ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ አንብቢ ፡ አንብቢ፡ ይለኛል።

ትምህርቴን ፡ በማጠናበት ፡ ጊዜም ፡ ስልችት ፡ ሲለኝ ፡ የምመለከተው ፡ ያን ተኑ ፡ መጽሐፍ ፡ ነው ፤ ማናቸውንም ፡ ገጽ ፡ ገልበጥ ፡ አድርጌ ፡ ሳነብ ፡ ጣዕም ፡ ያለው፡ ምስጢር ፡ አገኝበታለሁ ። ለመሆኑ ፡ እንዴት ፡ ይኸን ፡ ሁሉ ፡ ለመሰብሰብ ፡ ቻልክ ። በውነቱ ፡ ይህን ፡ መጽሐፍ ፡ ካገሩ ፡ የወጣ ፡ የዘመድ ፡ ናፍቆት ፡ የያዘውና፡ የተበሳጨ፡ ሰው ፡ በትዕግሥት ፡ ቢያነበው ፡ ልቡናውን ፡ የሚያጽናና ፡ ልዩ ፡ የሆነ ፡ መንፈሳዊ ፡ ትም ህርት ፡ ሊያገኝበት ፡ የሚያስችለው ፡ ነው ። ደግሞም ፡ አብዛኛው ፡ ቃል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ምስጋና ፡ ስላለበት ፡ ጸሎትም ፡ ሊሆን ፡ ይችላል ።

አ ባ ባ ፤

በጻፍክልኝ ፡ ደብዳቤ ፡ ላይ ፡ መጽሐፉን ፡ አንብበሽ ፡ ከውስጡ ፡ የፈለግሽውን ፡ ሁለትም ፡ ሦስትም ፡ ቢሆን ፡ ምስጢራዊ ፡ ግጥሞች ፡ ተርጕመሽ ፡ አስተያየትሽን ፡ ጻፊ ፡ ስላልከኝ ፤ ማናቸውም ፡ ነገር ፡ እስኪዝምሩት ፡ ለጊዜው ፡ ማስጨነቁ ፡ የታወቀ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ብዙ ፡ ተቸግሬበት ፡ ነበር ፤ ግን ፡ ያማርኛውን ፡ አነጋገር ፡ እያሰላሰልኩ ፡ ሳመዛዝነው፡ ምስጢሩን ፡ ከሞላ ፡ ጐደል ፡ ለመረዳት ፡ የቻልኩ ፡ ይመስለኛል ።

ለመሆኑ ፡ ያገራችን ፡ አነጋገር ፡ አማርኛችን ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ አስገራሚ ፡ ቃላት፡ አለው ። ይህነንስ ፡ የሚናገሩ ፡ በሰው ፡ አእምሮ ፡ ውስጥ ፡ ገብተው ፡ የሚያውቁ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚደርሰውን ፡ ተረድተው ፡ ትንቢትና ፡ ምሳሌ ፡ የሚሰጡ ፡ ሰዎች ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ የበሰለ ፡ አንጐል ፡ አላቸው ። በውነቱ ፡ ምን ፡ ዐይነት ፡ ስጦታ ፡ እንዳላቸው ፡ የትልቅነታ ቸውን ፡ መጠን ፡ ጭምር ፡ በዚህ ፡ መገመት ፡ ይቻላል ።

1 እኽል ፡ ሽምቼ ፡ ለመዝራት ፡
ክፈል ፡ ተባልኩኝ ፡ ብድራት ፤
አላውቀው ፡ እንኳ ፡ ቊናውን ፡
ትንሽ ፡ ትልቅ ፡ ይሆን ።

ባማርኛችን ፡ ቀጥታ ፡ ስሜቱ ፡ ዘር ፡ የሚሆን ፡ እኽል ፡ ተበድሬ ፡ ክፈል ፡ ተባልኩ ፤ ብድሩንም ፡ ለመክፈል ፡ መስፈሪያው ፡ ቊና ፡ (ልኩ) ፡ ትንሽ ፡ ወይም ፡ ትልቅ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አላውቅም ፡ የሚል ፡ ነው ።

ምስጢራዊ ፡ ትርጉሙ ፡ ደግሞ ፤ ትንሽም ፡ ቢሆን ፡ እትልቅ ፡ ማዕርግ ፡ ይደርስ ፡ ይሆናል ፡ ማለት ፡ ነው ።

2 የልጃገረድ ፡ አውታታ ፡
አውራ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ተኝታ ፡
ተነሽ ፡ በኋት ፡ ምነው ፤
ይህ ፡ ሁሉ ፡ አለማፈር ፡ ነው ።

ሠሙ ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡ ዘዋሪ ፡ የሆነች ፡ ልጃገረድ ፡ አደባባይ ፡ አውራ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ተኝታለችና ፡ ምነው ፡ አትነሽም ፡ ወይ ፤ ሰው ፡ አታፍሪም ፡ ወይ ፡ በኋት ፡ ማለት ፡

ምስጢራዊው ፡ ፍች ፤ ግራ ፡ የገባት ፡ ይህች ፡ ልጃገረድ ፡ መሄጃ ፡ አጥታ ፡ ሆድ ፡ ብቧት ፡ ባደባባይ ፡ ተቀምጣለችና ፡ ከሐዘኗ ፡ አጽናኗት ፡ ምከሯትም ፡ (ተቈጧት) ፡ ዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ አላፊ ፡ ቀሪ ፤ ሰዉም ፡ ሖማች ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ ማለት ፡ ይሆናል ።

3 ከብት ፡ ጠፍቶብኝ ፡ በሌሊት ፡
ስፈልግ ፡ አደርኩ ፡ ስዋትት ፤
እነግርሃለሁ ፡ ተጣርቼ ፡
ይኸን ፡ ቀን ፡ ወጥቼ ፡ አይቼ ።

ከብት ፡ (በቅሎ ፡ ወይም ፡ ላም) ፡ ጠፍቶኝ ፡ ሌሊት ፡ ስፈልግና ፡ ስንከራተት ፡ አደርኩ ፤ ምናልባት ፡ ቢገኝልኝ ፡ ወጥቼ ፡ አይና ፡ ጮክ ፡ ብዬ ፡ ወይም ፡ ተጣርቼ ፡ እነግርሃለሁ ፡ የሚል ፡ ሲሆን ፤ ችግር ፡ በበዛበት ፡ በመጥፎ ፡ ቀን ፡ ገንዘብ ፡ አጣሁ ፡ ችግሩም ፡ ጠናብኝ ፡ ለማግኘት ፡ መድከሜና ፡ መንገላታቴ ፡ አልቀረም ፡ በዚህም ፡ ምክንያት ፡ የገጠመኝን ፡ ለፈጣሪዬ ፡ ቀኖና ፡ ገብቼ ፡ እነግርሃለሁ ፡ (በጸሎት ፡ እጠራሃለሁ) ፡ የችግሩም ፡ ቀን ፡ አልፎልኝ ፡ ገንዘብ ፡ አግኝቼ ፡ (ጠግቤ) ፡ የሚል ፡ ትርጓሜ ፡ ይሰጣል ።

4 ተፈረደብህ ፡ ብዙ ፡ ዓመት ፡
በራስህ ፡ ጥፋት ፡ እስራት ፤
የኔ ፡ ወንጀሌ ፡ ቢቀልም ፡
በወሬ ፡ አልፈታም ።

በሠራኸው ፡ በራስኽ ፡ ጥፋት ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ እስራት ፡ ተፈረደብህ ፤ ነገር ፡ ገን ፡ የኔ ፡ ጥፋት ፡ ምንም ፡ ቀላል ፡ ቢሆን ፡ ወርም ፡ ቢሞላኝ ፡ ባጭር ፡ ቀን ፡ አልፈታም ።

ምስጢሩ ፤ ላባታችን ፡ ላዳም ፡ እንደ ፡ ተነገረው ፡ ጥረህ ፡ ግረህ ፡ ብላ ፡ ተብሎ ፡ ስለ ፡ ተፈረደ ፤ ሰው ፡ ሆይ ፡ ከሞት ፡ በቀር ፡ መገላገያ ፡ ስለሌለህ ፡ ለድካም፡ ተፈጥረሃል ፤ ስሕ ተትም ፡ ትእዛዝ ፡ በመተላለፍ ፡ የመጣ ፡ ፍዳ ፡ ነው ። ያደረግሁትም ፡ በደል ፡ ቀላል ፡ ቢሆን ፡ ባልተረጋገጠ ፡ ወሬ ፡ አልደነግጥም ፡ (አልፈራም) ።

5 አባቴ ፡ ከካዱኝ ፡ በውነቱ ፡
ምን ፡ ያለፋኛል ፡ በከንቱ ፤
እኔ ፡ የምለው ፡ ከቤት ፡ ደጅ ፡
አያት ፡ ብዬ ፡ ነበር ፡ እንጅ ።

አባቴ ፡ ከካዱኝና ፡ ከረገሙኝ ፡ ለምን ፡ በከንቱ ፡ እለፋለሁ ፤ እደክማለሁ ፤ ከቤት ፡ ከደጅ ፡ ሳልለይ ፡ የምመላለሰው ፡ ያባቴን ፡ አባት ፡ አያቴን ፡ ለመፈለግ ፡ ጓጉቼ ፡ ነበር ።

ምስጢሩ ፤ አባቴ ፡ ከረገሙኝ ፡ ከካዱኝ ፡ በከንቱ ፡ ለምን ፡ እደክማለሁ ፡ (አገለግላ ለሁ) ፤ ምክንያት ፡ አድርጌ ፡ ከቤት ፡ የምገባውና ፡ የምወጣው ፡ (የምመላለሰው) ፡ የምፈል ጋትን ፡ ሴት ፡ ለመመልከት ፡ ነበር ።

ናፋቂ ፡ ልጅህ ፡
ሐረገ ፡ ወይን ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ።
2312, 19th. St.N.W.,
WASHINGTON 9, D. C..
U. S. A,

## ሦስተኛ ።

ከዚህ ፡ በታች ፡ ያለውን ፡ የሐዘን ፡ እንጕርጕሮ ፡ ሠሙንና ፡ ወርቁን ፡ ለይተህ ፡ ታሪኩንም ፡ መርምረህ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ ባጭር ፡ ጻፍ ።

(ሀ) ልዑል ፡ ጌታዬ ፡ ከልምድህ ፡

(ለ) አንዳንድ ፡ እያለ ፡ ቀረልህ ፤

(ሐ) ዘንድሮ ፡ ግንቦትን ፡ ወዴት ፡ ዋልህ ፤

(መ) ዓምናስ ፡ ዓለም ፡ ማያ ፡ ነበርህ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ ፡ (ል ፡ መ) ፡

በግጥሙ ፡ ዳርቻ ፡ ከደራሲው ፡ ስም ፡ ብሥራት ፡ ወ ፡ ሐ ፡ ከሚለው ፡ ቀጥሎ ፡ ል ፡ መ ፡ የተባሉ ፡ ፊደሎች ፡ ስለሚታዩ ፡ ምን ፡ ማለት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለማወቅ ፡ ባደረግሁት ፡ ጥያቄ ፡ «ልዑል ፡ መኰንን» ፡ ማለት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ተረዳሁት ። ስለዚህም ፡ በየፊደሉ ፡ ተራ ፡ ግጥሙ ፡ የሚሰጠውን ፡ ምስጢር ፡ እጽፋለሁ ።

(ሀ) ልዑል ፡ ጌታዬ ፡ ከልምድህ ፤

ልዑል ፡ መኰንን ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ብዙ ፡ ተወዳጅ ፡ ከሆኑ ፡ ልምዶችህ ፤ ማለት ፡ ማብላት ፡ ማጠጣት ፡ መስጠት ፡ ማማለድ ፡ መጠየቅ ፡ ማጽናናት ።

(ለ) አንዳንድ ፡ እያለ ፡ ቀረልህ ፤

ካስለመድከን ፡ ልምድ ፡ አንዳንዱ ፡ እየተጓደለ ፡ እየቀረ ፡ እኛም ፡ እየተሳቀቅን ፡ ሄድን ።

(ሐ) ዘንድሮ ፡ ግንቦትን ፡ ወዴት ፡ ዋልህ ፤

በዛሬው ፡ ዓመት ፡ በግንቦት ፡ ወር ፡ ምነው ፡ አላየንህ ፡ ወዴት ፡ አገር ፡ ሄደህ ፡ ዋልህ ፡ ብሎ ፡ ያሉበትን ፡ ለማወቅ ፡ መጠየቅ ።

(መ) ዓምናስ ፡ ዓለም ፡ ማያ ፡ ነበርህ ።

ባለፈው ፡ ዓመት ፡ በዚሁ ፡ ወር ፡ ሐረር ፡ አጠገብ ፡ ዓለም ፡ ማያ ፡ በሚባለው ፡ ቀበሌ ፡ ነበርህ ፡ ብሎ ፡ ዓምና ፡ የነበሩበትን ፡ አገር ፡ መግለጽ ።

ሠም ፡ ለበስ ፡ ወርቁ ፡ (ምስጢሩ) ፡ ግን ፡ ስለ ፡ ድንገተኛው ፡ ሞታቸው ፡ ደራሲው ፡ ጥልቅ ፡ በሆነ ፡ ስሜት ፡ ሐዘኑን ፡ ገልጦ ፡ ይገኛል ። ይኸውም ፡ በዝርዝር ፡ ሲመረምሩት ፡

## (ሀ) ልዑል ፡ ጌታዬ ፡ ከልምድህ ፡

በሠሙ ፡ እንደ ፡ ተገለጠው ፡ ሁሉ፡

## (ለ) አንዳንድ ፡ እያለ ፡ ቀረልህ ፤

ለሕዝቡ ፡ ያስለመድከው ፡ ልዩ ፡ ልዩ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ አንተ ፡ በመጥፋትህ ፡ (በመሞትህ) ፡ እየተጓደለ ፡ መሄድ ፡ ዠመረ ።

## (ሐ) ዘንድሮ ፡ ግንቦትን ፡ ወዴት ፡ ዋልህ ፤

በዚሁ ፡ ወር ፡ ሥጋቸው ፡ ከነፍሳቸው ፡ ተለይቶ ፡ መሞታቸውንና ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ አለመኖራቸውን ፡ የሚገልጥ ፡ ጥያቄ ።

## (መ) ዓምናስ ፡ ዓለም ፡ ማያ ፡ ነበርህ ።

ዓምና ፡ በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ ከኛው ፡ ጋራ ፡ በማኽላችን ፡ ነበርኽ ፤ በምታደርግልን፡ ልግስና ፤ ባለህ ፡ ትሕትናና ፡ መልካም ፡ ምግባር ፡ በእውነቱ ፡ ዓለም ፡ ደስታና ፡ ፍሥሓ ፡ የምናደርግብህና ፡ የምናገኝብህ ፡ ጌታችን ፡ ነህ ፡ በማለት ፡ ነበርን ፤ በማውጋት ፡ የደረሰውን ፡ ሐዘንና ፡ ጸጸት ፡ በፈሊጥ ፡ መግለጥ ።

አክባሪና ፡ አፍቃሪ ፡ ልጅህ ፡
ታሪኩ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ።

# አራተኛ ።

ከዚህ ፡ ግርጌ ፡ ያለውን ፡ ጥንታዊ ፡ የሐዘን ፡ ግጥም ፡ ካነበብክና ፡ ከመረመርክ ፡ በኋላ ፡ የሚሰማህን ፡ ምስጢር ፡ ሠሙንና ፡ ወርቁን ፡ ፀመለየት ፡ ታሪኩንም ፡ በመግለጽ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ ለመጻፍ ፡ ሞክር ። ስለ ፡ ታሪኩ ፡ ነበርን ፡ የሚያውቅ ፡ ሰው ፡ ፈልገህ ፡ ብትጠይቅ ፡ አትከለከልም ።

(ሀ) ቆመህ ፡ ስትሸገት ፡

(ለ) ዳኛው ፡ እያደላ ፡

(ሐ) ባፋረዱህ ፡ እንጂ ፡

(መ) እትህ ፡ ምን ፡ ልበላ ።

አ ባ ባ ፤

እንዳዘዝከኝ ፡ ሁሉ ፡ ይህንን ፡ ግጥም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ደጋግሜ ፡ አነበብኩት ፤ የያዘውንም ፡ ምስጢር ፡ ለማወቅና ፡ ለመረዳት ፡ በልዩ ፡ ልዩ ፡ አንጻር ፡ ተመለከትኩት ፤ ታሪክንና ፡ ነበርን ፡ ከሚያውቀው ፡ አባባ ፡ ብሥራት ፡ ወልደ ፡ ሐና ፡ ዘንድም ፡ ሄጄ ፡ ነበር ፡ ስለዚህ ፡ ራሴ ፡ በመመራመር ፡ ያገኘሁትንና ፡ ከሽማግሌም ፡ ጠይቄ ፡ የተረዳሁትን ቀጥሎ ፡ እንዳለው ፡ ልገልጽልህ ፡ እደፍራለሁ ።

ከአራቱ ፡ ስንኞች ፡ የመዠመሪያዎቹ ፡ (ሀ)ና ፡ (ለ) ፡ በፊት ፡ ለፊቱ ፡ ወይም ፡ በሠሙ ፡ ሲተረጐሙ ፡ ከችሎት ፡ ላይ ፡ ሥርዐት ፡ ገጥሞ ፡ ክርክር ፡ ሲያደርግ ፡ ዳኛው ፡ አድላዊ ፡ ሆኖ ፡ ባላጋራውን ፡ እንደ ፡ ደገፈበት ፡ ይገልጣል ። የሚቀጥሉት ፡ ሁለቱ ፡ መሥመሮች ፡ (ሐ)ና ፡ (መ) ፡ ደግሞ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ አድልዎ፡ ከተሠራብህ ፡ እግዚአብሔርን፡ ከሚፈራ፡ ትክክለኛ ፡ ዳኛ ፡ ዘንድ ፡ ሄደህ ፡ እውነቱ ፡ ይገለጥ ፡ ዘንድ ፡ ፍርድ ፡ አግኝ ፡ እንጂ ፡ እኔማ ፡ ሴቲቱ ፡ ምን ፡ ላደርግልህና ፡ ልረዳህ ፡ እችላለሁ ፡ የሚል ፡ ስሜት ፡ ይሰጣሉ ።

ሠም ፡ ለበስ ፡ የሆነው ፡ ወይም ፡ ወርቁ ፡ የሚሰጠው ፡ ምስጢር ፡ ግን ፡ (ሀ)ና ፡ (ለ) አንተ ፡ የተበደልክ ፡ ሆነህ ፡ ከባለሥልጣን ፡ ፊት ፡ ፍትሕ ፡ ለማግኘት ፡ «አቤት ፡ አቤት» ፡ ስትልና ፡ ስትጮኽ ፡ ዳኛው ፡ ዳኝነት ፡ የእግዚአብሔር ፡ መሆኑን ፡ ዘንግቶ ፡ አላዳመጠህም ፤ ይልቁንም ፡ ተሜነህ ።

በ(ሐ)ና ፡ በ(መ) ፡ አፋ ፡ በሚባለው ፡ ስለት ፡ ባለው ፡ ቈላፋ ፡ ጐራዴ ፡ አረዱህ ፤ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ኑሮ ፡ አለኝ ፤ ልብሴ ፤ ጕርሤ ፡ ትዳሬ ፡ የሆንከው ፡ ወንድሜ ፡ አንተ ፡ ከሞትክ ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ልበላ ፡ ነው ። እንዴትስ ፡ አድርጌ ፡ ዕድሜዬን ፡ እጨርሳለሁ ፡ ስትል ፡ የሟቹ ፡ እኅት ፡ ሐዘኗንና ፡ ጸጸቷን ፡ በምስጢር ፡ እንደ ፡ ገለጠች ፡ የሚያሳይ ፡ ነው ።

ውድ ፡ አባቴ ፤

ከላይ ፡ እንደ ፡ ገለጥኩት ፤ አባባ፡ ብሥራት ፡ ይህ ፡ ግጥም ፡ ታሪክ ፡ ያለው፡ መሆኑን፡ ዘርዝሮ ፡ አስረድቶኛል ። ስለዚህም ፡ ምንም ፡ እንደ፡ሰማሁት ፡ ሁሉ ፡ በሰፊው ፡ አድርጌ፡ ለመጻፍ ፡ የተወሰነልኝ ፡ ገጽ ፡ ባይፈቅድ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ ባጭሩ ፡ ለመጻፍ ፡ እሞክራለሁ ።

(ታሪክ) ፤

ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ በመጨረሻው ፡ ዘመነ ፡ መንግሥታቸው ፡ እጅግ ፡ አለመጠን ፡ ብስጩ ፡ ሆነው ፡ ነበር ፤ ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ከምሕረት ፡ ይልቅ ፡ የጭካኔ ፡ አገዛዛቸው ፡ ስላደላ ፡ ሕዝቡ ፡ ፍትሕ ፡ አጥቶ ፡ ያለቅስ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ በጽሑፍ ፡ ካለው ፡ ታሪክ ፡ በላይ ፡ ዛሬም ፡ በዕድሜ ፡ የቈዩት ፡ አንዳንድ ፡ ሽማግሎች ፡ ያወራሉ ። ድኻውም ፡ ደፍሮ ፡ ተጠገቶ ፡ አቤቱታውን ፡ ቢያሰማ ፡ ይደበደብ ፡ ወይም ፡ ይገደል ፡ ነበር ። ለዚህም ፡ ምስክር ፡ የሚሆነው ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ አንድ ፡ የተበደለ ፡ ድኻ ፡ አቤቱታ ፡ ቢያቀርብላቸው ፡ እንደ ፡ ድፍረት ፡ ቈጥረውት ፡ አፉ ፡ በሚባለው ፡ ጐራዴ ፡ እንዲገደል ፡ አዘው ፡ ወዲያው ፡ ተደብድቦ ፡ ሞተ ። ከዚህም ፡ የተነሣ ፡ ይህንን ፡ ግፍ ፡ ያየችና ፡ የተመለከተች ፡ እኅቱ ፡ ያፄ ፡ ቴዎድሮስን ፡ ፍርድ ፡ አለመጠበቅና ፡ ማኰደል ፤ የወንድሟን ፡ ፍትሕ ፡ አጥቶ ፡ በግፍ ፡ መደብደብ ፤ የሷን ፡ መበደልና ፡ መጐዳት ፡ ለመግለጥ ፡ ስትል ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ የተነገረውን ፡ የሐዘን ፡ እንጕርጕሮ ፡ ለማድረግ ፡ በቃች ፡ ይባላል ።

ይህች ፡ ሴት ፡ በሁለት ፡ መሥመሮች ፡ ብቻ ፡ እንደዚህ ፡ አድርጋ ፡ ሙሉ ፡ ታሪክ ፡ የያዘ ፡ የሐዘን ፡ እንጕርጕሮ ፡ ለመግጠም ፡ መቻሏ ፡ በእውነቱ ፡ የሚያስደንቅ ፡ ነው ። ይኸውም ፡ ከያዘው ፡ ታሪኩ ፡ ሌላ ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሕዝብ ፡ የተፈጥሮ ፡ ዕውቀት ፡ የሚገልጥ ፡ በመሆኑ ፡ እኔንም ፡ ሆነ ፡ ጓደኞቼን ፡ እጅግ ፡ አድርጎ ፡ እንደሚያስደስተንና ፡ እንደሚጠቅመን ፡ ጥርጥር ፡ የለውም ።

አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ የሚባለው ፡ መጽሐፍ ፡ ከመዠመሪያ ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ ቢመረመር ፡ ይህንኑ ፡ የመሰለ ፡ ምስጢር ፡ የያዘ ፡ ሆኖ ፡ ስለሚገኝ ፡ ወጣቶች ፡ ስንፍና ፡ ሳናገባና ፡ ሳንሰለች ፡ እያንዳንዱ ፡ ግጥም ፡ በሚሰጠን ፡ ጠቃሚ ፡ ምክር ፡ እንጠቀምበት ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እንኳ ፡ ታሪኩ ፡ ባይገባንና ፡ ለመረዳት ፡ ብንቸገር ፡ ሽማግሎች ፡ አባቶቻችን ፡ ሊያስረዱን ፡ ይችላሉ ፤ እነሱም ፡ በመጠየቃቸው ፡ እንደሚደሰቱ ፡ ጥርጥር ፡ የለውም ።

ውድ ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፤

በመጽሐፉ ፡ ውስጥ ፡ ተሰብስበው ፡ የሚገኙት ፡ ግጥሞች ፡ ተተርጕመው ፡ ከነታሪካቸው ፡ ቢገለጹ ፡ ይጠቅሙ ፡ ይሆናል ፡ በማለት ፡ ለማደራጀት ፡ በመድከም ፡ ላይ ፡ መሆንህን ፡ ዐውቃለሁ ።

እንደኔ ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ፈልጎ ፡ ማግኘት ፡ የበለጠ ፡ ዋጋ ፡ አለው ። እወንዝ ፡ ሂዶ ፡ የተያዘ ፡ ዓሣ ፡ ከመግዛት ፡ በመንጠቆ ፡ ፈልጎ ፡ መያዙ ፡ የቱን ፡ ያኽል ፡ ደስ ፡ እንደሚያሰኝ ፡ ከማንም ፡ የተሰወረ ፡ አይደለም ።

መመራመር ፡ አእምሮን ፡ ያሠራል ፤ ካባቶች ፡ ያስተዋውቃል ፤ ታሪክ ፡ ያስተምራል ፤ ተተርጕሞ ፡ ከተገኘ ፡ ግን ፡ የሚያደክም ፡ የለም ፤ ድካምም ፡ ከቀረ ፡ መሥራት ፡ (መፈለግ) ፡ የለም ፡ ማለት ፡ ነው ።

ባልበሰለ ፡ አእምሮዬ ፡ ከተጠየቅሁት ፡ ውጭ ፡ ለተወደድከው ፡ አባቴ ፡ ሐሳብና ፡ አስተያየት ፡ ለመስጠት ፡ በመሞከሬ ፡ ከድፍረት ፡ እንዳይቈጠርብኝ ፡ ይቅርታ ፡ እጠይቃለሁ ።

ሠኔ ፡ ፳፰ ፡ ቀን ፡ ፲፱፻፶፩ ፡ ዓ ፡ ም ፡

ፍጹም ፡ ታዛዥ ፡ የሆንኩ ፡ ልጅህ ፡

ሚሊዮን ፡ ወልደ ፡ መስቀል ።

# አምስተኛ ።

በዱሮ ፡ ጊዜ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ለጌታው ፡ ችግሩን ፡ ለመግለጽ ፡ ሐዘኑንና ፡ በደሉን ፡ ለማስታወቅ ፡ የጊዜንም ፡ ሁኔታና ፡ ወቀሣን ፡ በስውር ፡ ለመናገር ፡ ሲፈልግ ፡ ሁለት ፡ ፍች ፡ ባለው ፡ አማርኛ ፡ በለሰለሰ ፡ አነጋገር ፡ እያደረገ ፡ በግጥም ፡ ያቀርባል ።

ይህነንም ፡ ዐይነት ፡ ግጥም ፡ ጊዜው ፡ እየረዘመ ፡ ሲሄድ ፡ ታሪኩ ፡ እየጠፋ ፡ የተባለበትም ፡ ምክንያት ፡ እየተረሳ ፡ ቢሄድም ፤ አባባ ፡ በዚሁ ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ተብሎ ፡ በተሰየመው ፡ መጽሐፍ ፡ መቅድም ፡ ላይ ፡ እንደ ፡ ገለጽከው ፡ ሁሉ ፤ ያንድ ፡ አገር ፡ ታሪክ ፡ በሐውልቶቹና ፡ በከተሞቹ ፤ ተቀብረው ፡ በተገኙ ፡ ዕቃዎቹ ፡ ሊመረመር ፡ እንደሚችል ፤ እንደዚሁም ፡ ምስጢሯ ፡ በተሰወረ ፡ ባንዲት ፡ ቃል ፡ ብዙ ፡ ታሪክ ፡ ሊታወቅ ፡ ይቻላል ።

ምስጢሩንና ፡ ታሪኩን ፡ ዘርዝሬ ፡ እንዳስረዳ ፡ ለጠየቅሽኝ ፡ በዘለሰኛና ፡ በመዲና፡ ለተገጠሙት ፡ ለነዚህ ፡ ሁለት ፡ ግጥሞች ፡ ያለኝ ፡ ስሜትና ፡ አስተያየት ፡ ይህ ፡ ነው ።

አዳራሹ ፡ ሰፊ ፡ በሩ ፡ አልጠበባችሁ ፤
በተራ ፡ በተራ ፡ ምነው ፡ መግባታችሁ ።

ይህ ፡ የትዝብት ፡ አነጋገር ፡ ይመስላል ፤ «አዳራሽ» ፡ ንጉሥ ፡ ወይም ፡ አንዳንድ ፡ ታላላቅ ፡ መኳንንት ፡ በሰፊው ፡ ደግሰው ፡ ግብር ፡ የሚያበሉበት ፡ ሲሆን ፡ ወደዚሁ ፡ በሩ ፡ ጠባብ ፡ ወዳልሆነው ፡ ስፍራ ፡ አንድ ፡ ባንድ ፡ በዝግታ ፡ በመቄነን ፡ መልክ ፡ ሲገቡ ፡ ተመልካች ፡ ባየ ፡ ጊዜ ፤ በሩ ፡ ሳይጠባችሁ ፡ በተራ ፡ በተራ ፡ መግባታችሁ ፡ መልካም ፡ ፈቃድ ፡ የላችሁም ፤ ወይም ፡ ግብሩን ፡ ንቃችሁ ፡ ነውን ፡ ብሎ ፡ በመጠየቅ ፡ በሐሳቡ ፡ ያለውን ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ ማለት ፡ ወቀሣውን ፡ በሽፍን ፡ እንደ ፡ ገለጸ ፡ ያሳያል ። ባንድ ፡ በልኩ ፡ ደግሞ ፡

በተራብ ፡ ተራ ፡ ምነው ፡ መግባታችሁ ፡ ሲል ፤ በቀጥታ ፡ ወቀሣውን ፡ ለመኳንንቱ፡ ያደረገ ፡ ይመስላል ፤ ይኸውም ፡ ሀብት ፡ ያላችሁ ፡ የደላችሁ ፡ ሰዎች ፡ በተራብ ፡ የዕለት ፡ እራት ፡ አጥቶ ፡ በተቸገረ ፡ ሰው ፡ ጉዳይ ፡ መግባታችሁ ፡ ያሳዝናል ፡ ማለቱ ፡ ነው ።

እንዲሁም ፡ ደግሞ ፤

ከዚያ ፡ ታች ፡ ያለችን ፡ ድውይ ፡
ከቶ ፡ ምን ፡ ቀመስሽ ፡ አልሻት ፡ ወይ ፤
ኋላ ፡ ጸጸቱ ፡ ባንች ፡ ይሆናል ፤
ተይ ፡ ሥጋ ፡ ብላሽ ፡ ይሆናል ።

ይህ ፡ መዲና ፡ ትልቅ ፡ ምክርን ፡ የያዘ ፡ ነው ። ግጥሙ ፡ የሚሰጠው ፡ የመዠመሪያ ፡ አስተያየት ፡ በሽተኛዋ ፡ ሥጋ ፡ ሳትለምንሽ ፡ አልቀረችምና ፡ በኋላ ፡ ጸጸት ፡ እንዳይሆን ብሽ ፡ አስቢበት ፡ ማለት ፡ ሲሆን ፤ የተደበቀው ፡ የወርቁ ፡ ምስጢር ፡ ግን ፡ ተይ ፡ ሥጋ ፡ ብላሽ ፡ ይሆናል ፡ አትንቀባረሪ ፡ ይህ ፡ የምትኰሪበት ፡ ሰውነት ፡ ተበላሽቶ ፡ አንቺም ፡ እንደርሷ ፡ የምትሆኚበት ፡ ቀን ፡ ይመጣ ፡ ይሆናልና ፡ አትጨክኚ ፡ ማለቱ ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ በበኩሌ ፡ የመሰለኝን ፡ ሐሳብ ፡ ስገልጽ ፡ ምናልባት ፡ ምስጢሩ ፡ ሌላ ፡ ዐይነት ፡ ፍች ፡ እንዳለው ፡ አርመህ ፡ እንድታስረዳኝ ፡ የከበረ ፡ ፈቃድህን ፡ እለምናለሁ ።

ታዛዥ ፡ ልጅህ ፡
በለጠ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ።

## ስድስተኛ ።

መጽሐፍን ፡ በመመልከት ፡ የሚገኘው ፡ ጥቅም ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ በማንበብ ፡ ያለፈውን ፡ ያስታውሱበታል ፤ የዕለቱን ፡ ይረዱበታል ፤ ስለዚህ ፡ እኔም ፡ አማርኛ ፡ ቅኔን ፡ ስመለከት ፡ ብዙ ፡ ጥልቅ ፡ የሆኑ ፡ ምስጢሮች ፡ አገኝቼበታለሁ ። አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ከትምህርት ፡ ቤቴ ፡ ስመለስ ፡ ገለጥ ፡ አድርጌ ፡ አንድና ፡ ሁለት ፡ ገጽ ፡ አንብቤ ፡ ወደ ፡ ልዩ ፡ ጕዳዬ ፡ እሄዳለሁ፡ ስል ፡ ያማርኛው ፡ ጣዕም ፡ የምስጢሩ ፡ ስሜት ፡ እየማረከኝ ፡ በቀን ፡ እስከ ፡ አጋማሹ ፡ ወይም ፡ እስከ ፡ መጨረሻው ፡ የማነብበት ፡ ጊዜ ፡ ይገኛል ።

ምስጢሩን ፡ ለማወቅ ፡ ከሰው ፡ መጠየቅ ፡ ሳስብ ፤ ጠይቆ ፡ ከመረዳት ፡ በራስ ፡ ሐሳብ፡ አውጥቶ ፡ አውርዶ ፡ መድረስ ፡ ብልጫ ፡ አለው ፡ በማለት ፡ ሐሳቤን ፡ ክትት ፡ አድርጌ ፡ አትኩሬ ፡ ስመለከተው ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ ታሪኩና ፡ ስሜቱ ፡ ከሚረቅብኝ ፡ በስተቀር ፡ ሌላው ፡ ይሰማኛል ። ይህነንም ፡ ለመረዳት ፡ የቻልኩት ፡ ንባቡን ፡ ባንድ ፡ ጊዜ ፡ በመውጣት ፡ ሳይሆን ፡ መጽሐፉ ፡ የማይሰለችና ፡ የማይጠገብ ፡ ስለ፡ሆነ ፡ ደጋግሜ ፡ በማንበቤ፡ ነው ። ስለዚህ ፡ ከተመለከትኋቸው ፡ ግጥሞች ፡ ሁለቱን ፡ ትርጉማቸውን ፡ ለመግለጽ ፡ እሞክራለሁ ።

ሰው ፡ ከሶኛል ፡ አሉ ፡ ቆሞ ፡ አደባባይ ፤
እውነት ፡ ነውር ፡ ሆኖ ፡ ሊያስቀጣኝ ፡ ነወይ ።

በዳኛ ፡ እውነትን ፡ ወንጀል ፡ አስመስሎ ፡ መከሰስ ፤
እውነት ፡ ነገር ፡ ነውር ፡ ሆኖ ፡ ሊያስቀጣኝ ፡ ነወይ ፡ ብሎ ፡ መተከዝ ።

በታንኳ ፡ በመርከብ ፡ ሲገቡ ፡ ብታይ ፡
እረ ፡ አባይን ፡ በግር ፡ ትገባለህ ፡ ወይ ።

በዋና ፡ በመርከብ ፡ የአባይን ፡ ወንዝ ፡ ገብቶ ፡ መሻገር ፤
ረኃብ ፡ ጕልበትንና ፡ ዐይንን ፡ ማድከሙን ፡ መናገር ፡ ነው ።

ከልብ ፡ የምትወድህ ፡ ልጅህ ፡
ጌጤነሽ ፡ ማኀተመ ፡ ሥላሴ ።

# ምኅጻረ፡ ቃላትና፡ ምልክት።

—ይህ፡ ዐይነት፡ ጭረት፡ የተደረገበት፡ መሥመር፡ የግጥሙ፡ ምስጢር፡ የሚገኝበትን፡ ቃል፡ ያመለክታል።

| | | |
|---|---|---|
| ሐ፡ወ፡ማ፡ሥ፡ | ማለት፡ | ሐረገ፡ ወይን፡ ማኅተመ፡ ሥላሴ። |
| ሑ፡ጂ፡ | » | ሑሴን፡ ጂብሪል። |
| መ፡ለ፡ | » | መዐዛ፡ ለማ። |
| መ፡አ፡ | » | መጠኑ፡ አደራ። |
| መዲ፡ቊ፡ | » | መዲና፡ ቊጥር። |
| ማ፡ወ፡እ፡ | » | ማኅተመ፡ ወርቅ፡ እሸቴ። |
| ሠ፡ | » | ሠም። |
| ራስ፡ኀ፡ተ፡ሃ፡ | » | ራስ፡ ኀይሉ፡ ተክለ፡ ሃይማኖት። |
| ራስ፡ዐ፡ | » | ራስ፡ ዐሊ። |
| ራስ፡ደ፡ | » | ራስ፡ ደረሰ። |
| ሰ፡ወ፡ኪ፡ | » | ሰይፉ፡ ወልደ፡ ኪዳን። |
| ቀኛ፡ኀ፡ደ፡ | » | ቀኛዝማች፡ ኀይሌ፡ ደለል። |
| ቀኛ፡ም፡ | » | ቀኛዝማች፡ ምስጋና። |
| በ፡ማ፡ | » | በላይነህ፡ ማንደፍሮ። |
| ብ፡ወ፡ሐ፡ | » | ብሥራት፡ ወልደ፡ ሐና። |
| ብ፡መ፡ሐ፡ወ፡ቂ፡ | » | ብላታ፡ መርስዔ፡ ሐዘን፡ ወልደ፡ ቂርቆስ። |
| ብ፡ወ፡ጊ፡ወ፡ዮ፡ | » | ብላታ፡ ወልደ፡ ጊዮርጊስ፡ ወልደ፡ ዮሐንስ። |
| ብ፡መ፡ | » | ብሩ፡ መኰንን። |
| ብ፡ጌ፡ኅ፡ወ፡ሥ፡ | » | ብላቴን፡ ጌታ፡ ኅሩይ፡ ወልደ፡ ሥላሴ። |
| ተ፡ተ፡ | » | ተገኝ፡ ተአምሩ። |
| ተ፡ግ፡ | » | ተቀዳ፡ ግዛው። |
| ነ፡ተ፡እ፡ | » | ነጋድራስ፡ ተሰማ፡ እሸቴ። |
| ና፡ማ፡ሥ፡ | » | ናርዶስ፡ ማኅተመ፡ ሥላሴ። |
| ን፡ሣ፡ሥ፡ | » | ንጉሥ፡ ሣህለ፡ ሥላሴ። |
| ን፡ኀ፡መ፡ | » | ንጉሥ፡ ኀይለ፡ መለኮት። |
| አ፡መ፡ | » | አለቃ፡ መርሻ። |
| አ፡ም፡ | » | አለቃ፡ ምሥራቅ። |
| አ፡በ፡ | » | አለቃ፡ በዛብህ። |
| አ፡ተ፡ሚ፡ | » | አባ፡ ተስፋ፡ ሚካኤል። |
| አ፡አ፡ | » | አለቃ፡ አክሊሉ። |
| አ፡እ፡ | » | አገኘሁ፡ እንግዳ። |
| አ፡ወ፡ጊ፡ | » | አለቃ፡ ወልደ፡ ጊዮርጊስ። |
| አ፡ደ፡ | » | አምኃ፡ ደስታ። |
| አ፡ገ፡ሐ፡ | » | አለቃ፡ ገብረ፡ ሐና። |
| አ፡እ፡ | » | አቶ፡ እሸቴ። |
| አ፡በ፡ | » | አቶ፡ በድሉ። |

## ምኅጻረ ፡ ቃላትና ፡ ምልክት ።

| | | |
|---|---|---|
| እ ፡ ጣ ፡ | ማለት ፡ | እቴጌ ፡ ጣይቱ ። |
| ካ ፡ እ ፡ | » | ካህኔ ፡ እንግዳ ። |
| ክ ፡ ር ፡ ዘ ፡ | » | ክነፈ ፡ ርግብ ፡ ዘለቀ ። |
| ወ ፡ | » | ወርቅ ። |
| ወ ፡ ሡ ፡ ኀ ፡ | » | ወይዘሮ ፡ ሡናይት ፡ ኀይሌ ። |
| ወ ፡ ት ፡ | » | ወይዘሮ ፡ ትደነቂያለሽ ። |
| ወ ፡ ጸ ፡ ጋ ፡ | » | ወልደ ፡ ጻድቅ ፡ ጋሼ ። |
| ዐ ፡ ቴ ፡ | » | ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ። |
| ዘለ ፡ ቍ ፡ | » | ዘለሰኛ ፡ ቍጥር ። |
| ዘ ፡ እ ፡ | » | ዘለቀ ፡ እውነቱ ። |
| ዘ ፡ ወ ፡ ጸ ፡ | » | ዘውግ ፡ ወልደ ፡ ጻድቅ ። |
| ዘፈ ፡ ቍ ፡ | » | ዘፈን ፡ ቍጥር ። |
| ይ ፡ በ ፡ | » | ይመኔ ፡ በውቀቱ ፡ (ዐዳኙ) ። |
| ዮ ፡ ን ፡ | » | ዮፍታሔ ፡ ንጉሤ ። |
| ዳ ፡ ፋ ፡ | » | ዳምጠው ፡ ፋንታ ። |
| ጌ ፡ ዐ ፡ | » | ጌታቸው ፡ ዐወቀ ። |
| ግ ፡ ው ፡ | » | ግራዝማች ፡ ውብቴ ። |

አንደኛ ፡ ምዕራፍ ።

# በመዲና ፡ ምስጋና ፡ ሐዘን ፡ ትካዜ ።

1 ሁለት ፡ አሽከሮች ፡ ነበሩኝ ፡
አንዱ ፡ ደስታ ፡ ከዳኝ ።

መከራ ፡ ብቻ ፡ ቀርቶኛል ፡
ስሄድ ፡ ይከተለኛል ።

ሠ ፡ ምንም ፡ እንኳን ፡ ደስታ ፡ የሚባለው ፡ አሽከሬ ፡ ቢከዳኝ ፡ መከራ ፡ የተ ባለው ፡ ሎሌዬ ፡ ይከተለኛል ፡ አይለየኝም ፡ አብሮኝ ፡ ነዋሪ ፡ ነው ።

ወ ፡ ሀብት ፡ ስላጣሁ ፡ በችግር ፡ እኖራለሁ ። ደስታ ፡ የለኝም ።

2 ሁለት ፡ ጓደኞች ፡ ሆነን ፡
እመጠጥ ፡ ቤት ፡ ገብተን ፡
እሱ ፡ ይጠጣል ፡ ዐረቄን ፡
እኔም ፡ ለጠላ ፡ አልቦዝን ።

ሠ ፡ ጠላ ፡ ለመጠጣት ፡ ቸል ፡ አልልም ፡ አልሰንፍም ።

ወ ፡ እኔም ፡ ለጠላኝ ፡ አልቦዝንም ፡ ላልወደደኝ ፡ የምዘነጋ ፡ አይደለሁም ፡ ቂሜን ፡ ተበቃይ ፡ ነኝ ፡ ለጠላቴ ፡ አልታለልም ።

3 ሁሉም ፡ ተደበላለቀ ፡
ያጥንት ፡ የነበረው ፡ አለቀ ።

ሠ ፡ ፊት ፡ የነበረው ፡ ተደበላለቀ ፡ ምንም ፡ አልቀረም ፡ አልተረፈም ፡ በጭራሽ ፡ አልቋል ።

ወ ፡ ያ ፡ ጥንት ፡ የነበረው ፡ ወግ ፡ ልማድ ፡ ሥርዐትና ፡ ባህል ፡ ተረሳ ፡ ተዘነጋ ።

4 ሰው ፡ ሁሉ ፡ ገብቶ ፡ አገሩን ፡
እህህናኔ ፡ ቀረን ።

እህህ ፡ የኔ ፡ ጓደኛ ፡
ቀን ፡ አይለየኝ ፡ ሌትም ፡ ስኛ ።

ሠ ፡ እህ ፡ የሚባለው ፡ ጓደኛዬ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ አይለየኝም ፡ ጧት ፡ ማታ ፡ ከጠገቤ ፡ አይታጣም ።

ወ ፡ ዘውትር ፡ ከማሰብና ፡ ከመተከዝ ፡ እህህ ፡ ከማለት ፡ ተለይቼ ፡ አላውቅም ።

5 ለራስ ፡ እንኳ ፡ ቅባቱ ፡
ውድ ፡ እኮ ፡ ነው ፡ በውነቱ ፡

—መልካም ፡ አገዛዝ ፡ የገዙ ፡
—ተፈሪ ፡ ነዎ ፡ በብዙ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ መልካም ፡ ገበያ ፡ የገበዩ ፡ በደኅና ፡ ዋጋ ፡ የገዙ ፡ እርስዎ ፡ ነዎት ።
ወ ፡ አገርዎን ፡ በመልካም ፡ አድርገው ፡ አስፋፍተው ፡ አደላድለው ፡ የገዙ ፡ ንጉሥ ፡ ተፈሪ ፡ ነዎት ።

6 ለባላንጣዎች ፡ ዘንቦላቸው ፡
—አምሮላቸዋል ፡ መከራቸው ።

ለኛም ፡ ድግሞ ፡ ዘንቦ ፡ አማረ ፡
—ደመናም ፡ ሆኖ ፡ አልቀረ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 156 ፡ 804 ፡ 1127)፡

ሠ ፡ አዝመራቸው ፡ ሆኗል ፤ ሰብሉ ፡ አምሯል ፤ ፍሬው ፡ አስደስቷል ።
ወ ፡ መከራ ፡ ሥቃያቸውን ፡ በሚገባ ፡ ተቀብለዋል ፤ ይበጅ ፡ ያድርግ ።

ሠ ፡ ደመናው ፡ አንዣቦ ፡ ተረግርጎ ፡ አልቀረም ፤ ዝናም ፡ ጣለ ።
ወ ፡ ደም ፡ መናም ፡ ሆኖ ፡ አልቀረ ፤ ደማችንን ፡ ተወጣን ፤ ተበቀልን ። ተጠቅተን ፡ እንዲያው ፡ በከንቱ ፡ አልቀረንም ፤ ዳኝነት ፡ አገኘን ።

7 ለነይለኛ ፡ ሴት ፡ ለምትቈጣ ፡
—ምነው ፡ መካሪ ፡ ባልታጣ ።

ሠ ፡ መካሪ ፡ አስታራቂ ፡ ሽማግሌ ፡ አይጥፋ ፤ አይታጣ ።
ወ ፡ ገሥጾ ፡ መክሮ ፡ የሚያኖር ፡ ባል ፡ ባይታጣ ፡ ባይጠፋ ፡ ደግ ፡ ነበር ።

8 —ለወልድ ፡ አብነት ፡ አለው ፤
ገድሎ ፡ ማዳኑን ፡ አየነው ።

ሠ ፡ ወልድ ፡ ከሞት ፡ የሚያድን ፡ መድኀኒት ፡ አለው ።
ወ ፡ ወልድ ፡ አብን ፡ ያየ ፡ እኔን ፡ አየ ፡ እንዳለው ፤ ከአብ ፡ ጋራ ፡ እኩልነት ፡ አለው ።

9 ለጌታ ፡ አድሬ ፡ እንደ ፡ ዋዛ ፡
አንዲት ፡ ላም ፡ እንኳ ፡ ሳልገዛ ፡

ምን ፡ ይለኛ ፡ ይሆን ፡ ዘመድ ፡
—ወተት ፡ ብዬ ፡ ብሄድ ።

ሠ ፡ ላንዲት ፡ ላም ፡ እንኳ ፡ ሳልበቃ ፡ ወተት ፡ ፍለጋ ፡ ብሄድ፡ ከቶ ፡ ሰው ፡ ምን ፡ ይለኛ ፡ ይሆን ።
ወ ፡ በችግር ፡ ምክንያት ፡ አገር ፡ ጥዬ ፡ ብዞር ፡ ብንከራተት ፡ ወተት ፡ ብዬ፡ ብሄድ ፡ ከቶ ፡ ዘመድ ፡ ምን ፡ ይለኛ ፡ ይሆን ።

10 ሊበላ ፡ ብሎ ፡ አንበጣ ፡
—ራዛው ፡ በላይ ፡ መጣ ።

ሠ ፡ ራዛ ፡ የሚባለው ፡ አሞራ ፡ አንበጣ ፡ ለመብላት ፡ በአየር ፡ ላይ ፡ መጣ ፤
ያንዣብብ ፡ ዠመር ።
ወ ፡ አሞራው ፡ ከተፎው ፡ በላይ ፡ የሚባለው ፡ ይኸው ፡ ታጥቆ ፡ ደረሰ ።

11 ላም ፡ ገዝቼ ፡ ጥገት ፡
እጠጣ ፡ ብዬ ፡ ወተት ፤

ቅሉ ፡ ተሰብሮ ፡ አዝናለሁ ፤
—በምናልባታለሁ ።

ሠ ፡ ወተቱን ፡ በምን ፡ አልበዋለሁ ፤ ዕቃ ፡ አጣሁ ፤ ማለቢያ ፡ ጮጮ ፡ ተቸ
ገርሁ ።
ወ ፡ በምናልባት ፡ አለሁ ፤ ድንገት ፡ ይሆንልኛል ፡ በማለት ፡ ተስፋ ፡ በማ
ድረግ ፡ በምኞት ፡ እቀመጣለሁ ፤ እኖራለሁ ።

12 ልብሴም ፡ አለቀ ፡ ላይ ፡ ታቹ ፤
የኔም ፡ ዘመዶች ፡ ሰለቹ ፤

ክርና ፡ መርፌስ ፡ አገኝሁ ፤
—ጠቃሚ ፡ ሰው ፡ አጣሁ ።

ሠ ፡ ጨርቅ ፡ የሚጥፍ ፡ ልብስ ፡ የሚሰፋ ፡ ሰው ፡ ተቸገርሁ ።
ወ ፡ ረዳት ፡ ወገን ፡ የሚጠቅመኝ ፡ አጋር ፡ አጣሁ ።

13 ልዑል ፡ መኰንን ፡ ከልምድህ ፡
አንዳንድ ፡ እያለ ፡ ቀረልህ ፤
ዘንድሮ ፡ ግንቦትን ፡ ወዴት ፡ ዋልህ ፡
—ዓምናስ ፡ ዓለም ፡ ማያ ፡ ነበርህ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ባለፈው ፡ ዓመት ፡ ዓለማያ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ነበርህ ፡ ከዚያ ፡ ታይ
ተሃል ።
ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ መደሰቻችን ፡ የኑሮ ፡ መጠገኛችን ፡ ነበርህ
ተድላ ፡ ደስታን ፡ ዓለምን ፡ የምናይብህ ፡ ነበርክ ።

14 ሐምሌ ፡ በባተ ፡ በሰባት ፡
ሥላሶች ፡ መጥተው ፡ ከሱ ፡ ቤት ፤

አብርሃም ፡ ልጁን ፡ መረቀው ፡
—ና ፡ ተባረክ ፡ አለው ።

ሠ ፡ ና ፡ ተባረክ ፡ ተመረቅ ፤ በረከት ፡ ተቀበል ፡ ብሎ ፡ ጠራው ።
ወ ፡ አብርሃም ፡ ልጁን ፡ ይሥሐቅን ፡ ና ፡ ተሠዋ ፡ ታረድ ፡ አለው ።

15 ጄዳ ፡ ነበረች ፡ ያች ፡ ገረድ ፡
ውሃ ፡ ልትቀዳ ፡ ለዘመድ ፤

ውላ ፡ መጣች ፡ እዚያው ፡ ሰብራ ፡
—እዩት ፡ የሰው ፡ እንስራ ።

ሠ ፡ ገረዲቷ ፡ የተውሶውን ፡ እንስራ ፡ ሰብራ ፡ መጣች ።
ወ ፡ እዩት ፡ የሰውን ፡ ሥራ ፤ የሰውን ፡ ተፈጥሮ ፡ አስተውሉ ፤ ሞቱን ፡ ከንቱነቱን ፡ ግብዝነቱንም ፡ ተመልከቱ ።

16 መልካሙ ፡ አገር ፡ ጐንደር ፡
ቤተ ፡ ክሲያን ፡ ስሞ ፡ ለመኖር ፤

አይቀርምና ፡ መዳኘት ፡
—ከተማ ፡ ሰው ፡ መግባት ።

ሠ ፡ ዳኛ ፡ ፍለጋ ፡ ወደ ፡ ከተማ ፡ መግባት ፡ ግድ ፡ ነው ።
ወ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ከተማስ ፡ ከተቈፈረ ፡ መቃብር ፡ መግባት ፡ አይቀርም ።

17 መልካም ፡ አታክልት ፡ አየሁ ፤
—እኔም ፡ አጸድቃለሁ ።

ሠ ፡ አትክልት ፡ እተክላለሁ ፤ አለማለሁ ።
ወ ፡ እኔም ፡ ቢመጸውቱኝ ፡ አስጠቅማለሁ ፤ አጸድቃለሁ ፤ ለነፍስ ፡ እሆናለሁ ።

18 መልካም ፡ ነበረ ፡ ጠጅሽ ፤
—ምነዋ ፡ አይጥም ፡ ጠላሽ ።

ሠ ፡ ጠላሽ ፡ አይጥምም ፤ አይጣፍጥም ፤ አልተዋጣልሽም ።
ወ ፡ ምነው ፡ እጠላሽ ፡ ውስጥ ፡ አይጥ ፡ ገባበት ።

19 መልካም ፡ ፈረስ ፡ ጭነህ ፡
ስትወጣ ፡ ስትወርድ ፡ አየንህ ፤

ከሜዳ ፡ ስትደርስ ፡ ዝግ ፡ አርገው ፡
—መቼም ፡ ጊዜው ፡ ጣይ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ቀኑ ፡ ገና ፡ ያልመሸ ፡ ጊዜው ፡ ያልጨለመ ፡ ነው ።
ወ ፡ ዘመን ፡ አዋራጅ ፡ ነው ፤ ጊዜ ፡ ይጥላል ፡ ያጐሳቍላል ።

20 መሸ ፡ መሰለኝ ፡ ሊጨልም ፤
—እንደ ፡ ቀን ፡ ጣይ ፡ የለም ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ቀን ፡ የሞቀ ፡ የደመቀ ፡ ፀሐይ ፡ አይታይም ።
ወ ፡ ሰውን ፡ የሚያዋርድ ፡ የሚያጐሳቍልና ፡ የሚጥል ፡ ጊዜ ፡ ነው ።

21 መተኪያ ፡ እንኳ ፡ ሌላ ፡ የለኝ ፤
—ጥላዬ ፡ ተሰብሮ ፡ አዝናለሁኝ ።

ሠ ፡ የጥላዬ ፡ መሰበር ፡ አሳዘነኝ ፡ ቈጨኝ ።

ወ ፡ አጋሬና ፡ ጥጌ ፡ የሆነው ፡ ጥላዬ ፡ ስለ ፡ ሞተብኝ ፡ መመኪያና ፡ መከ
በሪያ ፡ በማጣቴ ፡ አዝኛለሁ ።

22 መተው ፡ ይገባናል ፡ በውነት ፡
—ይኸን ፡ ምን ፡ አለበት ።

ሠ ፡ ምናለበት ፡ አያገዳም ፡ ኢያሉ ፡ ነገርን ፡ ማቃለል ።

ወ ፡ በውስጡ ፡ ምን ፡ አለበት ፡ ምን ፡ ተቀምጦበት ፡ ይሆን ፡ ብሎ ፡ መጠ
ያየቅ ።

23 መች ፡ አልቆልኝ ፡ ነው ፡ የምመጣ ፤
—ይኸ ፡ የሥጋ ፡ ጣጣ ።

ሠ ፡ የሥጋ ፡ ዕዳ ፡ ተከፍሎ ፡ ባለማለቁ ፡ መማረር ፡ መበሳጨት ።

ወ ፡ የሥጋዊ ፡ ኑሮ ፡ አድካሚ ፡ የማይሞላ ፡ የማይሳካ ፡ ነው ።

24 መንዠስ ፡ ይለኛል ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ብመንዠስስ ፡ ምን ፡ አለ ፤
—አብሮ ፡ የኖረ ፡ ሆነና ፡ አመልኳሹ ፡ እንቢ ፡ አለ ።

ሠ ፡ የሚያመነዥሰኝ ፡ ቆሞሱ ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ አልፈቀደም ።

ወ ፡ የተፈጥሮ ፡ ባሕሪዬ ፡ አሸነፈኝ ፤ ዐመሌን ፡ ማሻሻል ፡ አልቻልሁም ፤
አቃተኝ ፤ ዋሾ ፡ ሆንኩ ፤ ጠባዬን ፡ ለማረም ፡ ተሳነኝ ።

25 መንገድ ፡ ስንጓዝ ፡ ሥንቅ ፡ የለን ፡
እንግባ ፡ መንደር ፡ ቢያበሉን ፤

ሄዶ ፡ አገኘነው ፡ ለሥራው ፡
—አንድም ፡ አልተገኘ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሄዷል ፤ ተበታትኗል ፤ ከቦታው ፡ የቀረ ፡ የለም ።

ወ ፡ አንድም ፡ ቁም ፡ ነገረኛ ፡ ሰው ፡ አልተገኘም ፤ ሁሉም ፡ ከንቱ ፡
ነው ።

26 መኳንንቱ ፡ ሠለጠኑ ፡
የጨጌን ፡ አገር ፡ ለመኑ ፤

እኔ ፡ የምፈራው ፡ ይህነን ፡
—ካቡን ፡ በላይ ፡ መሆኑን ።

ሠ ፡ ከጳጳስ ፡ በላይ ፡ መሆንን ፡ ከአቡን ፡ መላቅን ፡ መብለጥን ፡ አለመ
መኘት ።

ወ ፡ እኔም ፡ የምፈራው ፡ ሞቶ ፡ ዐፈር ፡ በገቡ ፡ ጊዜ ፡ ከመቃብሩ ፡ በላይ ፡
ያለውን ፡ የርብራብ ፡ ድንጋይ ፡ ነው ።

27 ሚካኤልና ፡ ገብርኤል ፡
ብታማልዱኝ ፡ ከድንግል ፡

አለ ፡ በሆዴ ፡ የሚጨንቀኝ ፡
—ተጋላ ፡ ብታዘልቀኝ ።

ሠ ፡ ከጠላት ፡ አደጋ ፡ ብታድነኝ ፡ በጨካኝ ፡ እጅ ፡ ከመውደቅ ፡ ብትሰውረኝ ።

ወ ፡ ተጋድላ ፡ ብታዘልቀኝ ፡ አማልዳ ፡ ከኵነኔ ፡ ብታድነኝ ፡ ብትታደገኝ ።

28 ማሳለፍማ ፡ ታውቃለህ ፤
—አትሰጥም ፡ እንጂ ፡ ከጠላህ ።

ሠ ፡ ከመጠጥህ ፡ ከጠላህ ፡ አትሰጥም ፤ ጠላህን ፡ አታቀምስም ፤ ትነፍጋለህ ።

ወ ፡ ከተቈጣህ ፡ ከጠላህ ፡ የሥጋም ፡ ሆነ ፡ የነፍስ ፡ ሀብት ፡ አትሰጥም ።

29 ማሳለፍ ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ ነው ፤
—አንድም ፡ ሰው ፡ አይቀረው ።

ሠ ፡ ሁሉንም ፡ አንድ ፡ ባንድ ፡ ያዳርሳል ፡ ማሳለፍ ፡ ማስተናበር ፡ ያውቃል ፤ ማደል ፡ ይችላል ፤ ሰው ፡ አይዘልም ፤ አያልፍም ።

ወ ፡ ሞት ፡ የሚረሳው ፡ ሰው ፡ ከቶ ፡ አይገኝም ፤ ይዋል ፡ ይደር ፡ እንጂ ፡ ከሱ ፡ የሚቀር ፡ ፈጽሞ ፡ የማይሞት ፡ አንድም ፡ ፍጡር ፡ የለም ።

30 ማታ ፡ ማታ ፡ ነው ፡ መጨነቄ ፤
—ወይ ፡ ቀን ፡ አለማወቄ ።

ሠ ፡ ሳይመሽ ፡ ቀን ፡ አለማሰቤ ፤ በብርሃን ፡ አለመዘጋጀቴ ፡ ቈጨኝ ።

ወ ፡ ውርደት ፡ የሚመጣበትን ፡ ጊዜ ፡ ሞትን ፤ የሀብት ፡ ማግኛ ፡ ዕለትን ፡ ለማወቅ ፡ አለመቻሌ ፡ ያስጨንቀኛል ።

31 ማጣፈጫ ፡ እንኳ ፡ ቢገድ ፡
ይበላ ፡ ነበር ፡ ያለውድ ፤

ቅመሙ ፡ ሁሉ ፡ ከዘለቀ ፡
—ያ ፡ ሁሉ ፡ ጨው ፡ አለቀ ።

ሠ ፡ የቅመሙ ፡ ኃይል ፡ ዘለቀ ፡ በዛ ፡ የጨው ፡ ጣእም ፡ ግን ፡ ጠፋ ፡ ሳያሰማቀረ ።

ወ ፡ ጨዋ ፡ ሽማግሌ ፡ የለም ፤ ሁሉም ፡ በሞት ፡ አለቀ ፤ አልተረፈም ።

32 ምቹ ፡ ባይኖረው ፡ ካናቱ ፡
እጅግ ፡ እንዳይጠብቅ ፡ ቅናቱ ፤

የወዳጅና ፡ የኮርቻ ፡
—አለመንካቱ ፡ ብቻ ።

ሠ ፡ ኮርቻው ፡ ከተስማማ ፡ አያቈስልም ፤ አይቈረቍርም ፤ ሰውነት ፡ አይጐዳም ።

ወ ፡ ወዳጅን ፡ አለመንካት ፡ አለማስቀየም ፡ አለማስከፋት ፡ ይገባል ።

33 ምነው ፡ ጌታዬ ፡ በደልሽኝ ፤
አጥፍቼም ፡ እንደሁ ፡ ሳትመክረኝ ፡
—በሰው ፡ ፊት ፡ ቀጣሽኝ ።

ሠ ፡ ለብቻዬ ፡ ሳትመክረኝ ፡ ለምን ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ባደባባይ ፡ አዋረድሽኝ ፤ አጋለጥሽኝ ።

ወ ፡ አጥቶ ፡ ነጥቶ ፡ ተቸግሮ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ ማየት ፡ አንገበገበኝ ፤ ዐይናቸው ፡ እንደ ፡ እሳት ፡ ገረፈኝ ።

34 ምነው ፡ ብጠራህ ፡ ዝም ፡ አልህ ፤
—ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ብልህ ።

ሠ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ብዬ ፡ ስጠራህ ፡ ምነው ፡ ዝም ፡ አልሽኝ ፤ አልሰማሽኝም ።

ወ ፡ ን ፡ ነ ፡ ኃ ፡ ሥላሴ ፡ ብልኅ ፡ ዐዋቂ ፡ አስተዋይ ፡ አርቆ ፡ ተመልካች ፡ ነህ ።

35 —ምነው ፡ ጠላ ፡ ጠላ ፡ እኔን ፤
ሁሉ ፡ ሲጠጣ ፡ ጠጁን ።

ሠ ፡ ምነው ፡ ለኔ ፡ ጠላ ፡ ብቻ ፤ ሌላም ፡ መጠጥ ፡ ስጠኝ ፡ እንጂ ።

ወ ፡ ምነው ፡ እኔን ፡ ጠላኝ ፤ ምን ፡ በደልሁት ፤ ምንስ ፡ አስቀየምሁት ።

36 ምነው ፡ አንድ ፡ ፋኖስ ፡ የላችሁ ፤
—ኩራዝ ፡ ብቻ ፡ ቤታችሁ ።

ሠ ፡ በቤታችሁ ፡ ከኩራዝ ፡ በቀር ፡ ፋኖስ ፡ የላችሁምን ።

ወ ፡ ቤተ ፡ ሰቦቻችሁ ፡ ሁሉ ፡ አጫጭር ፡ ናቸው ፤ ታዳጊ ፡ የለባቸውም ፤ ረዣዥም ፡ አይደሉም ፤ ኩራዝ ፡ ብቻ ፡ ናቸው ።

37 ምነው ፡ ዝም ፡ አለኝ ፡ እግዜር ፤
—እየተጣራሁ ፡ ሳጥር ።

ሠ ፡ አጥር ፡ እያጠርሁ ፡ እየጮኽኩ ፡ ብጣራ ፡ አልሰማም ፡ አለኝ ፤ ገሸሽ ፡ አደረገኝ ።

ወ ፡ ሳጥር ፡ ሳጣጥር፡ ስጮኽ፡ ሳለቅስ፡ ያምላክ፡ ረድኤት፡ ምነው፡ ራቀኝ ።

38 ምንም ፡ በደል ፡ ሳይኖራት ፡
—ሰው ፡ አማሽ ፡ ብለው ፡ ሰደቧት ።

ሠ ፡ እነካኪ ፡ በጥባጭ ፡ አላኳሽ ፡ ነች ፤ አንዱን ፡ ካንዱ ፡ ታጣላለች ፡ ብለው ፡ አሟት ።

ወ ፡ ሰው ፡ ታሚያለሽ ፡ ስም ፡ ታጠፊያለሽ ፡ እያሉ ፡ ያወሩባታል ።

39 ምን ፡ ነገረችሽ ፡ ባልንጀራሽ ፤
—አዝኜ ፡ አዝኜ ፡ ብላሽ ።

ሠ ፡ አዝኜ ፡ አዝኜ ፡ ብላ ፡ ባልንጀራሽ ፡ ደጋግማ ፡ ስትጠይቅሽ ፡ ምነው ፡
ዝም ፡ ያልሽ ።

ወ ፡ አዝኜ ፡ አዝኜ ፡ ከንቱ ፡ ሆንኩ ፤ መና ፡ ቀረሁ ፤ ጸጸቴ ፡ ልቅሶዬ ፡ ዋጋ ፡
አጣ ።

40 ምን ፡ ወጥ ፡ ይበሏል ፡ የታመነ ፡
—ሥጋ ፡ ደዌ ፡ ከሆነ ።

ዳኑ ፡ አሉ ፡ ሁሉም ፡ የታመሙ ፡
በሥጋና ፡ በደሙ ።

ሠ ፡ የሥጋ ፡ መብል ፡ ካልተስማማ ፡ ሕመም ፡ ካመጣ ፡ ከሱ ፡ የተሻለ ፡
ሌላ ፡ ምን ፡ ይበሏል ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ አምላክ ፡ በሚገባ ፡ ካልተቀበሉት ፡ ደዌ ፡ ሥጋ ፡ ደዌ ፡ ነፍስ ፡
ያመጣል ፤ ጉዳት ፡ ያስከትላል ፤ መከራ ፡ ሥቃይ ፡ ይሆናል ።

41 ሞታለች ፡ ተብሎ ፡ እኅቴ ፡
አይለቀስ ፡ ከቤቴ ፤

በዘፈን ፡ ነው ፡ በከበሮ ፡
—መች ፡ እንዲህ ፡ ነበር ፡ ልጅ ፡ ድሮ ። (ዘ ፡ እ) ፣

ሠ ፡ ብጥንት ፡ ዘመን ፡ ልጅን ፡ ሲድሩ ፡ በዘፈን ፡ በደስታ ፡ ሌት ፡ ተቀን ፡
በመጨፈር ፡ ነበር ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ በቀላሉ ፡ አልነበረም ።

ወ ፡ የቀድሞ ፡ ጊዜ ፡ ልጆች ፡ ለወላጆቻቸው ፡ ታዛዦች ፡ ላወገኖቻቸው ፡
ትሑቶች ፡ ነበሩ ።

42 ሞት ፡ ዕቃዬ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡
ወሰደው ፡ አሉ ፡ በቶሎ ፤

ሌላውስ ፡ ይቅር ፡ ቢሻው ፡
—ዐይኑ ፡ እንኳ ፡ አሳስቶት ፡ በተወው ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፣

ሠ ፡ ለዐይኑ ፡ እንኳ ፡ ተሳስቶ ፡ ባልወሰደው ፡ በተወው ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ሞት ፡ ዐይኑ ፡ አሳስቶት ፡ አራርቶት ፡ አሳዝኖት ፡
አንጉቶት ፤ በሕፃንነቱ ፡ ባልቀጨው ፡ ባልቀጠፈው ።

43 ሠሪው ፡ ፍጥረቱን ፡ አታለለ ፡
በኖራ ፡ ሠራሁ ፡ እያለ ፤

መች ፡ ይፈርስ ፡ ነበር ፡ ቤታችን ፡
—እውነት ፡ ኖራ ፡ ቢሆን ። (ማ ፡ ወ ፡ እ) ፣

ሠ ፡ በኖራ ፡ የተሠራ ፡ ቢሆን ፡ ቤታችን ፡ ይጠነክር ፡ ነበር ፤ በየጊዜው ፡
እየፈረሰ ፡ ባላስቸገረንም ፡ ነበር ።

ወ ፡ እውነት ፡ ቢኖር ፡ ሁሉም ፡ ይቃና ፡ ይሳካ ፡ ነበር ፤ እውነት ፡ የሌለ
በት ፡ ሥራ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ያሳፍራል ።

44 ሥራም ፡ አልሠራ ፡ ምናምን ፤
—እያትማ ፡ ጣቴን ።

ሠ ፡ የጣቴን ፡ መለስለስ ፡ ዳብሰህ ፡ እየው ።
ወ ፡ ሀብት ፡ ማጣቴን ፡ ድኽነቴን ፡ እየው ፤ ተመልከተው ፤ ተረዳው ፤ መቸ
ገሬን ፡ ዕወቀው ።

45 ሥጋስ ፡ ከተገኘ ፡ በውነት ፤
—እረ ፡ አብስሎ ፡ ይብላው ፡ ስጡት ።

ሠ ፡ ጠብሶ ፡ ቀቅሎ ፡ ይመገበው ፡ ስጡት ፡ አትንፈጉት ።
ሠ ፡ ረኃብ ፡ ያቈራምደው ፤ ያቃጥለው ፡ በርብሮ ፡ ይጕዳው ፤ ይግደለው ።

46 ሥጋ ፡ እበላለሁ ፡ የግዱ ፤
—እነሉልሰገድ ፡ ታረዱ ። (1)

ሠ ፡ ፍሪዳ ፡ ከጣሉ ፡ ከብት ፡ ካረዱ ፡ ሥጋ ፡ ካልቸ ገረ ፡ ቅርጫ ፡ እገባለሁ ።
ወ ፡ እነራስ ፡ ሉልሰገድ ፡ ቶራ ፡ መስክ ፡ ላይ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ተዋግተው ፡ ሞቱ ።

47 ረኸም ፡ አይደል ፡ አጭር ፤
ወፍራምም ፡ አይደል ፡ ቀጭን ፤
ታግሎ ፡ የጣለኝ ፡ ከሰው ፡ ደጅ ፡
—እኔን ፡ ያኽል ፡ ነው ፡ እንጂ ። (ቀኛ. ም.)

ሠ ፡ ከኔ ፡ የማይበልጥ ፡ ያካል ፡ ግዝፈት ፡ የሌለው ፡ አጭር ፡ ቀጭን ፡ ሲ
ሆን ፡ ታግሎ ፡ ጣለኝ ፤ እኩያዬ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ አሸነፈኝ ።
ወ ፡ እኔን ፡ ያደከመኝና ፡ ያብረከረከኝ ፡ ረኃብ ፡ ነው ፤ የትም ፡ ወድቄ ፡
የቀረሁት ፡ ችጋር ፡ ጠንቶብኝ ፡ የምበላው ፡ እኽል ፡ አጥቼ ፡ ነው ።

48 ራሴን ፡ አሞኝ ፡ እያያችሁ ፡
ምነው ፡ ሰከረ ፡ ትላላችሁ ፡
አሁን ፡ ማን ፡ ሰጠኝ ፡ ለኔ ፡ ጠጅ ፤
—እንጀራ ፡ አዞረኝ ፡ እንጂ ።

ሠ ፡ እንክርዳድ ፡ ያለበትን ፡ እንጀራ ፡ በልቼ ፡ ራሴ ፡ ዞረ ፤ ናላዬ ፡ ተናወጠ ፡
እንጂ ፡ በመጠጥ ፡ አልሰከርኩም ።
ወ ፡ እንጀራ ፡ ፍለጋ ፡ እንከራተታለሁ ፤ እወጣለሁ ፤ እወርዳለሁ ፤ እዞራ
ለሁ ፤ እቅበዘበዛለሁ ።

49 ራስክን ፡ ፈተህ ፡ ተርትረህ ፡
የሚሠራ ፡ ሰው ፡ አጥተህ ፡

(1) የኢትዮጵያ ፡ መሳፍንትና ፡ መኳንንት ፡ መክሮ ፡ በመስከረም ፡ 16 ፡ ቀን ፡ 1909 ፡ ዓ. ም. ልጅ ፡ ኢያሱን ፡ ከመንግሥታቸው ፡ እንዳስወጧቸው ፡ ወዲያው ፡ በጥቅምት ወር ፡ አባታቸው ፡ ንጉሥ ፡ ሚካኤል ፡ የወሎን ፡ ጦር ፡ ይዘው ፡ ገሥግሠው ፡ ሲመጡ ራስ ፡ ሉልሰገድ ፡ ከነፊታውራሪ ፡ ዘውዴ ፡ ጐበና ፡ ከነአሳላፊ ፡ አቤ ፡ ጋራ ፡ ግምባር ቀደም ፡ ሆነው ፡ ተልከው ፡ ነበርና ፡ ቶራ ፡ መስክ ፡ ላይ ፡ በሠራዊት ፡ ብዛት ፡ ከበው ወግተው ፡ ስለስገደሏቸው ፡ የተገጠመ ፤

ይምጣልህ ፡ እንጂ ፡ ተጠንቅቆ ፤
—ባንተ ፡ ሥራ ፡ ማን ፡ ዐውቆ ።

ሠ ፡ አንተ ፡ በምትፈቅደው ፡ ዐይነት ፡ ቄንዳላ ፡ መሥራት ፡ ጠኵር ፡ መጐንጐን ፡ ማን ፡ ያውቃል ።

ወ ፡ ያምላክን ፡ ሥራ ፡ ማን ፡ ያውቃል ፤ ፈጣሪያችን ፡ ሆይ ፡ ሥራህ ፡ የሚደንቅ ፤ በምርምር ፡ የማይደረስ ፡ ነው ፤ ጥበብህን ፡ ለመረዳት ፡ የሚችል ፡ የለም ፤ ሥራህን ፡ ጠልቆ ፡ ማወቅ ፡ ለፍጡር ፡ አይሆንለትም ።

50 ራቴን ፡ (እራቴን) ፡ ሰጥቶኝ ፡ በጨለማ ፡
ወይ ፡ አሽከር ፡ የለኝ ፡ የሚሰማ ፤

ገድሎኝ ፡ ነበር ፡ አሳንቆ ፡
—ተንጀራ ፡ ሣር ፡ ደባልቆ ።

ሠ ፡ አሸር ፡ ባሸር ፡ ሻጣ ፡ ብቻ ፡ የሆነ ፡ እንጀራ ፡ ሰጥቶ ፡ አሳነቀኝ ።

ወ ፡ በሀብት ፡ ላይ ፡ መከራ ፡ ጨምሮ ፡ ደስታና ፡ ሐዘንን ፡ ጐን ፡ ለጐን ፡ አድርጎ ፡ ሰጠኝ ።

51 ሰማይን ፡ ያኽል ፡ ዳገት ፡
መቃብርን ፡ ያኽል ፡ ቍልቍለት ፡

በቅሎ ፡ ለምኚ ፡ ተዋረጂ ፤
—ነፍሴ ፡ በግር ፡ አትሂጂ ።

ሠ ፡ መለመን ፡ ውርደትም ፡ ቢሆን ፡ ቅሉ ፡ በእግር ፡ አትሂጂ ፤ ፈረስ ፡ በቅሎ ፡ ለምነሽ ፡ አስጪኚ ።

ወ ፡ ነፍሴ ፡ በምጽአት ፡ ጊዜ ፡ በግራ ፡ እንዳትቆሚ ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ አትሥሪ ፤ ቀናውን ፡ መንገድ ፡ ያዢ ፤ በጎ ፡ ፈቃድን ፡ ተመልከቺ ።

52 ሰብስቤ ፡ ይዤ ፡ ልብሳቸውን ፡
—ምነው ፡ ወንድሞቼ ፡ ዕራቍታቸውን ።

ሠ ፡ ምነው ፡ በልብስ ፡ ተራቄቱ ፤ ዕርቃነ ፡ ሥጋቸውን ፡ ሆኑ ፤ ሰውነታቸውን ፡ የሚከልሉበት ፡ አጡ ፤ ግንዳቸውን ፡ ቀሩ ።

ወ ፡ ምነው ፡ ወንድሞቼ ፡ እኅታቸውን ፡ ራቁ ፤ በሞት ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለዩ ።

53 ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሳይማር ፡ ሲያውቅ ፡
—እኔስ ፡ ተምሬም ፡ አላውቅ ።

ሠ ፡ ተምሬ ፡ እንዳልተማረ ፡ ደነቆርሁኝ ፤ ግራ ፡ ገባኝ ፤ ፈዘዝኩ ።

ወ ፡ እኔስ ፡ ተምሬም ፡ አላውቅ ፤ ምሕረት ፡ አግኝቼም ፡ አላውቅ ፤ ይቅርታ ፡ አልተደረገልኝም ።

54 ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሬ ፡ ሲያስጠምድ ፡
ኻያ ፡ ሠላሳ ፡ ብዙ ፡ ጥንድ ፤

የኔስ ፡ ዶማዬ ፡ ጠቅማኛለች ፤
—ጭራ ፡ ታበላኛለች ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ዶማዬ ፡ እየጫረች ፡ እየቈፈረች ፡ ትመግበኛለች ፤ የዕለት ፡ ምግቤን ፡ ችላኛለች ።

ወ ፡ በአዝማሪነት ፡ ጭራ ፡ እየከረከርኩ ፡ መሰንቆ ፡ እየመታሁ ፡ እኖራለሁ ፤ ትዳሬ ፡ ኑሮዬ ፡ ምግቤ ፡ በዘፈን ፡ ነው ።

55 ሰው ፡ ሁሉ ፡ ከዚያ ፡ መንደር ፡
ምሳውን ፡ ይጋበዝ ፡ ዝመር ፡

ይቀምሰው ፡ የለ ፡ ከዚያ ፡ አምባ ፤
—ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ውሎ ፡ ይግባ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ለኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የሚሆን ፡ ምግብ ፡ ከዚያ ፡ መንደር ፡ አይገኝም ፤ እንግዲህ ፡ ጠሙን ፡ ውሎ ፡ ይግባ ።

ወ ፡ የዐፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴን ፡ ዕድሜ ፡ ያርዝምልን ፤ ውሎ ፡ ይግባ ፤ ክፉ ፡ አይንካው ።

56 —ሰው ፡ መላክ ፡ አይሆንም ፡ ብለው ፡
አልረዳም ፡ አለ ፡ ይህ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ከቶ ፡ እንደ ፡ መልአክ ፡ ረቂቅ ፡ መሆን ፡ አይችልም ፤ ወደ ፡ መልአክነት ፡ መለወጥ ፡ አይሆንለትም ።

ወ ፡ ሰው ፡ አትላክ ፡ ምስጢራችን ፡ አይሰማ ፡ አንተው፡ ራስህ፡ ና ፡ ብለው ፡ አልገባው ፡ አለ ።

57 ሰውን ፡ ሲቀብሩ ፡ ሲከፈን ፡
በሰሌን ፡ አርጎ ፡ በሣጥን ፤
—ቀረ ፡ ባፈር ፡ መሆን ።

ሠ ፡ በዐፈር ፡ በድቤ ፡ መቀበር ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ጊዜ ፡ ሞት ፡ ቀረበ ፤ ዐፈር ፡ መሆኛ ፡ ጊዜ ፡ ደረሰ ፤ ዕድሜያችን ፡ አለቀ ፤ ሞታችን ፡ መጣ ።

58 ሲከፋ ፡ ጊዜ ፡ ሲቸግር ፡
—አገር ፡ የሰው ፡ አገር ።

ሠ ፡ ከተቸገሩ ፡ አገር ፡ የሰው ፡ አገር ፡ ነው ፤ አያኰራም ፤ ችግር ፡ ሰውን ፡ በገዛ ፡ አገሩ ፡ ያዋርደዋል ፤ ያሳፍረዋል ፤ ነጻነት ፡ የሌለውን ፡ ሰው ፡ ያስመስላል ።

ወ ፡ አገሬ ፡ በባዕድ ፡ እጅ ፡ ተያዘች ፤ የኔነቷ ፡ ቀረ ፤ የሰው ፡ ሆነች ።

59 ሲጠጣ ፡ ኖሮ ፡ ማኅበር ፡
ጠላና ፡ ጠጅ ፡ ሳይቸገር ፡

እንደ ፡ ምናምን ፡ እንደ ፡ ድኻ ፡
—አዳል ፡ ከፈለ ፡ ውሃ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ እንደሌለው ፡ እንደ ፡ መናጢ ፡ ድኻ ፡ ማኅበሩን ፡ በውሃ ፡ አ
ወጣ ፡ በጠላ ፡ ሳይከፍል ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ራስ ፡ አዳል ፡ ወንዝን ፡ አቋርጦ ፡ ባሕርን ፡ ሠንጥቆ ፡ ተሻገረ ።

60 ሳላይ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በድንገት ፡
—ሚስቴን ፡ ሳይ ፡ በወሰዳት ። (መዲ ፡ ቀኑ ፡ 164) ፡

ሠ ፡ ሚስቴን ፡ ሳላይ ፡ በስውር ፡ አስኰበለላት ፡ እንጂ ፡ ነፍሴ ፡ ቆማ ፡ ዓይኔ ፡
እያየ ፡ ይወስዳት ፡ ኖሯል ?

ወ ፡ ሥዕል ፡ ሣይ ፡ ወሰዳት ፡ አበኰበለላት ፡ አስከዳት ።

61 ስማኝ ፡ ልንገርህ ፡ አትስነፍ ፡
—ተው ፡ እየሠራህ ፡ እለፍ ።

ሠ ፡ ያለስንፍና ፡ በትጋት ፡ ሥራህን ፡ ሥራ ፡ በከንቱ ፡ ጊዜህን ፡ አታሳ
ልፍ ።

ወ ፡ ይሻልሃልና ፡ ለአምላክ ፡ ተገዝተህ ፡ በማገልገል ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ እየሠ
ራህ ፡ እለፍ ፡ ሙት ።

62 ስምህ ፡ ሲጠራ ፡ ከናባትህ ፡
—ወልደ ፡ ማርያም ፡ በላይነህ ።

ሠ ፡ ሙሉ ፡ ስምህ ፡ ወልደ ፡ ማርያም ፡ በላይነህ ፡ ነው ።

ወ ፡ ሥጋን ፡ በመዋሐድ ፡ ከማርያም ፡ የተወለድህ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ከፍ
ጡር ፡ በላይ ፡ ነህ ፡ ከሁሉ ፡ የላቅህ ፡ ክብር ፡ የመላብህ ፡ ነህ ።

63 ስታጠቅ ፡ አደርኩ ፡ ስፈታ ፡
ከዚህ ፡ ላለው ፡ ለምድር ፡ ጌታ ፡

እዚያ ፡ ላይ ፡ ደግሞ ፡ በሰማይ ፡
—መኰንን ፡ አለ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ በሰማይም ፡ ደግሞ ፡ ከእግዚአብሔር ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ቀጪ ፡ የሆነ ፡
አለቃ ፡ ሹም ፡ አለ ፡ ወይ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ ከሞት ፡ በኋላ ፡ መኰንን ፡ መሠቃየት ፡ አለ ፡ እኮ ፡
የዘለዓለም ፡ ፍርድ ፡ ይሰጣል ።

64 ስንቅ ፡ አለቀብኝ ፡ ስትል ፡
የስንቅ ፡ መያዣህ ፡ ቢጐድል ፡

በል ፡ አሁን ፡ እንካ ፡ ተቀበል ፡
—በሰፌው ፡ አገልግል ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ በትልቅ ፡ የስፌት ፡ አገልግል ፡ ሥንቅህን ፡ ያዝ ፡ ድርሻህን ፡ ውሰድ ።

ወ ፡ ከልብህ ፡ በትጋት ፡ ሥራ ፡ በብዙ ፡ ቅንነት ፡ ጠንክረህ ፡ አገልግል ።

65 ስኳርን ፡ ባልወድ ፡ ለጤናዬ ፡
—ማር ፡ እባክህን ፡ ጌታዬ ።  (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ እባክህ ፡ ማር ፡ እንዳለህ ፡ ስጠኝ ፡ መድኀኒት ፡ መቅመሻ ፡ ላድርገው።
ወ ፡ ጌታዬ ፡ እባክህ ፡ ማረኝ ፤ ይቅርታ ፡ አድርግልኝ ፤ ምሕረት ፡ አውርድ
ልኝ ፤ ከአንዠትህ ፡ ማረኝ ።

66 ቀስቅሱትና ፡ ይናገር ፡
—ተኛ ፡ አሁን ፡ እግዚአብሔር ።

ሠ ፡ አሁን ፡ ተኛ ፤ ሸለብ ፡ አደረገው ፤ ዐይኑን ፡ ከደነ ፤ እንቅልፍ ፡ ወሰ
ደው ።
ወ ፡ ፈጣሪያችን ፡ ሆይ ፡ ከኛ ፡ ጋራ ፡ ሁን ፤ ርዳን ፡ አቤቱ ፤ አትለየን ።

67 ቀፎ ፡ ማር ፡ ቢኖር ፡ ከደጄ ፡
ልሼ ፡ ጨረስኩት ፡ አውርጄ ፤

በጅ ፡ መብላት ፡ ደግ ፡ ነው ፡ እንደራሴ ፤
—አልጠቀመኝም ፡ ምላሴ ።  (ብ ፡ መ) ፡

ሠ ፡ እየላስሁ ፡ መብላቴ ፡ አልጠቀመኝም ፤ አላጠገበኝም ፤ ከአንዠቴ ፡
አልደረሰም ።
ወ ፡ ነገር ፡ በማሳካትና ፡ በአንደበተ፡ ርቱዕነት፡ አልተጠቀምሁም ፤ ነገርን፡
ብቻ ፡ መሣሪያ ፡ ማድረግ ፡ አልበጀኝም ፤ ጐዳኝ ።

68 ቀፎ ፡ አለ ፡ አሉ ፡ ባገርህ ፤
—እረ ፡ ተው ፡ ማር ፡ እባክህ ።

ሠ ፡ እባክህ ፡ ማር ፡ ስጠኝ ፡ ዳርገኝ ።
ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ምሕረትን ፡ አውርድ ፤ ይቅር ፡ በል ፤ ፊትህን ፡ መልስ ።

ጌታዬ ፡ በደለኛውን ፡ ማር ፤ የዛሬን ፡ አሳልፍ ፤ እባክህ ፡ አትበቀል ።

69 ቃል ፡ ዐዋጁ ፡ ዮሐንስ ፡
ተጣልቶህ ፡ ሳለ ፡ ሄሮድስ ፡

የምትመገበው ፡ አላጣህ ፤
—ምነው ፡ ስለት ፡ በላህ ።  (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ለምን ፡ የብፅዐት ፡ ገንዘብ ፡ በላህ ፤ የታቦት ፡ ሀብት ፡ አጠፋህ ፤ የስ
ለት ፡ ገንዘብ ፡ አባከንክ ።
ወ ፡ ሳትበድል ፡ ወንጀል ፡ ሳይኖርብህ ፡ ግፍ ፡ ሳትሠራ ፡ በሰይፍ ፡ ተቈረ
ጥህ ፤ ተከለልህ ፤ በሰማዕትነት ፡ ሞትህ ።

70 ቈላ ፡ ወርጄ ፡ ጥጥ ፡ ብዘራ ፡
አላብብ ፡ አለኝ ፡ አላፈራ ፡

አሁን ፡ እራሹ ፡ ነገረኝ ፤
—አፈራለሁ ፡ አለኝ ።

ሠ ፡ ፍሬ ፡ ማፍራት ፡ ዘር ፡ መስጠት ፡ ዐውቃለሁ ፡ አለኝ ።
ወ ፡ በመቃብር ፡ ዐፈር ፡ መሆኔ ፡ ታወሰኝ ፡ ተሰማኝ ።

71 በልቼ ፡ መጣሁ ፡ ከስላም ፡ ጋራ ፤
—እንግዲህ ፡ ምኔ ፡ አማራ ።

ሠ ፡ ከእስላም ፡ ጋር ፡ ከበላሁ ፡ ምኑን ፡ ክርስቲያን ፡ ሆንኩ ፤ ሰልሜ ፡ በሁ
ለት ፡ ቢላዋ ፡ በልቼ ፡ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ሃይማኖት ፡ ተገኘ ።
ወ ፡ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ያምርብኛል ፤ ማንስ ፡ ከቁም ፡ ነገር ፡ ይቈጥረኛል ።

72 በመንገድ ፡ ሲሄድ ፡ ያዩት ፡
ተጠርቶ ፡ እኮ ፡ ነው ፡ በድንገት ፡

ምስጢር ፡ ሳይገባ ፡ ወቀሣ ፡
—እንዴት ፡ በሰው ፡ ይነሣ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ የማንን ፡ ጌታ ፡ ማን ፡ ያማዋል ፤ ጌታዬ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ለምን ፡
ይታማል ፤ በክፉ ፡ ይነሣል ።
ወ ፡ ያንን ፡ መሳይ ፡ ጐበዝ ፡ አንበሳ ፡ እንዴት ፡ ይውደቅ ፤ በሰው ፡ እጅ ፡
ይነሣ ።

73 በሬ ፡ ብገዛው ፡ በሠላሳ ፡
አላርስም ፡ አለኝ ፡ እያገሣ ፤

እንዳልዋጋው ፡ ቀንድ ፡ የለኝ ፡
—እግዜር ፡ ጐዳ ፡ አድርጎኝ ።

ሠ ፡ የሚዋጋበት ፡ ቀንድ ፡ የሌለው ፡ ፍጥረት ፡ አደረገኝ ፤ ጠላቴን፡ የም
ላከልበት ፡ ባላጋራዬን ፡ የምመክትበት ፡ ግዕዛን ፡ ሳያድለኝ ፡ ቀረ ፡
ወ ፡ እግዜር ፡ በደለኝ ፤ በትዳሬ ፡ በንብረቴ ፡ ጐዳኝ ፤ በኑሮዬ ፡ እንድጠ
ቀምና ፡ እንዲደላኝ ፡ ሳያደርግ ፡ ቀረ ።

74 በርስትም ፡ ሆነ ፡ በከብት ፡
ፍርድ ፡ ቤት ፡ ቆሜ ፡ ስሻገት ፡

ዳኛው ፡ ተፈጠም ፡ ቢለኝም ፡
—ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ይሙት ፡ አልልም ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ከዳኛ ፡ ፊት ፡ ቆሜ ፡ ስፈጠም ፡ የሰማንያ ፡ ቃሌን ፡ ስሰጥ ፡ እንኳ ፡ ደፍሬ፡
ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ይሙት ፡ አልልም ፤ በንጉሥ ፡ ስም ፡ አልምልም ።
ወ ፡ ምኞቴ ፡ ሐሳቤ ፡ ሁሉ ፡ ለንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ ዕድሜ ፡ ነው ፤ የምጸል
የው ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ይኑር ፡ ይሰንብት ፡ እያልኩ ፡ ነው ።

75 በቅሎ ፡ ከመንገድ ፡ ጠፍታኝ ፡
ኮርቻ ፡ ይገዬ ፡ ስታዩኝ ፡

እስቲ ፡ ሁላችሁም ፡ አስታውሱ ፤
—መርገፍ ፡ አለና ፡ እንዳትረሱ ።

ሠ ፡ ያበቅሎውን ፡ ዕቃ ፡ እንዳትዘነጉ ፤ መርገፉ ፡ እንዳይረሳ ፡ አስታውሱ ።
ወ ፡ በመቃብር ፡ ረግፎ ፡ መቅረትን ፡ ተገንዘቡ ፤ ሰው ፡ መሆንን ፡ አትርሱ ፤
አንድ ፡ ቀን ፡ ዐፈር ፡ መሆንን ፡ አስታውሱ ።

76 በበቅሎ ፡ ሆኜ ፡ ስዞር ፡
ካንዱ ፡ ወዳንዱ ፡ አገር ፡

በሕልሜም ፡ አይደል ፡ በውኔ ፤
—ብዙ ፡ መከር ፡ አየሁ ፡ እኔ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ በበቅሎ ፡ ሆኜ ፡ እየተዘዋወርኩ ፡ ብዙ ፡ ሰብል ፡ አየሁ ፤ አዝመራ ፡
ጐበኘሁ ፤ መከር ፡ ተመለከትኩ ።
ወ ፡ ብዙ ፡ መከራ ፡ ደረሰብኝ ፤ ታላቅ ፡ ችግር ፡ ወደቀብኝ ።

77 በቤትህ ፡ ስትኖር ፡ ለብቻህ ፡
—በምን ፡ ምክንያት ፡ ሰው ፡ አማህ ።

ሠ ፡ በምን ፡ ሥራህ ፡ ታማህ ፤ ሰው ፡ አነሣህ ፤ ከአፍ፡ አገባህ ፤ ከሰው ፡ ም
ላስ ፡ ወደቅህ ።
ወ ፡ ለምን ፡ ሰውን ፡ ታማለህ ፤ ትቦጭቃለህ ፤ ስም ፡ ታጐድፋለህ ።

78 በርሻ ፡ ዘዴ ፡ በግብርና ፡
ነበር ፡ የሚገኝ ፡ ብልጽግና ፡

ከኔ ፡ ዘንድ ፡ የለም ፡ ተስፋ ፤
—ዘሩም ፡ እንደ ፡ በቀለ ፡ ጠፋ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የተዘራው ፡ ዘር ፡ ከበቀለ ፡ በኋላ ፡ ጠፋ ፤ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ።
ወ ፡ ዘሩ ፡ የተባለውም ፡ ሰው ፡ በቀለ ፡ እንደሚባለው ፡ ሞተ ፤ ባጭር ፡
ተቀጨ ።

79 በከንቱ ፡ ይደክማል ፡ ሰው ፤
—እኔ ፡ ካሳዬን ፡ ላልተው ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ካሳ ፡ መቀበሌን ፡ መቀጮ ፡ ማስከፈሌን ፡ ላልተው ፡ ሰው ፡ በከ
ንቱ ፡ ይደክማል ፤ ለማስታረቅ ፡ ይሞክራል ።
ወ ፡ ያም ፡ ሆነ ፡ ይህ ፡ እኔ ፡ ካሳዬን ፡ አልተውም ፤ ከሱ ፡ አልለያይም ፤
አልፋታም ።

80 በዋድላ ፡ አድርጋ ፡ በደላንታ ፡
በቅሎዬ ፡ ጠፋች ፡ ተሳስታ ፤

ፈረስ ፡ አገኘሁ ፡ ከወንድሜ ፤
—ኮርቻ ፡ አጣሁ ፡ ደግሜ ።

ሠ ፡ ዛሬም ፡ የፈረስና ፡ የበቅሎ ፡ ኮርቻ ፡ አጣሁ ።
ወ ፡ አግኝቼ ፡ ኵርቼ ፡ ሳለሁ ፡ እንደ፡ ገና ፡ እድኽነት ፡ ላይ ፡ ወደቅሁ ፤ ሳላ
ውቅበት ፡ ቀርቼ ፡ ተዋረድሁ ፤ አሳይቶ ፡ ነሣኝ ።

81 በጣም ፡ አደነቅሁ ፡ ተመልክቼ ፤
—የሰው ፡ እንስራ ፡ አይቼ ።

ሠ ፡ በሸክላው ፡ ሥራ ፡ ተደሰትሁ ፤ አሠራሩ ፡ አስደነቀኝ ።
ወ ፡ የሰውን ፡ ተፈጥሮ ፡ አደነቅሁ ፤ ከንቱነቱም ፡ አሳዘነኝ ።

82 በጧት ፡ ገበያ ፡ የሄድኩት ፡
አዲስ ፡ ልብስ ፡ ነበር ፡ ለመግዛት ፤
—ልብሱ ፡ ካገኘሁ ፡ በጥቂት ፡
ሁሉንም ፡ በተውሁት ።

ሠ ፡ በጥቂት ፡ ዋጋ ፡ አሮጌ ፡ ልብስ ፡ ለመግዛት ፡ ብችል ፡ ገበያ ፡ ልውጣ ።
ወ ፡ በመጠኑ ፡ ልቤ ፡ ማድረግን ፡ ማስተዋልን ፤ መገንዘብን ፡ ባደለኝ ።

83 በጥበብ ፡ መንገድ ፡ የምትሄዱ ፡
በኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ተራመዱ ።

አላለቀም ፡ ሥንቃችሁ ፤
—እናንተ ፡ በሶ ፡ አላችሁ ።

ሠ ፡ የበሶ ፡ ዱቄት ፡ አላችሁ ፤ ሥንቅ ፡ አላጣችሁም ፤ አላለቀባችሁም ፤
የምትበሉት ፡ አላጣችሁም ።
ወ ፡ እናንተም ፡ በሱ ፡ ድናችኋል ፤ ነጻነትን ፡ አግኝታችኋል ፤ ትምህርትን ፡
ዕውቀትን ፡ ገብይታችኋል ።

84 እጾም ፡ አዳራሽ ፡ ገብተን ፡
ዐጕል ፡ ክንብንብ ፡ ሽፍንፍን ፡
ከላይኛው ፡ ምች ፡ ላያድን ።

እንዳይታዩ ፡ ከወደዱ ፡
—ይልቁን ፡ በጋረዱ ። (ተ ፡ ተ) ፡

ሠ ፡ ከመከናነብና ፡ ከመሸፋፈን ፡ ይልቅ ፡ መጋረጃ ፡ ቢያስጥሉ ፡ ክለላ ፡
ቢያደርጉ ፡ መልካም ፡ ነበር ።
ወ ፡ በጾም ፡ ቀን ፡ ቡግ ፡ እያረዱ ፡ ይበሉ ፡ ዠመር ፤ ጾሙን ፡ ተዉት ፤
ነውሩን ፡ ናቁ ፤ ሕግና ፡ ልማድን ፡ ናቁ ፡ አፈረሱ ።

85 ቡቃያው ፡ ደርሶ ፡ ስላየን ፡
ዛሬም ፡ ለጊዜው ፡ ደስ ፡ አለን ፡

ደግሞ ፡ ወደዚያው ፡ በተራው ፡
—መከራችን ፡ ደራሽ ፡ ነው ።

ሠ ፡ አዝመራችን ፡ ፈጥኖ ፡ ይደርሳል ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ አንቸገርም ።
ወ ፡ መንገላታታችንና ፡ ሥቃይ ፡ መቀበላችን ፡ የማይቀር ፡ ነው ፡ መከራ ፡ ይመጣብናል ፡ ፍዳ ፡ እናያለን ፡ ደስታችን ፡ አልቋል ።

86 ቢማጠኑህም ፡ ከመንገድ ፡
አቤት ፡ ጌታዬ ፡ ብለህ ፡ ሂድ ፡

እምትሻገት ፡ እንደሆን ፡
—እኛም ፡ ዳኛ ፡ አይደለን ።

ሠ ፡ እኛም ፡ ዳኛ ፡ አይደለንም ፡ ፍርድ ፡ ለማየት ፡ ሥልጣን ፡ የለንም ።
ወ ፡ እኛም ፡ ዳኂ ፡ አይደለንም ፡ ነገ ፡ ዛሬ ፡ እንሞት ፡ አናውቀውም ፡ ሻቾች ፡ ረጋፊዎች ፡ ነን ።

87 ቢንቁህ ፡ አንተን ፡ ወንድሜን ፡
በጥፊ ፡ መቱኝ ፡ እኅትክን ፡

ባትቈጣው ፡ ነው ፡ ተው ፡ ባትለው ፡
—ዐይኔን ፡ ዐይኔን ፡ ባለው ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ አንተን ፡ ወንድሜን ፡ ቢንቅህና ፡ ቢደፍርህ ፡ አንተም ፡ ፊት ፡ ብታሳየውና ፡ ባትገስጸው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ብትቆጣው ፡ ኖሮ ፡ ደፍሮ ፡ እኔን ፡ እህትህን ፡ ዓይን ፡ ዓይኔን ፡ በጥፊ ፡ ይመታኝ ፡ ኑሯልን ?
ወ ፡ እንዲህ ፡ ከሚሰድበኝና ፡ ከሚያዋርደኝ ፡ በደበደበኝ ፡ ዐይኔ ፡ ሥቤን ፡ ባለኝ ፡ ይሻል ፡ ነበር ።

88 ባለሁበት ፡ ሰፈር ፡
እኔን ፡ ጠበበኝ ፡ ምድር ፡

አንተ ፡ ነህና ፡ አለኝታዬ ፡
—አስፋ ፡ ወሰን ፡ ጌታዬ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ያለሁበት ፡ ቦታ ፡ ጠቦኛልና ፡ እባክህ ፡ ጌታዬ ፡ ጥቂት ፡ ሰፋ ፡ አድርግልኝ ።
ወ ፡ አለኝታዬ ፡ የምመካበት ፡ ጌታዬ ፡ ልዑል ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ነው ።

89 ባላገር ፡ ነው ፡ ጥሩ ፡ ስልሽ ፡
ለምን ፡ ከተማ ፡ መጣሽ ።

ሠ ፡ ከከተማ ፡ አገር ፡ ቤት ፡ ይሻላል ፡ ይመቻል ፡ ይደላል ፡ ስልሽ ፡ ለምን ፡ እከተማ ፡ መጣሽ ።

ወ ፡ ባል ፡ አገር ፡ ነው ፡ ሁሉን ፡ የሚችል ፡ ልበ ፡ ሰፊ ፡ ለሚስት ፡ የሚ
መች ፡ ነው ፡ ስልሽ ፡ ለምን ፡ ፈታሽው ።

90 ባልንጀራዬ ፡ ድንገት ፡ መጥቶ ፡ እደርም ፡ ብለው ፡ ተጓደደ ፤
—ቀን ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ሄደ ።

ሠ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ሳይውል ፡ ሳያድር ፡ ወዲያው ፡ ሄደ ፤ ሳይቈይ ፡ ወዲ
ያው ፡ ተመለሰ ።

ወ ፡ ጊዜ ፡ እንደ ፡ መጣ ፡ ይሄዳል ፤ ተድላና ፡ ደስታ ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ነው ፤
ሲያልፍ ፡ አይታወቅም ።

91 ባልንጀሮቼ ፡ እናምስቱ ፡
ቅኔና ፡ ድጓ ፡ ሲፈትቱ ፡

ምስጢሩን ፡ እንኳ ፡ አላየሁ ፤
—ተክኜ ፡ እንዲያው ፡ ቀረሁ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ክህነት ፡ ተቀብዬ ፡ ሳልቀድስ ፡ ከመቅደስ ፡ ሳልገባ ፡ ቀረሁ ።

ወ ፡ ከጓደኞቼ ፡ በማነሴ ፡ እጅግ ፡ ተናደድሁ ፤ ገመንሁ ፡ ዐረርሁ ።

92 ቤተ ፡ ክሲያን ፡ ስሜ ፡ በሌት ፡
ዳዊት ፡ ደግሜ ፡ በጧት ፡

እነግርሃለሁ ፡ ላንት ፡ ጕዳይ ፤
—አንድ ፡ ባንድ ፡ ይጠናል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ አንዱ ፡ ባንዱ ፡ እንዴት ፡ ይጨከናል ፤ ለምን ፡ አይተዛዘንም ።

ወ ፡ አንድ ፡ ራሱን ፡ የተወለደ ፡ አምላክ ፡ ባንድ ፡ ቅንጣት ፡ ልጅ ፡ እን
ዴት ፡ ይጨከናል ፡ ለምን ፡ አይራራም ።

93 ቤት ፡ ሥራልን ፡ ብንለው ፡
ዕንጨት ፡ መረጠ ፡ አናጢው ፤

ሰው ፡ ሲያነሣ ፡ ሳንቃውን ፡
—አንተም ፡ አትተው ፡ ማዘኑን ።

ሠ ፡ የማእዘኑን ፡ ዕንጨት ፡ አትርሳ ፡ አትዘንጋ ፤ ትተህ ፡ አትምጣ ።

ወ ፡ ሐዘንን ፡ ትካዜን ፡ ጸሎትን ፡ መራራትን ፡ አትተው ።

94 ብቻ ፡ ጐንደሬም ፡ አይደለሽ ፤
—ላስታም ፡ ወዳጄ ፡ ነሽ ።

ሠ ፡ ጐንደሬ ፡ ብቻ ፡ ሳትሆኚ ፡ ላስታም ፡ ትወለጃለሽ ።

ወ ፡ ሕመም ፡ ቢያድርብሽም ፡ አልተውሽም ፤ አልንቅሽም ፤ ወዳጅነት
ሽን ፡ አልዘነጋውም ፡ አስታምምሻለሁ ።

95 ብንጠይቃቸው ፡ የጥንቱን ፡
—ነዋሪ ፡ አይደለንም ፡ አሉን ።

ሠ ፡ እንግዶች ፡ ነን ፡ በዚህ ፡ ቦታ ፡ አልቈየንም ፤ እምብዛም ፡ አልተቀመ ጥንም ፡ አሉን ።

ወ ፡ እኛም ፡ አንኖርም ፤ አንሰነብትም ፤ ሓቾች ፡ ነን ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የም ንቀር ፡ አይደለንም ።

96 —ተስቦ ፡ ገብቶ ፡ ከቤቴ ፡
አልወጣም ፡ ብሎኝ ፡ ዓመቴ ።

ሠ ፡ ወረርሽኝ ፡ በሽታ ፡ ከቤቴ ፡ ገብቶ ፡ መጣል ፡ ከዠመረ ፡ ዓመት ፡ ሆኖ ታል ።

ወ ፡ ችግር ፡ ከቤቴ ፡ ገብቶ ፡ አልወጣልህ ፤ አላልፍልህ ፡ አለኝ ።

97 ተበደለ ፡ አሉ ፡ እግዚአብሔር ፤
—እረ ፡ በማን ፡ አገር ።

ሠ ፡ በየት ፡ አገር ፡ በማን ፡ ስፍራ ፡ እረ ፡ እንዴት ፡ ብሎ ፡ ይህ ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ አገሩ ፡ ያምላክ ፡ ነው ፤ ሌላ ፡ ባለቤት ፡ የለውም ፤ እማን ፡ ላይ ፡ ቆመሽ ፡ እግዜርን ፡ ታሚያለሽ ፡ እንደሚሉ ፡ ሁሉ ።

98 ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ሲሉህ ፡
በሥራህ ፡ ሁሉ ፡ ውድ ፡ ነህ ፤

እኔስ ፡ መሰልከኝ ፡ ማርያምን ፡
—የጌታ ፡ እናት ፡ ብትሆን ። (1)

ሠ ፡ እንደናት ፡ የተመቸህ ፡ አዛኝ ፡ ርኅሩኅ ፡ ጌታ ፡ ብትሆን ።

ወ ፡ የጌታችን ፡ የፈጣሪያችን ፡ እናት ፡ ማርያምን ፡ በደግነት ፡ ብትመስል ።

99 ተወደደልህ ፡ የሴት ፡ ቃል ፡
—እንዴት ፡ ነሽ ፡ እግዚአብሔር ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ እንዴት ፡ ነሽ ፡ ብሎ ፡ በሴት ፡ አንቀጽ ፡ እግዚአብሔርን ፡ መጥራት ፡ (መጽሐፍ ፡ ቅድስት ፡ ሥላሴ ፡ እንደሚል) ።

ወ ፡ እግዚአብሔር ፡ መች ፡ መንሣት ፡ ብቻ ፡ ይሰጣል ፡ እንጂ ፡ (እግዚአ ብሔር ፡ ወሀበ ፤ ወእግዚአብሔር ፡ ነሥአ) ፡ እንዳለ ፡ ኢዮብ ።

100 ተዋት ፡ አትገላግላት ፡ ዝም ፡ በላት ፤
—የማትታረቅ ፡ ሴት ፡ ናት ።

ሠ ፡ ይቅር ፡ ለግዜር ፡ የማትል ፡ ዕርቅ ፡ የማትፈልግ ፡ ቂመኛ ፡ ናት ።

ወ ፡ የማትመከር ፡ የማትመለስ ፡ አሳበ ፡ ግትር ፡ የማትቀጣ ፡ ናት ፤ «ውሃ ፡ ቢወቅጡት ፡ እንቦጭ» ፡ እንደሚባለው ።

---

(1) ባ፲፰፻፸፫ ፡ ጥር ፡ ፲፱ ፡ ቀን ፡ ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ ራስ ፡ አዳልን ፡ ከጐዣም ፡ ጠርተው ፡ በበጌምድር ፡ ደብረ ፡ ታቦር ፡ ከተማ ፡ ላይ ፡ ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ብለው ፡ ባነገሡዋቸው ፡ ጊዜ ፡ አዝማሪ ፡ መርሻ ፡ የገጠመው ።

101—ተደጋድጌ ፡ እኔም ፡
ቈላ ፡ መኖሬን ፡ አልወድም ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ከደጋ ፡ አገር ፡ ተወልጄ ፡ አድጊያለሁ ።
ወ ፡ ከስቼ ፡ ተጐሳቍዬ ፡ አይመስሉ ፡ መስዬ ፡ በቈላ ፡ መኖርን ፡ አልፈቅድም ።

102 ተጣልቻለሁ ፡ ካምላክ ፡ ጋራ ፡
በብዙም ፡ አይደል ፡ ባንድ ፡ እንጀራ ፡

ርሱ ፡ እንኳ ፡ አይበላ ፡ ሆድ ፡ የለው ፤
—ከለከለኝ ፡ ምነው ።

ሠ ፡ ምነው ፡ እንጀራውን ፡ እንቢ ፡ አለኝ ፤ እየራበኝ ፡ ነፈገኝ ፤ ነሣኝ ።
ወ ፡ ሀብት ፡ አሳጣኝ ፤ መተዳደሪያ ፡ ነሣኝ ፤ የምፈናፈንበት ፡ አጣሁ ።

103 ተፈረደብህ ፡ ብዙ ፡ ዓመት ፡
በራስህ ፡ ጥፋት ፡ እስራት ፤

የኔ ፡ ወንጀሌ ፡ ቢቀልም ፡
—በወሬ ፡ አልፈታም ።

(ዘለ ፡ ቍ ፡ 553) ፡

ሠ ፡ ባንድ ፡ ወር ፡ እስራት ፡ ብቻ ፡ አልማርም ፤ አልለቀቅም ፤ ገና ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ እታሰራለሁ ።
ወ ፡ በወሬ ፡ አልፈታም ፤ በስብቀት ፡ በነገር ፡ ብዛት ፡ አልሸበርም ፤ በወሬኛ ፡ ቃል ፡ ድል ፡ አልሆንም ።

104 ታውቃለህ ፡ አሉ ፡ ሱሪ ፡ ቅድ ፤
—እንደኛ ፡ ተዋረድ ።

ሠ ፡ እንደኛ ፡ ያለ ፡ ተዋረድ ፡ ሱሪ ፡ ቅድ ፡ ታውቃለህ ።
ወ ፡ እንደኛ ፡ ተዋርደህ ፡ ኑር ፤ ራስህን ፡ ዝቅ ፡ ዝቅ ፡ አድርግ ፤ አትታበይ ።

105 ትላንት ፡ ራስ ፡ ዐሊን ፡ ስናያቸው ፡
ብዙ ፡ ዐጀብ ፡ ነበራቸው ፡
ምነዋ ፡ ዛሬ ፡ ብቻቸው ፤
—ለካስ ፡ መልኩሰው ፡ ነው ።

ሠ ፡ ለካስ ፡ ዓለም ፡ በቃኝ ፡ ብለዋል ፤ መንኵሰው ፡ ከሰው ፡ ተለይተዋል ፤ ብቸኛ ፡ ሆነዋል ።
ወ ፡ ለካስ ፡ መልኩ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ ለመስፍን ፡ ለንጉሥ ፡ ክብሩ ፡ ማዕርጉ ፡ ሞገሱ ፡ ሰራዊቱ ፡ ነው ፤ የሚደምቁት ፡ የሚከበሩት ፡ በዐጀብ ፡ ኖሯል ።

106 ትላንት ፡ ተኝተው ፡ ሌሊት ፡
አንቀዣበረኝ ፡ ያሉት ፡

ሐሰትም ፡ አይደል ፡ እውነት ፡
—ይህ ፡ ሁሉ ፡ ያለሙት ።

ሠ ፡ ሕልምዎ ፡ እውነት ፡ ነው ፤ ቅዠት ፡ አይደለም ፤ ይደርሳል ፤ ርግጥ ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ቋሚ ፡ (ሕያው) ፡ ቀኑን ፡ የሚጠብቅ ፡ ሙት ፡ ነው ፤ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ሁሉም ፡ ከሞት ፡ አይቀርም ።

107 ትላንት ፡ የመጣው ፡ መንገደኛ ፡
ጕሽ ፡ መጠጣቱን ፡ አናውቅ ፡ እኛ ፤
ከላይ ፡ ዐዳዩ ፡ ካልሰጠው ፡
—ጥሩ ፡ አያገኝም ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ያልደፈረሰ ፡ የጠራ ፡ መጠጥ ፡ አይገኝም ፤ ሁሉም ፡ ጉሽ ፡ ነው ፤ ተበጥብጧል ።

ወ ፡ ያለአምላክ ፡ ፈቃድ ፡ ሰው ፡ ጥሮ ፡ ደክሞ ፡ በራሱ ፡ ኀይል ፡ ማግኘት ፡ አይችልም ፤ ከላይ ፡ ያልተሰጠውን ፡ መውሰድ ፡ የሚሆንለት ፡ የለም ።

108 ትልቁም ፡ በሬ ፡ ደከመው ፤ ትንሹም ፡ ወይፈን ፡ ተጐዳ ፡
—ወይፈን ፡ ታላገኘሁ ፡ በምን ፡ አርሼ ፡ ልብላው ።

ሠ ፡ ለማፍረስ ፡ ለማበላሸት ፡ ቁርጥ ፡ ሐሳብ ፡ አደረግሁ ።

ወ ፡ ሰው ፡ የተሠራው ፡ ከዐፈር ፡ ነው ፤ መፍረስ ፡ መበስበስ ፡ ስላለበት ፡ እዘኑ ፤ ይህንን ፡ አስተውሉ ።

109 ትልቅ ፡ አዳራሽ ፡ ሠርቼ ፡
ሳንቃ ፡ ጕበኑን ፡ አበጅቼ ፡
አፈረሰብኝ ፡ ክዳኑ ፤
—ላፈርሰው ፡ ነው ፡ እዘኑ ።

ሠ ፡ አዲስ ፡ ያልቀና ፡ ቀንበር ፡ ያልገባ ፡ ወይፈን ፡ ካላገኘሁ ፡ በሬ ፡ እገዛለሁ ።

ወ ፡ ዕድለኛና ፡ ባለፈንታ ፡ አልሆንኩም ፤ ዕድል ፡ ፈንታዬ ፡ ጽዋ ፡ ተርታዬ ፡ አልደረ ሰም ።

110 ትንሽ ፡ ቤት ፡ ሠራሁ ፡ እንዳቅመኛ ፡
ሁለት ፡ ሦስት ፡ ሰው ፡ የሚያስተኛ ፡
አላስገባ ፡ አለች ፡ ያቺው ፡ ጠባ ፡
—ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ እየገባ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ አለተራው ፡ ተደራርቦ ፡ እየገባ ፡ በሩን ፡ አጠበበው ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሰውን ፡ እየተመቀኘ ፡ ተንኰል ፡ መሥራት ፡ ቤት ፡ መዝጋት ፡ ትዳር ፡ ማፍ ረስ ፡ ሆነ ።

111 ትንሽ ፡ አገልግል ፡ ሰፍተሽ ፡
እንዳትጕላላ ፡ እባክሽ ፤

እኛ ፡ እንኳ ፡ እንዳናያት ፡
—እዚያ ፡ ላይ ፡ ስቀያት ።

ሠ ፡ አላይኛው ፡ ቤት ፡ ሰቅለሽ ፡ አኑሪያት ፤ አንጠልጥያት ።
ወ ፡ በሰማይ ፡ ቤት ፡ ሥቃይ ፡ ሡነኔ ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ አለ ።

112 ትኋን ፡ ቍንጫ ፡ ተባዮች ፡
አሉ ፡ የሰው ፡ ደም ፡ መጣጮች ፤

እነርሱን ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡
—እናስታውስ ፡ እንጂ ፡ ቅንቅንን ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ ተባይ ፡ የሰው ፡ ደም ፡ መጣጭ ፡ ሕዋሳትን ፡ የሚቀነቅን ፡ መኖሩን ፡ እናስታውስ ።
ወ ፡ ደጋጉን ፡ ግብረ ፡ መልካሙን ፡ ሰው ፡ እናስብ ፤ ክፉ ፡ አንሥራ ፤ ቅን ፡ ሐሳብ ፡ ይኑረን ።

113 ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ልንገርህ ፡
የንጀራ ፡ አባቴ ፡ ነህ ፤

ምን ፡ ጊዜም ፡ አትከፋ ፤
—አንተ ፡ ብልህ ፡ በይፋ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ በገሃድ ፡ አንተ ፡ ብዬ ፡ ብጠራህ ፡ አንቱ ፡ ሳልልህ ፡ ብቀር ፡ አትቈጭ ፤ አይክፋህ ።
ወ ፡ ብልኅ ፡ አስተዋይ ፡ ነህ ፡ አርቆ ፡ መመልከት ፡ ትችላለህ ።

114 ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሲሄድ ፡
አይታክተውም ፡ መንገድ ፤

ምን ፡ አገር ፡ አለ ፡ ያላየው ፡
—ሁሉን ፡ ተረገጠው ።

ሠ ፡ ሁሉንም ፡ ዞሮ ፡ አየው ፤ ጐበኘው ፤ አዳረሰው ፤ ዳር ፡ ድንበሩን ፡ ተመለከተው ።
ወ ፡ ን ፡ ነ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሁሉንም ፡ ያዘ ፡ መላ ፡ ኢትዮጵያን ፡ በግዛት ፡ ጠቀለለ ።

ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ በዳሪ ፡
ይመስሉኝ ፡ ነበር ፡ ሰው ፡ አንዋሪ ፡

ጢትና ፡ ማታ ፡ ብናይዎ ፡
—ይህቺ ፡ ናት ፡ ጠባይዎ ።

ሠ ፡ ጠባይዎ ፡ ምንም ፡ የማትለወጥ ፡ የማትዛባ ፡ እንከን ፡ የሌለባት ፡ ነች ።
ወ ፡ ርኅሩኅ ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥት ፡ ነዎት ፡ ደግ ፡ የናትነት ፡ ባሕርይ ፡ ያለ ባት ፡ ጠባይ ፡ አለችዎ ።

116 ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ በፈረስ ፡
ብከተልህም ፡ አልደርስ ፤

አንተ ፡ ቁምልኝ ፡ እባክህ ፡
—በሞቴ ፡ ልቅደምህ ።

ሠ ፡ እባክህ ፡ እፊት ፡ እፊትህ ፡ ቀድሜህ ፡ ልሂድ ፤ ወደ ፡ ኋላ ፡ አልቅር ።
ወ ፡ በሞቴ ፡ ልቅደምህ ፤ ካንተ ፡ በፊት ፡ እኔ ፡ ልሙት ፤ ሞትህን ፡ አያሳ የኝ ።

117 ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ጳጳስ ፡
አርበኞችህን ፡ ስታቀስ ፤

ደስ ፡ አላት ፡ በጣም ፡ ኢትዮጵያን ፡
—የነፍስ ፡ አባቷ ፡ ብትሆን ።

ሠ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የንስሐ ፡ አባት ፡ መምህር ፡ ብትሆናት ፡ ደስ ፡ አላት ።
ወ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሕዝቧን ፡ ከጠላት ፡ ተከላክለህ ፡ ስላተረፍክላትና ፡ ነጻ ፡ ስላወጣህላት ፡ ደስ ፡ አላት ።

118 ነፍሴ ፡ ያለውል ፡ ደንግጣ ፡
ከግድግዳ ፡ ሥር ፡ ተሸጕጣ ፡

አወጣትም ፡ ብል ፡ ቸገረኝ ፤
—ተሥጋ ፡ እንቢ ፡ አለችኝ ።

ሠ ፡ ተሸንቅራ ፡ ተጣብቃ ፡ ቀረች ፤ ተቀርቅራ ፡ ተሰክታ ፡ ተወተፋ ፡ አል ወጣም ፡ አለች ።
ወ ፡ ከሥጋዊ ፡ ሥራ ፡ አልለይም ፡ አለች ፤ ሥጋዊ ፡ ፈቃድ ፡ አየለባት ፤ ዓለማዊ ፡ ሆነች ።

119 ንጉሥ ፡ መጡ ፡ አሉ ፡ አገራችን ፡
አጥር ፡ እጠሩ ፡ ልጆቻችን ፤

አፋፍ ፡ ብቅ ፡ ብለን ፡ ብናየው ፡
—ሁሉም ፡ አላፊ ፡ ነው ።

ብቻ ፡ በኛ ፡ ደጅ ፡ ይጓዛል ፤
—በዚያም ፡ በዚያም ፡ ያልፋል ።

(1) ሠ ፡ ያልፋል ፡ ይጓዛል ፤ ሁሉም ፡ ሀያጅ ፡ ነው ፤ ወደኛ ፡ ያቀና ፡ የለም ።
ወ ፡ ሁሉም ፡ ኀላፊ ፡ ጠፊ ፡ ሟች ፡ ነው ፤ ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ለዘለዓለም ፡ ነዋሪ ፡ አይደለም ።

(2) ሥ ፡ በያለበት ፡ ይጓዛል ፤ በየፊናው ፡ ይሄዳል ፤ በየበኩሉ ፡ ይወጣል ፡ ይወርዳል ።

ወ ፡ ተድላና ፡ ደስታ ፡ ይለዋወጣል ፤ ጌትነት ፡ ሀብት ፡ በሁሉም ፡ ያልፍበታል ፤ አዱኛ ፡ ጤዛ ፡ ነው ።

120 ንጉሥ ፡ ሲወጣ ፡ ወደ ፡ ደጅ ፡
—ገላን ፡ ታጥቦ ፡ ነው ፡ እንጅ ።

ሥ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ መውጣት ፡ አካልን ፡ ታጥቦ ፡ ጸድቶ ፡ ሰውነትን ፡ ተለቃልቆ ፡ ነው ።

ወ ፡ ወደ ፡ ሩቁ ፡ መሄድና ፡ ማቅናት ፡ መገመሪያ ፡ እቅርብ ፡ ያለውን ፡ ገላን ፡ የሚባለውን ፡ አገር ፡ ወግቶ ፡ አሳምኖ ፡ ነው ።

121 ንጉሥ ፡ ከዚያ ፡ ማዶ ፡ ሰፍረዋል ፤
—በደብር ፡ በደብሩ ፡ ሽሽ ፡ እንጀራ ፡ ጥለዋል ።

ሥ ፡ አንዳንድ ፡ ሺሕ ፡ እንጀራ ፡ መጥን ፡ አግባ ፡ ብለው ፡ ንጉሥ ፡ አዘዋል ።
ወ ፡ ሽሽ ፡ አምልጥ ፡ እጅህን ፡ አውጣ ፡ እንዳትማረክ ፡

122 ንጉሥ ፡ በደረቅ ፡ አይውጡ ፤
—ጭቃ ፡ ጭቃውን ፡ ይርገጡ ።

ሥ ፡ ጭቃ ፡ ጭቃውን ፡ እያዩ ፡ ይራመዱ ፤ ተጠንቅቀው ፡ ይለፉ ።

ወ ፡ ጭቃ ፡ ሹሞችዎን ፡ ይቅጡ ፤ ሕዝቡን ፡ እንዳይጫኑ ፡ አጥብቀው ፡ ይያዟቸው ።

123 ንጉሥ ፡ የሰጡኝ ፡ ታላቅ ፡ ዕቃ ፡
ላገር ፡ ለምድር ፡ የሚበቃ ፤

አድጦኝ ፡ ወድቆ ፡ እስኪሰበር ፡
—ስይዘው ፡ ቀሎኝ ፡ ነበር ። (መዲ ፡ ቍ ፡ 178) ፡ (ራስ ፡ ፡ ደ) ፡

ሥ ፡ የያዝኩት ፡ ዕቃ ፡ አልከበደኝም ፤ ቀሎኝ ፡ ነበር ።

ወ ፡ በጇ ፡ ሳለ ፡ የተሰጠኝ ፡ ግዛትና ፡ ሥልጣን ፡ ታላቅ ፡ ሲሆን ፡ እንቀው ፡ አቃልለው ፡ ነበር ፤ እንዲህ ፡ አልተጨነቅሁበትም ፡ ነበር ።

124 ንግሥት ፡ ዘውዲቱ ፡ ኰብለሽ ፡
እልም ፡ ካለው ፡ ዱር ፡ ገብተሽ ፡

አንቺ ፡ በሄድሽበት ፡ እኔም ፡ መጣሁ ፤
—አንዳች ፡ የጣሰው ፡ አጣሁ ።

ሥ ፡ አንዳችም ፡ ጫካውን ፡ ውድማውን ፡ ጥሶ ፡ ደኑን ፡ ገላልጦ ፡ ከዳር ፡ የዘለቀ ፡ አጣሁ ።

ወ ፡ አንዳችም ፡ የታደለ ፡ ሐሳቡ ፡ የተቃናለት ፡ የለም ፤ አንዳችም ፡ ዕጣ ፡ ክፍሌ ፡ የሆነ ፡ የሚጠቅመኝ ፡ አላገኘሁም ።

125 አላውቀውም ፡ ነበር ፡ አገሬን ፤
—ለካስ ፡ መቄት ፡ ኖሯልን ።

ሠ ፡ የትውልድ ፡ አገሬ ፡ መቄት ፡ የሚባለው ፡ መሆኑን ፡ ዛሬ ፡ ገና ፡ ተረዳሁት ።

ወ ፡ ለመከራ ፡ ለሥቃይ ፡ መቅ ፡ ለመግባት ፡ መፈጠሬን ፡ ዐወቅሁት ፤ ተገነዘብሁት ።

126 አልተከልኩ ፡ እንኳ ፡ ከጓሮዬ ፡
—ዱባ ፡ ለመከራዬ ።

ሠ ፡ ለችጋር ፡ ጊዜ ፡ የሚሆን ፡ የባሕር ፡ ቅል ፡ ዱባ ፡ አላለማሁም ፡ አልተከልሁም ።

ወ ፡ ድንገት ፡ መከራ ፡ ወደቀብኝ ፤ መከራዬ ፡ ዱባለ ፤ ዱብዳ ፡ ደረሰብኝ ፤ ፍርጃ ፡ መጣብኝ ።

127 አሐዱ ፡ ብሎ ፡ ቅዱስ ፡
እንዴት ፡ ይጠፋል ፡ ለቄስ ፤

በስመ ፡ አብን ፡ ሳያውቅ ፡ እንዴት ፡ ኖረ ፡
—እንደኔ ፡ ያልተማረ ።

ሠ ፡ ቀለም ፡ ያላወቀ ፡ መሀይምን ፡ ሰማይ ፡ ብልጭ ፡ ቢል ፡ በስመ ፡ አብ ፡ የማይል ።

ወ ፡ እንደኔ ፡ ያልተማረ ፡ ምሕረትን ፡ ያላገኘ ፡ ይቅር ፡ ያልተባለ ፡ የተፈረደበት ።

128 አምላክን ፡ መስሎ ፡ ቴዎድሮስ ፡
ንዑና ፡ ሑሩ ፡ ሲል ፡ ዋለ ፡ ኀሙስ ፡

ሰኞ ፡ መቅደላ ፡ ተጨነቀ ፤
—ሰው ፡ መሆኑ ፡ ታወቀ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ለመግደል ፡ ለማዳን ፡ ሥልጣን ፡ የነበረው ፡ እንደ ፡ አምላክ ፡ የተፈራው ፡ ንጉሥ ፡ ሰው ፡ መሆኑ ፡ ተገለጠ ፤ ታወቀ ።

ወ ፡ ኀይለኛው ፡ ቴዎድሮስ ፡ እንደ ፡ ማንም ፡ እንደ ፡ ተራ ፡ ሰው ፡ ሞተ ።

129 አምላክን ፡ አሙት ፡ እንደ ፡ ሰው ፤
—ምንናምን ፡ ብለው ።

ሠ ፡ ምን ፡ ብለው ፡ አሙት ፤ ምንስ ፡ እንከን ፡ አገኙበት ፤ ምን ፡ ስም ፡ አወጡለት ።

ወ ፡ ማን ፡ ፈጠረን ፡ ማንን ፡ እንመን ፡ አሉ ።

130 አሞራ ፡ አይደለሁ ፡ ሳቢሳ ፡
ላባይ ፡ ለጣና ፡ የምሣሣ ፤

ከባሕሩ ፡ ቆሜ ፡ ቢያየኝ ፡
—እኔን ፡ ደሴት ፡ አለኝ ።

ሠ ፡ በውሃ ፡ የተከበበ ፡ መሬት ፡ አደረገኝ ።
ወ ፡ እኔን ፡ ደስ ፡ መች ፡ አለኝ ፤ ፍሥሐና ፡ ደስታ ፡ አላገኘሁም ።

131 አስሮ ፡ ገንዞ ፡ ሲሰጡት ፡
—ምን ፡ ይበላ ፡ መሬት ።

ሠ ፡ አስሮ ፡ ገንዞ ፡ ሲሰጡት ፡ ምን ፡ ያድርግ ፡ መሬት ፡ አይበላሳ ።
ወ ፡ መሬት ፡ ምንኛ ፡ በላተኛ ፡ ነው ፤ በቃኝ ፡ የማይል ፡ ቢበላ ፡ ቢበላ ፡ ጠ
ገብሁን ፡ የማያውቅ ።

132 አርባ ፡ ሑዳዴን ፡ መሐደድ ፡
አክፍለት ፡ አለ ፡ የግድ ፤

የሰው ፡ ሁሉ ፡ መጐጃው ፡
—በማማት ፡ እንጂ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ሰው ፡ በማማት ፡ ጦም ፡ ይደክማል ፡ ሰውነቱ ፡ ይጐዳል ።
ወ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ የሚጐዳው ፡ በሐሜትና ፡ በነገር ፡ ነው ።

133 አስቤ ፡ ትላንት ፡ ሌሊት ፡
ለመጻፍ ፡ ነበር ፡ ድርሰት ፤

እኔስ ፡ አጣሁኝ ፡ አንድም ፡ ቃል ፡
—እባክህ ፡ ማን ፡ ልበል ። ( ብ . ወ . ሐ )

ሠ ፡ ምን ፡ ብዬ ፡ ልጻፍ ፤ ሐሳብ ፡ ንገረኝ ፤ ቃል ፡ ማዋጣት ፡ ርዳኝ ።
ወ ፡ ማንን ፡ ይለምኗል ፤ እንዳንተስ ፡ ማን ፡ ቸር ፡ አለ ።

134 አሳድጊያለሁ ፡ ሶሎግ ፡ ውሻ ፡
የዱር ፡ አራዊት ፡ መቀስቀሻ ፤

ተመልካቾችም ፡ አፋፍ ፡ ሁኑ ፡
—በሉ ፡ እናንተም ፡ አድኑ ።

ሠ ፡ እናንተም ፡ ወደ ፡ አደናችሁ ፡ ሂዱ ፤ ደን ፡ ለደን ፡ ዋሉ ፤ አውሬ ፡ ግ
ደሉ ።
ወ ፡ እናንተም ፡ ከሞት ፡ አትድኑም ፡ አትተርፉም ፤ ሓኞች ፡ ናችሁ ።

135 አሽከሬን ፡ ልኬ ፡ ከዘመድ ፡
እጠብቃለሁ ፡ ከመንገድ ፤

አሻግሬ ፡ ሳይ ፡ መንገዱን ፡
—እረ ፡ ሰው ፡ ምናምን ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ሰው ፡ በመንገዱ ፡ አይታይም ፤ ወጪ ፡ ወራጅም ፡ የለም ፤ ጭር ፡ ብሏል ።
ወ ፡ እንግዲህ ፡ የሰው ፡ ነገር ፡ በቃኝ ፤ ላምነው ፡ አልችልም ፤ ከንቱነቱን ፡ ተረዳሁት ።

136　አቈልቍዬ ፡ ባይ ፡ መሬቱን ፡
ቈስሎ ፡ አገኘሁት ፡ እግሬን ፤

ምን ፡ አሳዘነኝ ፡ ለግሬ ፡ ቍስል ፡
—ስሄድ ፡ እኖር ፡ ይመስል ።

ሠ ፡ ስሄድ ፡ አልኖርም ፡ አሁን ፡ ዐርፋለሁ ።
ወ ፡ ሽማች ፡ ነኝ ፤ ቆሜ ፡ አልኖርም ፡ ነገ ፡ ጧት ፡ ልሞት ፡ ምን ፡ ያሳዝነኛል ።

137　አባቱ ፡ ልጁን ፡ ተጣልቶት ፡
በጣም ፡ አዘኖበት ፡ ረግሞት ፤

ይታረቀዋል ፡ አሁንም ፡
—ረግሞት ፡ አይቀርም ።

ሠ ፡ ተጣልቶት ፡ አማሮት ፡ አሳቅሎት ፡ አይቀርም ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ ይታረቀዋል ።
ወ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ሞት ፡ የማይቀር ፡ ነው ፡ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ይመጣል ።

138　አባቴ ፡ ከካዱኝ ፡ በውነቱ ፡
ምን ፡ ያለፋኛል ፡ በከንቱ ፤

እኔ ፡ የምለው ፡ ከቤት ፡ ደጅ ፡
—አያት ፡ ብዬ ፡ ነበር ፡ እንጅ ።　　　(ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ላባቴ ፡ አባት ፡ ላያቴ ፡ ብዬ ፡ ነበር ፡ የምለፋው ፡ የምጥረው ፡ የምወጣው ፡ የምወርደው ።
ወ ፡ ጥረቴ ፡ ጭንቀቴ ፡ ሁሉ ፡ የምወዳትን ፡ ልጅ ፡ ለማየት ፡ ነበር ።

139　አንተ ፡ ያውድማ ፡ ቅረተኛ ፡
ተጠንቀቅና ፡ ነቅተህ ፡ ተኛ ፤

ታስወስዳለህ ፡ ምርትህን ፡
—ያፍሰዋልና ፡ አትመን ።

ሠ ፡ ሌባ ፡ ምርቱን ፡ ያፍሠዋል ፡ የውድማውን ፡ እኽል ፡ ይዝቀዋልና ፡ ተጠንቀቅ ።
ወ ፡ አድር ፡ ባይ ፡ ባፍ ፡ የሚደልል ፡ እንደበትን ፡ የሚጠባበቅ ፡ ነገረ ፡ ሠሪ ፡ አለና ፡ ተጠንቀቅ ።

140　አንቺም ፡ እንደዚህ ፡ ላትመቺ ፡
—እኔም ፡ ባልመጣሁ ፡ ወዳንቺ ።

ሠ ፡ ሳልመጣ ፡ በቀረሁ ፡ እቤቴ ፡ በዋልሁ ፡ በተሻለ ፡ ነበር ።

ወ ፡ እኔም ፡ ባልሽ ፡ ደረስሁ ፤ ይኸው ፡ መጣሁ ፤ አልቀረሁም ።

141 አንዘልቀውም ፡ ያንስ ፡ ደን ፡
—እንዲያው ፡ አለምናምን ።

ሠ ፡ ያለሥንቅ ፡ ያለጥሪት ፡ አይዘለቅም ፤ በባዶ ፡ እጅ ፡ መሄድ ፡ አይቻልም ።

ወ ፡ ዓለም ፡ ኀላፊ ፡ ጠፊ ፡ ነው ፤ ከንቱ ፡ ነው ።

142 አንድ ፡ ሰው ፡ የለ ፡ አስነሽ ፤
—ሁሉም ፡ ቀብሮ ፡ ተመላሽ ።

ሠ ፡ ሁሉ ፡ እመሬት ፡ ጨምሮ ፡ ተመላሽ ፡ ነው ፤ ለማስነሣት ፡ የሚችል ፡ የለም ፤

ወ ፡ ሰው ፡ የሚያውቀው ፡ ነገር ፡ ሠርቶ ፡ አሳብቆ ፡ ማጣላትን ፡ በተንኰል ፡ ያንዱን ፡ ቤት ፡ ማዘጋትን ፡ ነው ።

143 አንድ ፡ ይበቃኛል ፡ ከሞትኩ ፡ እኔ ፤
—ብዙ ፡ ከፋኝ ፡ ለምኔ ።

ሠ ፡ ብዙ ፡ ገናዥ ፡ አያስፈልገኝም ፤ ብገነዝ ፡ ባልገነዝ ፡ ግድ ፡ የለኝም ።

ወ ፡ እኔ ፡ ብዙ ፡ ከፋኝ ፤ ሆድ ፡ ባሰኝ ፤ እጅግ ፡ ተቀየምኩ ፤ ተመረርኩ ፤ ተበደልኩ ።

144 አወይ ፡ ዳኛ ፡ አወይ ፡ ዳኛ ፡
—ሌባን ፡ ወሰደው ፡ ቀማኛ ። (1)

ሠ ፡ ሌባ ፡ ሰረቀው ፤ ወይስ ፡ ቀማኛ ፡ ወሰደው ፤ ዳኛው ፡ የት ፡ ደረሰ ።

ወ ፡ እንደሌባ ፡ ያለ ፡ ድንገተኛ ፡ ሞት ፡ ዳኛውን ፡ ወሰደብን ፤ ነጠቀን ።

145 አውሬ ፡ ተነሥቶ ፡ ከበለሳ ፡
አጋዘንና ፡ ድፋርሳ ፡

ድፋርሳውማ ፡ ምን ፡ አለን ፤
—አጋዘን ፡ ጨረሰን ።

ሠ ፡ አጋዘን ፡ የሚባለው ፡ አውሬ ፡ አንዳንድ ፡ እያለ ፡ ጐዳን ።

ወ ፡ ሞት ፡ አጠቃን ፤ አንዳንድ ፡ እያለ ፡ እያጋዘ ፡ ጨረሰን ፤ ምንም ፡ አልተረፍንም ።

146 አያሳስትም ፡ ሰዓት ፡
ቀጠሮ ፡ ያከብራል ፡ ሞት ፤

(1) ዐፄ ፡ ኢዮአስ ፡ በሞቱ ፡ ባ፲፭ኛው ፡ ዓመት ፤ ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ ፪ኛው ፡ በነገሡ ፡ በመዠመሪያው ፡ ዘመን ፡ ሽፍታ ፡ በዛና ፡ በኢትዮጵያ ፡ ሁከትና ፡ ድብልቅልቅ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አንዲት ፡ የጐንደር ፡ ሴት ፡ ሰላም ፡ በመጥፋቱ ፡ ተቈርቍራ ፡ የተናገረችው ።

ሽማግሌ ፡ አይል ፡ ሕፃን ፡
ሞት ፡ ጠያቂ ፡ ሁሉን ።

አሁን ፡ ይመጣል ፡ በውነት ፡
—ሙት ፡ ብሎ ፡ አይቀርም ፡ ሞት ።

ሠ ፡ ምሎ ፡ አይቀርም ፤ ቀጠሮ ፡ ያከብራል ፤ ባለው ፡ ይረጋል ፤ ቃሉን ፡ ይጠብቃል ።

ወ ፡ ሞት ፡ ከተቀጠበው ፡ ቀን ፡ አያልፍም ፤ ዕድሜ ፡ ሲያልቅ ፡ ሰዓት ፡ ሲደርስ ፡ ይመጣል ፤ አይረሳም ፡ አይዘነጋም ።

147 አይፈራም ፡ እሱ ፡ በውነት ፡
ቢመጣም ፡ እንኳ ፡ ያ ፡ ሞት ፤
መኰንን ፡ ኀይሉን ፡ እዩት ፡
—በመድፉ ፡ ወጣበት ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ መድፉን ፡ ሄደበት ፤ ወጣበት ፤ እመድፉ ፡ ላይ ፡ ቆመበት ።

ወ ፡ የልዑል ፡ መኰንን ፡ አስከሬን ፡ በመድፍ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ተጓዘ ፤ ወደ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሄደ ።

148 አዳል ፡ ተሰማ ፡ መጣ ፡ ዘሩ ፡
—ተለውጠ ፡ ባገሩ ። (1)

ሠ ፡ ለዘር ፡ የሚሆነው ፡ እኽል ፡ ባገር ፡ ተፈልጎ ፡ ተገኝቶ ፡ መጣ ።

ወ ፡ አዳል ፡ የተሰማ ፡ ልጅ ፡ ላገሩ ፡ መድኅን ፡ መሥዋዕት ፡ ለመሆን ፡ ገሥ ገሥ ፡ መጣ ።

149 አዳምንና ፡ሔዋንን ፡
እንዳሳታቸው ፡ ሰይጣን ፡

—እኔም ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ባጠፋሁ ፡
ሳዝን ፡ እኖራለሁ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 2) ፡

ሠ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ባለማስተዋል ፡ በስሕተት ፡ በሠራሁት ፡ ሥራ ፡ ሳዝን ፡ ስተክዝ ፡ እኖራለሁ ።

ወ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ የሰው ፡ ዐይን ፡ ባጠፋሁ ፡ ሳለቅስ ፡ ስጸጸት ፡ እኖራለሁ ።

150 አገሬ ፡ አግባኝ ፡ ብላኝ ፡ እቴ ፡
እየታከተው ፡ ጕልበቴ ፡

ቢካፈሉትም ፡ የኛን ፡ ዕጣ ፡
—በይ ፡ መሬትም ፡ አናጣ ።

---

(1) ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ በራስ ፡ ደስታ ፡ ሞት ፡ ተናደው ፡ ጐዣምን ፡ ለማጥፋት ፡ በመጡ ፡ ጊዜ ፡ ራስ ፡ አዳል ፡ ከየአድባራቱ ፡ አርባ ፡ አርባ ፡ ሰው ፡ ልከው ፡ አገሩ ፡ ከወረራ ፡ ስለ ፡ ዳነ ፡ አዝማሪ ፡ መርሻ ፡ ያዘመረው ።

ሠ ፡ አትዘኚ ፡ ግድ ፡ የለሽም ፤ ርስት ፡ አንተከላለን ፤ መሬት ፡ እንመራለን ፤ ጕልት ፡ እናገኛለን ።

ወ ፡ ሻቾች ፡ ነን ፤ የምንቀበርበት ፡ መሬት ፡ አናጣም ፤ የኋላ ፡ ኋላ ፡ አፈር ፡ ይበላናል ፤ ምሥጥ ፡ ያነክተናል ።

151 አጋፋሪ ፡ አይቁም ፡ ከበሩ ፡
ምነው ፡ ሕዝብዎ ፡ መመረሩ ፤

አሁን ፡ ሳይጠሩት ፡ ገቢው ፡ ማነው ፡
—ቤትዎ ፡ ተፈሪ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ቤትዎ ፡ የሚታፈር ፡ ነው ፤ ደፍሮ ፡ ማን ፡ ይገባል ።

ወ ፡ ትዳርዎ ፡ ንብረትዎ ፡ ንጉሥ ፡ ተፈሪ ፡ (ቀ ፡ ኃ ፡ ሥ) ፡ ናቸው ፤ ማዕርግዎን ፡ ክብርዎን ፡ ያገኙት ፡ በርሳቸው ፡ ነው ።

152 አፋፍ ፡ ላይ ፡ ዘልቆ ፡ ጠርቶን ፡
—እረ ፡ ምን ፡ ብሎ ፡ አለን ፡ ይሆን ።

ሠ ፡ ምን ፡ ብሎ ፡ ነው ፡ ያለን ፤ ንገሩ ፡ ያለን ፡ ምንድነው ፤ የላከንስ ፡ ምን ፡ ይሆን ።

ወ ፡ ለመሆኑ ፡ ምን ፡ ተመገቡ ፡ ምን ፡ ብሉ ፡ ምንስ ፡ ቅመሱ ፡ ብሎ ፡ ጠይቋል ፡ ወይ ።

153 እኽል ፡ ሸምቼ ፡ ለመዝራት ፡
ክፈል ፡ ተባልኩኝ ፡ ብድራት ፤

አላውቀው ፡ እንኳ ፡ ቍናውን ፡
—ትንሽ ፡ ትልቅ ፡ ይሆን ።

ሠ ፡ የቍናውን ፡ መጠን ፡ ትንሽ ፡ ይሁን ፡ ትልቅ ፡ አለካሁትም ፤ አልገመትሁትም ።

ወ ፡ የአምላክ ፡ ነገር ፡ አይታወቅም ፤ አልባሌውን ፡ ሰው ፡ ያነሣዋል ፤ በሥልጣን ፡ ያሳድገዋል ።

154 እላይ ፡ እታች ፡ ቤት ፡ ሁለት ፡ ቦታ ፡
መርማሪዎች ፡ አሉ ፡ የጸጥታ ፤

—የታችኛውስ ፡ ያደላል ፤
—የላይኛው ፡ ነው ፡ ትክክል ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ ከታች ፡ ቀበሌ ፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ የላይኛው ፡ ፍርድ ፡ ቤት ፡ ይሻላል ፤ ፍርድ ፡ ይመለከታል ፤ ፍትሕ ፡ ያያል ፤ ሕግን ፡ ይጠብቃል ።

ወ ፡ ያምላክ ፡ ፍርድ ፡ ትክክል ፡ ነው ፡ አይዛባም ፤ አይሻርም ፡ ጕድለት ፡ የለበትም ።

155 እሑድ ፡ ቅዳሜ ፡ ቢሆን ፡
እበላ ፡ ነበር ፡ ምሳዬን ፤

እንዲህ ፡ በጦም ፡ ቀን ፡ የምዞረው ፡
—ለጊዜ ፡ ማድረሻ ፡ ነው ።

ሠ ፡ የምሳ ፡ መብሊያ ፡ ሰዓት ፡ እስኪደርስ ፡ መቈያ ፡ መዳረሻ ፡ ነው ።
ወ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ ዕለተ ፡ ሞትን ፡ መጠባበቂያ ፡ ጊዜ ፡ ማሳለፊያ ፡ ነው ።

156 እመቤታችን ፡ አርግዛ ፡
በሄሮድስ ፡ አዝና ፡ ተክዛ ፡

ልጅዋም ፡ አልዳነ ፡ እሷም ፡ ሞተች ፡
—ወልዳ ፡ አዝላ ፡ የነበረች ።

ሠ ፡ ልጅ ፡ ወልዳ ፡ በአንቀልባ ፡ በዠርባዋ ፡ አዝላ ፡ ነበር ።
ወ ፡ ወልድን ፡ አዝላ ፡ የነበረች ፡ እመቤታችንና ፡ ልጅዋም ፡ ጌታችን ፡ እን ደ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሞቱ ።

157 እመቤታችን ፡ ግብጽ ፡ ወርዳ ፡
ከየሩሳሌም ፡ ተሰዳ ፡

የተቀበለችው ፡ ሥቃይ ፡
—ሰው ፡ ወልዳ ፡ አይደለም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ሥቃይ ፡ የተቀበለችው ፡ መከራ ፡ ያየችው ፡ ግፍ ፡ የደረሰባት ፡ ልጅ ፡ በመውለዷ ፡ አይደለም ፡ ወይ ።
ወ ፡ ወልድ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ ሰው ፡ አምላክ ፡ ሆነ ፤ በወልድ ፡ ልደት ፡ ያዳም ፡ ልጅ ፡ ከበረ ፡ (ምስጢረ ፡ ሥጋዌ) ።

158 እማውቀው ፡ ሰው ፡ ኀረ ፡ ቤቴ ፡
ሲሄድ ፡ እያየሁ ፡ በፊቴ ፡

ሳልጠራው ፡ ቀረሁ ፡ ያን ፡ ሰውዬ ፡
—አለምናምን ፡ ብዬ ።

ሠ ፡ የሚበላ ፡ ሳይኖር ፡ ባዶ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሳላስተናግደው ፡ ቀረሁ ፤ ሳልጋብዘው ፡ በውጭ ፡ ሰደድኩት ።
ወ ፡ የሥጋዬን ፡ ነገር ፡ እያየሁ ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ አምኜ ፡ የነፍሴን ፡ ነገር ፡ ዘነጋሁት ፤ ረሳሁት ።

159 ሩቅ ፡ ዘመቻ ፡ ዘምቼ ፡
ሁለት ፡ ጥገቶች ፡ አግኝቼ ፡

በምን ፡ ይበሏል ፡ ባዋዜ ፡
—ይህነን ፡ አልቦ ፡ ጊዜ ።

ሠ ፡ እንግዲህ ፡ ይህችን ፡ ላም ፡ አልቦ ፡ ወተቷን ፡ መጠጣት ፡ ነው ።
ወ ፡ ደኅና ፡ ጊዜ ፡ የለም ፤ ሰዓቱ ፡ አልቋል ፤ የችግርና ፡ የመከራ ፡ ዘመን ፡ ነው ።

160 ራሴን ፡ አሞኝ ፡ ብታገም ፡
በሆዴ ፡ ረጋ ፡ ደም ፤

ምነው ፡ ቤተ ፡ ክሲያን ፡ ባልገባሁ ፡
—ደም ፡ ሆኜ ፡ በቀረሁ ።

ሠ ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ በግዳጅ ፡ ምክንያት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ባልሄድኩ ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ባልገባሁ ።

ወ ፡ ለመሞት ፡ ለመቀበር ፡ ባልተፈጠርሁ ፤ ሳልወለድ ፡ ደም ፡ ሆኜ ፡ ብቀር ፡ በተሻለኝ ፡ ነበር ።

161 እሰው ፡ ማሽላ ፡ ገብተህ ፡
ወይ ፡ አልተቀመጥህ ፡ ቆመህ ፡

በሩቅ ፡ ያየህ ፡ ሰው ፡ ፈጀው ፡ ይላል ፤
—ቈርጦ ፡ መሄድ ፡ ይሻላል ።

ሠ ፡ እኽል ፡ ውስጥ ፡ ቆመህ ፡ ከምትቀር ፡ የምትፈልገውን ፡ እሸት ፡ ቈርጠህ ፡ ብትሄድ ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ መናቅ ፡ ጨርሶ ፡ ትቶ ፡ መሄድ ፡ በፍጹም ፡ ልብ ፡ መመነን ፡ ይጠቅማል ።

162 እሱም ፡ ሥላሴ ፡ ተቀኘ ፡
የሚመልሰውም ፡ አልተገኘ ፤

ንባቡ ፡ አማረ ፡ እያላችሁ ፡
ለምን ፡ ታሳልፉታላችሁ ፡

ዜማ ፡ ሰበረ ፡ ብላችሁ ፡
—መልሱት ፡ እባካችሁ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ አልሆነም ፡ በሉት ፤ አቃኑለት ፤ መልሳችሁ ፡ አስተካክሉለት ።

ወ ፡ እባካችሁ ፡ ትችሉ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ልዑል ፡ መኰንንን ፡ ከሞት ፡ አድኑት ፤ አትርፉት ፤ አስቀሩት ።

163 እሳት ፡ ይዥለሁ ፡ በገል ፡
ውስጡን ፡ ሸፍኜ ፡ በቅጠል ፤

አላነደውም ፡ ይጢስ ፡
—ቀን ፡ እወጣ ፡ ድረስ ።

ሠ ፡ እስኪነጋ ፡ ቀን ፡ እስኪወጣ ፡ ይጭስ ።

ወ ፡ ደኅና ፡ ጊዜ ፡ እስኪመጣ ፡ ክፉው ፡ ወራት ፡ እስኪያልፍ ፡ እቈያለሁ ፤ እታገሣለሁ ።

164 እስቲ ፡ አታድርገኝ ፡ የሰው ፡ ሞኝ ፤ (1)
—ብስል ፡ ሰው ፡ እንጂ ፡ ነኝ ። (መዲ ፡ ቍ ፡ 60) ፡

ሠ ፡ ሠዓሊም ፡ ብሆን ፡ መናቅ ፡ የለብኝም ፤ ወንድነት ፡ አለኝ ፤ ሰው ፡ ነኝ ፡ እኮ ።

ወ ፡ መመራመርና ፡ ማስተዋል ፡ የምችል ፡ ባለአእምሮ ፡ ፍጡር ፡ ነኝ ።

165 እስቲ ፡ ጠይቁልኝ ፡ ወንድሜን ፡
—ደሞ ፡ አገርሸቶት ፡ እንደሆን ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ታሞ ፡ በሽታው ፡ ተመልሶበት ፡ ተኝቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እስቲ ፡ ጠይቁልኝ ።

ወ ፡ አገር ፡ መግዛት ፡ ርስት ፡ ጕልት ፡ ማግኘትና ፡ መሾም ፡ ፈልጎት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እስቲ ፡ ጠይቁልኝ ።

166 እቤቴ ፡ ጓሮ ፡ ዘርቼው ፡
—ወይኔ ፡ አፈራልኝ ፡ ልቅመሰው ።

ሠ ፡ ወይኔ ፡ አፈራልኝ ፤ ሸተልኝ ፤ ደርሶልኛል ፤ ፍሬ ፡ ሊሰጠኝ ፡ ነው ።

ወ ፡ ወዮታን ፡ ሐዘንን ፡ አተረፍኩ ፤ ልቅሶዬን ፡ ይዤ ፡ ቀረሁ ።

167 እናንት ፡ የጐዣም ፡ መኳንንት ፡
ጭቃ ፡ አይንካችሁ ፡ በክረምት ፤

ባገራችሁ ፡ በወንዛችሁ ፡
—ወየው ፡ ወየው ፡ በራችሁ ። (2)

ሠ ፡ በራችሁ ፡ ጭቃ ፡ ነው ፤ ምድራኻችሁ ፡ ማጥ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ የእግር ፡ ማረፊያና ፡ መተላለፊያ ፡ አይገኝም ።

ወ ፡ በራችሁ ፡ ሮጣችሁ ፡ አምልጡ ፤ እግራችሁን ፡ አውጡ ።

168 እኔም ፡ በልቼ ፡ አልጠገብሁ ፤
—እንዲያው ፡ አ ፡ ብዬ ፡ ቀረሁ ።

ሠ ፡ አፌን ፡ ከፍቼ ፡ ቀረሁ ፤ ሳልከድን ፡ ተውሁት ፤ እንዳላቀቅሁት ፡ ቀረ ።

ወ ፡ እንዲያው ፡ አብዬ ፡ ቀረሁ ፤ ቃላባይ ፡ ሐሰተኛ ፡ ወላዋይ ፡ ሆኜ ፡ ተገኘሁ ።

(1) በጥንት ፡ ዘመን ፡ የእጅ ፡ ብልኀት ፡ ዐዋቂዎች ፡ ይናቁ ፡ ነበርና ፡ ታላቁ ፡ ራስ ፡ ኀይሉ ፡ ዲማ ፡ ጊዮርጊስን ፡ ያሠሩት ፡ የነበረውን ፡ አለቃ ፡ ቀጸላ፡ የሚባለውን፡ አንድ ፡ ያስቀየመው ፡ ሰው ፡ በዝቅተኛ ፡ መንፈስ ፡ ስለ ፡ ተመለከተው ፡ የተናገረው ።

(2) ደጃች ፡ ብሩ ፡ አልገዛም ፡ ስላሉ ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ጐዣምን ፡ በወረሩ ፡ ጊዜ ፡ ሊቀ ፡ መኳስ ፡ መርሻ ፡ የሚባል ፡ አዝማሪ ፡ በፈሊጥ ፡ ያገሩን ፡ ባላባቶች ፡ ለማዳን ፡ እሰፈር ፡ ገብቶ ፡ ያዘመረው ።

169 እኔም ፡ ተሠራሁ ፡ ጠጕሬን ፡
አላፍ፡ር ፡ ብዬ ፡ ነውሬን ፤

ሌሎች ፡ ሲላጩ ፡ እያየ ፡ ዐይኔ ፡
—ለምን ፡ ተሠራሁ ፡ እኔ ።

ሠ ፡ ጠጕሬን ፡ ባልተሠራሁ ፡ ቈንዳላ ፡ ባልሆንሁ ፡ ባሳደግሁትና ፡ ባጐፈ
ርሁት ፡ በተሻለኝ ፡ ነበር ።

ወ ፡ በሞት ፡ ለመጥፋት ፡ ባልተፈጠርሁ ፤ ሰው ፡ ሳልሆን ፡ በቀረሁ ።

170 እኔስ ፡ ምንም ፡ ምን ፡ አላዝን ፡
—ሳይደላኝ ፡ ጊዜ ፡ እኔን ።

ሠ ፡ ጊዜው ፡ አልተመቸኝም ፤ ዘመኑ ፡ አልሆነኝም ፤ ይህ ፡ ዓመት ፡ አልደ
ላኝም ።

ወ ፡ ውርደት ፡ ብስጭት ፡ ሲደርስብኝ ፡ እንደ፡ ምን ፡ አላዝንም፤ ሲከፋኝ፡
ሆድ ፡ ሲብሰኝ ፡ ለምን ፡ አልተከዝም ፤ አልጸጸትም ።

171 እኔስ ፡ አልችልም ፡ ዘንድሮ ፡
—እንዲህ ፡ ታምሶ ፡ ኑሮ ።

ሠ ፡ ተጨቃጭቆና ፡ ተነዛንዞ ፡ ኑሮ ፡ ሰለቸኝ ፤ አምባጓሮው ፡ መረረኝ ፤
ታከተኝ ።

ወ ፡ ዘንድሮ ፡ መታሰር ፡ መጉላላት ፡ በዛብኝ ፡ ንዝንዙ ፡ አበቀተኝ ።

172 እኔስ ፡ ፈራሁት ፡ ያን ፡ ሰውዬ ፡
—መሬት ፡ ይቀራል ፡ ብዬ ።

ሠ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ክፉኛ ፡ ወደቀ ፡ እንጂ ፡ የሚነሳ ፡ አልመሰለኝም ፡ በዚያው ፡
እንዳይቀር ፡ እፈራለሁ ።

ወ ፡ ምንም ፡ ዕድሜ ፡ ቢበዛ ፡ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ መሞትና ፡ ዐፈር ፡ መሆን ፡
አይቀርም ።

173 እኔና ፡ ሞት ፡ ባንድነት ፡
ገብተን ፡ ተማሪ ፡ ቤት ፡

እኔ ፡ ገና ፡ ስቈጥር ፡
—እሱ ፡ ያግዝ ፡ ገሥመር ።

ሠ ፡ እሱ ፡ ሀ ፡ ግእዝ ፡ ለ ፡ ግእዝ ፡ እያለ ፡ ፊደልን ፡ ይቈጥራል ፤ ግእ
ዙንና ፡ ካዕቡን ፡ ለመለየት ፡ ይጣጣራል ፤ የፊደልን ፡ ዘር ፡ ለማወቅ ፡
ይታገላል ።

ወ ፡ ሞት ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ እየገደለ ፡ በየጊዜው ፡ ይወስዳል ፤ ሙታንን ፡
ያግዛል ፤ ወደ ፡ መቃብር ፡ አንድ ፡ ባንድ ፡ ያወርዳል ።

174 እኔስ ፡ ዐዳዩ ፡ በደለኝ ፤
—አዟሪ ፡ ሥጋ ፡ ሰጠኝ ።

ሠ ፡ አዟሪ ፡ የሚባለውን ፡ ሥጋ ፡ ዳረገኝ ፤ አጐረሠኝ ፤ በዚህ ፡ ደጐመኝ ፤ ሸነገለኝ ።

ወ ፡ የሚያንከራትት ፡ ዕረፍት ፡ የሚነሣ ፡ ተፈጥሮን ፡ ዐደለኝ ፤ ዘዋሪ ፡ ሰውነትን ፡ ሰጠኝ ።

175 እኔ ፡ ወዳጄን ፡ ልጠይቅ ፡
መጥቼ ፡ ነበር ፡ ከሩቅ ፤

ገባ ፡ ይሉኛል ፡ ወደ ፡ ጓዳ ፡
የቤቱን ፡ ዕቃ ፡ ሊያሰናዳ ።

ባጠገቡ ፡ ዕቃ ፡ እያለው ፡
—ለምን ፡ የፊቱን ፡ ረሳው ።

ሠ ፡ እፊቱ ፡ የተቀመጠውን ፡ ዕቃ ፡ ለምን ፡ ሳያዘጋጀው ፡ አለፈ ፤ ሰግዶድ ፡ ሳያደርገው ፡ ቀረ ፤ ሳይሰበስበው ፡ ሄደ ።

ወ ፡ ለምን ፡ የፊቱን ፡ ረሳው ፤ የቀድሞውን ፡ ውለታ ፡ እንዴት ፡ ረሳው ፤ ለ ምን ፡ የጥንቱን ፡ ሁናቴ ፡ ዘነጋው ፤ ያለፈውን ፡ አልተገነዘበም ።

176 እንኳን ፡ በሬና ፡ ትልቅ ፡
—በቤቴም ፡ ጥጃ ፡ አላውቅ ፤

እንዲያውስ ፡ ለምን ፡ ተዠምሮ ፡
ይኸ ፡ የዋዛ ፡ ኑሮ ።

ሠ ፡ እንኳን ፡ በሬ ፡ ጥጃም ፡ የለኝ ፤ በግቢዬም ፡ ከብት ፡ ጮኾበት ፡ አያ ውቅ ።

ወ ፡ ትዳር ፡ የለኝም ፤ በቤቴ ፡ ተጥዶበትም ፡ አያውቅ ፤ ጐዠም ፡ አል ወጣሁ ፤ ብቸኛ ፡ ነኝ ።

177 እንደ ፡ ይብራ ፡ እንደ ፡ ሳቢሳ ፡
ምነው ፡ ለወንዡ ፡ የምሣሣ ፤

ማን ፡ አሳየብኝ ፡ ጥበቡን ፡
—የውሃ ፡ ዳር ፡ ቤቴን ።　　(ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ በውሃ ፡ አጠገብ ፡ በባሕር ፡ አካባቢ ፡ በወንዝ ፡ ዳር ፡ ያለ ፡ ቤቴን ፤ ማን ፡ አሳየብኝ ፤ እንዴት ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ጠቈመብኝ ፤ መራብኝ ፡ አመለከተብኝ ።

ወ ፡ ትዳሬ ፡ እንደ ፡ ነገሩ ፡ ሲሆንና ፡ የማድረው ፡ ጥሬ ፡ ቈርጥሜ ፡ ውሃ ፡ ጠጥቼ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ለምን ፡ ይመለከቱኛል ።

178 እንዳላበራ ፡ ጧፌ ፡ አለቀ ፤
—የሠሚ ፡ አገሩ ፡ ራቀ ።

ሠ ፡ መብራት ፡ እንዳላበራ ፡ ጧፌ ፡ አለቀ ፤ ሌላም ፡ ጧፍ ፡ እንዳልነክር፡ ሠም ፡ የለኝ ፤ በቅርብ ፡ አይገኝም ።

ወ ፡ የሚሰማ ፡ ታጣ ፤ አቤቱታ ፡ ተቀባይ ፡ ዳኛ ፡ ጠፋ ።

179 እንዴት ፡ ከርመሃል ፡ እያሉ ፡
ይጠይቁኛል ፡ ሰዎች ፡ ሁሉ ፡
የዘንድሮውን ፡ አላውቅም ፤
—ባምናው ፡ አልጐዳም ።

ሠ ፡ ባለፈው ፡ ዓመት ፡ አልተጐዳሁም ፤ ዓምና ፡ አልተቸገርሁም ፡ ነበር ፤ እንደ ፡ ዘንድሮ ፡ ሆኜ ፡ አላውቅም ።

ወ ፡ አምላክን ፡ በማመኔ ፡ አልጐዳም ፤ አልቸገርም ፤ ጥፋት ፡ አያገኝኝም ።

180 እንግዲህ ፡ ሰው ፡ አይኵራ ፡
አምላክ ፡ በሠራው ፡ ሥራ ፤
መላ ፡ ሐባሻን ፡ ያዳነው ፡
—ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ነው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ያዳነን ፡ ከሞት ፡ ያተረፈን ፡ የሥላሴ ፡ ኃይል ፡ ነው ።

ወ ፡ ን ፡ ነ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ባስገኘው ፡ ነጻነት ፡ ሌላው ፡ አይታበይ ፤ በርሱ ፡ ድካም ፡ የቀረው ፡ አይዝናና ፤ አይፎክር ።

181 እንዲህ ፡ ሸልመው ፡ ሊሰጡኝ ፡
—ባዝና ፡ አከረሙኝ ። (1) (መዲ ፡ ቍ ፡ 121) ፡ (ራስ ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ እንዲህ ፡ ሊያስደስቱኝ ፡ አሳዘኑኝ ፤ አስቀየሙኝ ፤ አስከፉኝ ፤ በግዞት ፡ አኖሩኝ ።

ወ ፡ «አዝና» ፡ ከሚባል ፡ ቦታ ፡ አባጁኝ ፤ አከረሙኝ ፤ እዚያ ፡ አሰነበቱኝ ፤ አስቀመጡኝ ።

182 እንግዳ ፡ አይደለሽ ፡ ባለቤት ፤
ገረድ ፡ አይደለሽ ፡ እመቤት ፤
ከቤት ፡ እንጀራ ፡ ሲጋገር ፡ ባበላሽው ፡ ነበር ፡
—ምነዋ ፡ እኔስ ፡ ባልኖር ። (2)

(1) ራስ ፡ ደረሶ ፡ ከንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ተቀያይመው ፡ «አዝና» ፡ ከሚባል ፡ ቦታ ፡ በግዞት ፡ ከቈዩ ፡ በኋላ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ማዕርግ ፡ ስለ ፡ ተሰጣቸው ፡ ኅሊናቸውን ፡ በመውቀሥ ፡ ጸጸታቸውንና ፡ ደስታቸውን ፡ የገለጡበት ።

(2) አንዲት ፡ ሴት ፡ የመዠመሪያ ፡ ባሏ፡ የሚበላው ፡ አጥቶ ፡ ከቤቷ ፡ ሄዶ ፡ ቢለምን፡ ፊት ፡ ነሥታ ፡ ስለ ፡ መለሰችው ፡ እቤት ፡ ያለው፡ ባሏ ፡ ነገሩን ፡ ያውቅ ፡ ነበርና ፡ ታዝቦ ፡ ወየው ፡ ለካ ፡ ለኔም ፡ ጊዜ ፡ ይኸው ፡ ነው ፡ ከሷ ፡ ጋራ ፡ ባልኖርስ ፡ ብሎ ፡ የተናገረው ።

ሠ ፡ እኔ ፡ እቤት ፡ ባልገኝ ፡ ባልኖርስ ፡ ለምን ፡ አንቺ ፡ አልጋበዝሽውም ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ ጨካኝ ፡ ከሆንሽ ፡ እኔም ፡ ካንቺ ፡ ጋራ ፡ አብሬ ፡ መኖርን ፡ አልፈቅድም ፤ ትዳሬን ፡ ጠልቻለሁ ፤ ብቸኛ ፡ ሆኜ ፡ መንኜ ፡ መቀመጥን ፡ እመርጣለሁ ።

183 እኛም ፡ አየነው ፡ ሁሉንም ፤
—እንዳንች ፡ ያለ ፡ አዳራሽ ፡ የለም ።

ሠ ፡ ያንችን ፡ ቤት ፡ የመሰለ ፡ ትልቅ ፡ አዳራሽ ፡ የለም ፤ ከሁሉ ፡ ይበልጣል ፤ የሚወዳደረው ፡ ጠፋ ።

ወ ፡ እንዳንቺ ፡ ያለ ፡ አነካኪ ፡ አላኳሽ ፡ ጠባየ ፡ መጥፎ ፡ አይገኝም ፡ አልተፈጠረም ።

184 እወጥ ፡ ቤት ፡ ሄጄ ፡ ድንገት ፡
ቋንጣ ፡ ጠብሼ ፡ ለመብላት ፡

ወድቄ ፡ ነበር ፡ እሳት ፡ ላይ ፡
—ሥጋ ፡ ሥጋዬን ፡ ሳይ ።

ሠ ፡ የሚጠበሰውን ፡ ሥጋ ፡ ስመለከት ፡ እሳት ፡ ሊፈጀኝ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ሥጋዊ ፡ ኑሮን ፡ በመመልከት ፡ የነፍሴን ፡ ነገር ፡ በመዘንጋት ፡ እገሃነመ ፡ እሳት ፡ ልገባና ፡ ልኰነን ፡ ነው ።

185 እዚያ ፡ ላይ ፡ ሆነህ ፡ ብትጠራኝ ፡
አቤት ፡ እንዳልል ፡ ድምጥ ፡ የለኝ ፤

እረ ፡ የት ፡ ሆኜ ፡ ልጠብቅ ፡
—መምጫህ ፡ አይታወቅ ።

ሠ ፡ የምትመጣበት ፡ ጊዜ ፡ አይታወቅም ፤ ሲጠብቁህ ፡ ትቀራለህ ፤ ሳያስቡህ ፡ ትመጣለህ ።

ወ ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ አመጣጥህ ፡ ድንገት ፡ ነው ፤ ቀጠሮ ፡ የለህም ፤ የመምጫህ ፡ ጊዜ ፡ አይታወቅም ።

186 እዚያ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ሲጠራኝ ፡
ባልንጀሮቼ ፡ ሳይነግሩኝ ፡

ባልሰማ ፡ እንጂ ፡ ነው ፡ ዝምታዬ ፡
—አቤት ፡ አቤት ፡ ጌታዬ ።

ሠ ፡ አቤት ፡ አቤት ፡ መጣሁ ፤ ጥሪህን ፡ አዳምጫለሁ ፤ ድምፅህን ፡ ሰምቻለሁ ።

ወ ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ሆይ ፡ ይቅር ፡ በለኝ ፤ ማረኝ ፡ ከክፉ ፡ አድነኝ ፤ ከመዓቱ ፡ ሰውረኝ ።

187 እዚያ ፡ ላይ ፡ ያለች ፡ ሸክላ ፡ ሠሪ ፡
ድኻ ፡ ናት ፡ አሉ ፡ ጦም ፡ አዳሪ ፤

ማን ፡ አስተማራት ፡ ጥበቡን ፡
—ገል ፡ ዐፈር ፡ መሆኑን ።

ሠ ፡ ዐፈር ፡ ሸክላ ፡ መሆኑን ፡ ሸክላ ፡ ከዐፈር ፡ መሠራቱን ፡ ማን ፡ ገለ ጠላት ፤ ይህን ፡ ብልኅት ፡ ማን ፡ ነገራት ፤ እንደዚህ ፡ ያለውን ፡ ጥበብ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ አስረዳት ።

ወ ፡ ገላ ፡ ዐፈር ፡ ትቢያ ፡ ነው ፤ ሰውነት ፡ በመቃብር ፡ ወደ ፡ መሬትነቱ ፡ ይለወጣል ።

188 እያለ ፡ ከርሱ ፡ የሚሻል ፡
ሁሉም ፡ ለሥጋ ፡ ያደላል ፤

ልኳንዳ ፡ ታርዶ ፡ ስላየሁ ፡
—እፈርስ ፡ ምድር ፡ ላይ ፡ ቆሚያለሁ ። (በ ፡ ማ)፡

ሠ ፡ ከብት ፡ ከታረደበት ፡ ፈርስ ፡ ካለበት ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ ቆሚያለሁ ።

ወ ፡ ልሞት ፡ ልፈርስ ፡ ልበሰብስ ፡ ለጊዜው ፡ በምድር ፡ ላይ ፡ እገኛለሁ ።

189 እግዚአብሔር ፡ ወርዶ ፡ ከምድር ፡
ፍጥረቱን ፡ ዋና ፡ ሲያስተምር ፡

አፋፍ ፡ ላይ ፡ ዘልቀን ፡ ብናየው ፡
—እያጣለቀ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ እባሕር ፡ ውስጥ ፡ እየደፈቀ ፡ አንዱ ፡ አንዱን ፡ እንዲያጣልቀው ፡ እያ ደረገ ፡ ዋና ፡ ያስተምራል ።

ወ ፡ በማጣት ፡ በመቸገር ፡ ሰዉ ፡ አለቀ ፤ የሚቀምሰው ፡ ባለማግኘቱ ፡ ሞተ ።

190 እረ ፡ ተው ፡ ርዳኝ ፡ እባክህ ፡
—አንተ ፡ ሰው ፡ በናትህ ። (መ . ቁ ፡ 194 )

ሠ ፡ በወለደችህ ፡ በናትህ ፡ ርዳኝ ፤ ተማጥኜሃለሁ ፤ ተስፋዬም ፡ አለኝታ ዬም ፡ ባንተ ፡ ላይ ፡ ነው ።

ወ ፡ አምላክ ፡ በናትህ ፡ በማርያም ፡ ሰው ፡ ነህ ፤ ሥጋ ፡ ለብሰሃል ፡ (ምስ ጢረ ፡ ሥጋዌ) ።

191 ከልፍኝ ፡ ተቀምጦ ፡ ማስጠራት ፡
አዳራሽ ፡ ገብቶ ፡ ማብላት ፡
ከገዳም ፡ ሄዶ ፡ መስጠት ፡

ከግንቦት ፡ ወዲህ ፡ መቼ ፡ ታ(የ)ዬ ፤
—እባክህ ፡ ቀረ ፡ ጌታዬ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ጌታዬ ፡ ሆይ ፡ ልምድህ ፡ ተረሳ ፤ ቸርነትህ ፡ ተዘነጋ ፤ በጎ ፡ አድራጎ ትህ ፡ ቀረ ፤ እንዳልነበረ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ እይ ፡ ሰው ፡ መሆን ፡ የማይሞት ፡ ሰው ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ሞተ ፡ ተቀበረ ፤ ከሱ ፡ ወዲያ ፡ እባክህ ፡ ስጠኝ ፡ አብላኝ ፡ አጠጣኝ ፡ የሚሉት ፡ ሰው—ጠፉ ፤ የሚለመን ፡ ታጣ ።

192 ከመንገድ ፡ ቈየኝ ፡ ብየዋለሁ ፤
ከቶ ፡ ምን ፡ ይገዠ ፡ እሄዳለሁ ፤

ያ ፡ ሞት ፡ መምጣቱ ፡ ቍርጥ ፡ ነው ፤
—ተቃጥሮ ፡ አይረሳም ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ቀጠሮ ፡ አይዘነጋም ፤ በቃሉ ፡ ይገኛል ፤ ቀጠሮ ፡ ያከብራል ።

ወ ፡ ሞት ፡ ሰውን ፡ ረስቶ ፡ አይተውም ፤ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ይወስደዋል ፤ ሰዓቱ ፡ ሲደርስ ፡ ይመጣል ።

193 ከሚበልጠው ፡ ሁሉ ፡
እረ ፡ ተማሩ ፡ በሉ ፤
እናንተ ፡ ሰዎች ፡ አስተውሉ ፤
—ከዳ ፡ ከዳ ፡ አትበሉ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ከወለላው ፡ ማር ፡ እንጂ ፡ ከዳውን ፡ አትብሉ ።

ወ ፡ ታማኝነት ፡ አይጕደላችሁ ፤ የክሕደትን ፡ ተግባር ፡ ተዉት ፤ ሁለት ፡ ልብ ፡ አትሁኑ ።

194 ከሰማየ ፡ ሰማያት ፡ ወርደህ ፡
ከድንግል ፡ ማርያም ፡ ተወልደህ ፡

ትጨክናለህ ፡ ምነው ፡
—አምላክ ፡ በናትህ ፡ ሰው ። (መ . ቁ ፡ 190 )

ሠ ፡ በናትህ ፡ ወገኖች ፡ በአዳም ፡ ልጅ ፡ ፊትህን ፡ አትመልስ ፤ ራራልን ፤ ይቅር ፡ በለን ፤ ማረን ።

ወ ፡ አምላክ ፡ በናትህ ፡ በማርያም ፡ በኩል ፡ ሰው ፡ ነህ ፤ ያዳምን ፡ ሥጋ ፡ ለብሰሃል ፡ (ምስጢረ ፡ ሥጋዌ) ።

195 ከሳ ፡ ደረቴ ፡ መነመነ ፤
ሕመም ፡ የለብኝ ፡ ምንድን ፡ ሆነ ፤

የዱሮ ፡ መልኬ ፡ ይጥፉኝ ፡ ወይ ፡
—ሰው ፡ ኑሮውን ፡ መሳይ ።

ሠ ፡ ሰውን ፡ መጥፎ ፡ ኑሮ ፡ ያጐሳቍለዋል ፤ መልካም ፡ ኑሮ ፡ ያቀማጥለዋል ፤ ያሳምረዋል ፤ ያደደሩ ፡ ግምት ፡ በመልኩ ፡ ይታወቃል ።

ወ ፡ ሰው ፡ በኑሮው ፡ ይገመታል ፤ ሀብታም ፡ ይሁን ፡ ደሀ ፡ በሁናቴው ፡ ይለያል ።

196 ከቤተ ፡ ክሲያን ፡ ኳሮ ፡ ጥጥ ፡ ዘርቼ ፡
አበጀዋለሁ ፡ ኰታኰቼ ፤

የልብሴስ ፡ ነገር ፡ ተይዟል ፤
—አፈራለሁ ፡ ብሏል ።

ሠ ፡ ፍሬ ፡ እሰጣለሁ ፤ ዘር ፡ አበረክታለሁ ፤ ሰብልም ፡ አስገኛለሁ ፡ ብሏል ።
ወ ፡ መቃብር ፡ ይጠብቀኛል ፤ መፍረስ ፡ መበስበስ ፡ አለብኝ ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ መሬትነት ፡ እለወጣለሁ ፤ ትቢያ ፡ እሆናለሁ ።

197 የቤቴ ፡ በታች ፡ አታክልት ፡
ወይን ፡ ትርንጎ ፡ ሽንኵርት ፤

ትርንጎዬንስ ፡ አስበላሁ ፤
—ወይኔን ፡ ይዤ ፡ ቀረሁ ።

ሠ ፡ የወይኔ ፡ ሰብል ፡ ብቻ ፡ ቀረኝ ፤ እሱ ፡ ብቻ ፡ ተረፈኝ ።
ወ ፡ ወዮታን ፡ ጸጸትን ፡ አተረፍኩ ፤ አልቅሼ ፡ ቀረሁ ፤ ትርፌ ፡ ሐዘን ፡ ብቻ ፡ ሆነ ።

198 ከብት ፡ ብገዛ ፡ ከረኛ ፡
ተያዘብኝ ፡ አሉ ፡ በዳኛ ፤

ጕዳቴን ፡ ሁሉ ፡ ብነግረው ፡
—የማያልፍልኝ ፡ ነው ።

ሠ ፡ በዋቢነት ፡ አያልፍልኝም ፤ ተያዥ ፡ ሊሆነኝ ፡ አይችልም ፤ መድን ፡ አይሆነኝም ።
ወ ፡ ሀብት ፡ አግኝቼ ፡ ችግሬ ፡ አያልፍልኝም ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ ራሴን ፡ አልችልም ፤ ተስፋም ፡ የለኝ ።

199 ከብት ፡ ጠፍቶብኝ ፡ በሌሊት ፡
ስፈልግ ፡ አደርኩ ፡ ስዋትት ፤

እነግርሃለሁ ፡ ተጣርቼ ፡
—ይሽን ፡ ቀን ፡ ወጥቼ ፡ አይቼ ።

ሠ ፡ ቀን ፡ በብርሃን ፡ አስረዳሃለሁ ፤ ሲነጋ ፡ አይቼ ፡ እነግርሃለሁ ።
ወ ፡ ይህ ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ አልፎልኝ ፡ ተናግሬው ፡ ተጫውቼው ።

200 ከኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ የምትውሉ ፡
ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ እንዳትሉ ፤

እኛም ፡ ሰምተናል ፡ ባዋጅ ፡
—የረጋ ፡ ሰው ፡ ወዳጅ ።

ሠ ፡ የማይከዳውን ፡ አብሮ ፡ የሚኖረውን ፡ የሚወድ ፡ ነው ።
ወ ፡ ደጎና ፡ ባሕርይ ፡ ያለውን ፡ የማይቸኵል ፡ ጭምት ፡ ሰውን ፡ ይወዳል ።

201 ከወዲያ ፡ መጣሁ ፡ ከደላንታ ፡
ማር ፡ ልገዛ ፡ ለጌታ ፤
ባየውም ፡ ደስ ፡ አላለኝ ፤
—እኔ ፡ ከዳ ፡ መሰለኝ ።

ሠ ፡ ወለላ ፡ የሌለበት ፡ ከዳ ፡ ማር ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ ተጠራጠርሁ ፤ ንጹሕ ፡ ማር ፡ አልመሰለኝም ።

ወ ፡ እከዳ ፡ እኰበልል ፡ መሰለኝ ፤ ከዛሬ ፡ ነገ ፡ ሀያጅ ፡ ነኝ፤ የምቈይ ፡ አይመስለኝም ፤ አልተመቸኝም ።

202 ከወዲያ ፡ ወዲህ ፡ ተጣርተው ፡
ሙታን ፡ ባንድ ፡ ላይ ፡ ተቃጥረው ፤
ያጫውታሉ ፡ የሞቱት ፡
—ቊመው ፡ ለሚሄዱት ።

ሠ ፡ ለሚሄዱት ፡ ለሚያልፉት ፡ ሁሉ ፡ ቆመው ፡ ያወራሉ ፤ ያጫውታሉ ።

ወ ፡ ከሞቱት ፡ እንስሶች ፡ የተገኙት ፡ (ቈዳ ፡ ጭራ ፡ ኾማት ፡ በገና ፡ ማሲንቆና ፡ ክራር) ፡ ነገ ፡ ለሚሞቱት ፡ ለሕያዋኑ ፡ ያጫውታሉ ።

203 ከዚያ ፡ ላይ ፡ ሆነህ ፡ ከተራራ ፡
—ሰው ፡ ከንቱ ፡ ብለህ ፡ ጥራ ።

ሠ ፡ «ሰው ፡ ከንቱ» ፡ የሚባለውን ፡ አሽከር ፡ ጥራ ፤ አስመጣው ፤ አቅርበው ።

ወ ፡ የሰውን ፡ ከንቱነት ፡ ተናገር ፤ ግብዝነቱንም ፡ አውራበት ።

204 ከዚያ ፡ ታች ፡ ያለችን ፡ ድውይ ፡
ከቶ ፡ ምን ፡ ቀመሽ ፡ አልሻት ፡ ወይ ፤
ኋላ ፡ ጸጸቱ ፡ ባንች ፡ ይሆናል ፤
—ተይ ፡ ሥጋ ፡ ብላሽ ፡ ይሆናል ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ለምናሽ ፡ ይሆናል ፤ እስቲ ፡ አስታውሺ ፤ ልብ ፡ አድርጊ ፡ አስላስሊ ።

ወ ፡ በውበትሽ ፡ አትኵሪ ፤ ሥጋሽ ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

205 ከዚያ ፡ ታች ፡ ያለችን ፡ ጠፍ ፡ መንደር ፡
ለምኖ ፡ ነበር ፡ ወታደር ፤
በከንቱ ፡ እንጂ ፡ ነው ፡ የተታለለ ፡
—አለማለሁ ፡ እያለ ።

ሠ ፡ አርሳለሁ ፡ አቀናለሁ ፡ አለማለሁ ፡ የሚለው ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

ወ ፡ ይህ ፡ ኀላፊ ፡ ጠፊ ፡ ዓለም ፡ አለሁ ፡ አለሁ ፡ እያለ ፡ የነፍስን ፡ ነገር ፡ ያስረሳል ፤ ሰውን ፡ ዓለማዊ ፡ ያደርገዋል ።

206 ከጎረ ፡ ቤቴ ፡ ብጣላ ፡
ሰው ፡ ሁሉ ፡ ለሱ ፡ አደላ ፤

ያለፈጣሪ ፡ ማን ፡ አለኝ ።
—ከሁሉም ፡ ባዳነኝ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ዘመድ ፡ የለኝም ፤ ባዕድ ፡ ነኝ ፤ ውልድና ፡ የለኝም ።

ወ ፡ ከመከራ ፡ ሁሉ ፡ በሰወረኝ ፤ ከጭንቀቱ ፡ ሁሉ ፡ ባተረፈኝ ፡ ከሥቃይ ፡ ባወጣኝ ።

207 ከጐዣምና ፡ ከዳሞት ፡
የቱ ፡ ይበልጣል ፡ በስፋት ፤

እኔስ ፡ በግምት ፡ ባየው ፡
—ትልቁ ፡ ዳሞት ፡ ነው ።

ሠ ፡ በጐዣም ፡ የሚገኘው ፡ «ዳሞት» ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ሰፊ ፡ ነው ።

ወ ፡ ሞት ፡ ከሁሉም ፡ የበለጠ ፡ ትልቅ ፡ ዕዳ ፡ ነው ፤ ከሱ ፡ የላቀ ፡ አስጨናቂ ፡ ነገር ፡ አይገኝም ።

208 ካንድ ፡ ቤት ፡ አድረን ፡ ሁላችን ፡
ገንዘብ ፡ ጠፍቶብን ፡ ተጨንቀን ፡

አንተ ፡ ወሰድከው ፡ ብለው ፡ አሉ ፤
—ምነዋ ፡ እኔ ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ።

ሠ ፡ በኔ ፡ ብቻ ፡ ምን ፡ አይተውብኛል ፤ እንዴት ፡ ጠረጠሩኝ ፤ ምን ፡ መስዬ ፡ ታየኋቸው ።

ወ ፡ ምነዋ ፡ እኔ ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ብተወውስ ፡ ምን ፡ ዕዳ ፡ አለብኝ ፤ ምን ፡ ያለፋኛል ፤ ለምን ፡ እታከታለሁ ፤ እወጣለሁ ፡ እወርዳለሁ ፤ መንኜ ፡ ብሄድስ ።

209 ከፉ ፡ ቢናገር ፡ ተቈጥቶ ፡
ጠላትህ ፡ ደሙ ፡ ፈልቶ ፡

እሱም ፡ እንዳንተ ፡ ሰው ፡ ነው ፤
—እረ ፡ ተው ፡ ሰብቀህ ፡ አትውጋው ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ነቅንቀህ ፡ ጦርህን ፡ ሰብቀህ ፡ አትውጋው ፤ አትግደለው ።

ወ ፡ አሳብቀህ ፡ ነገር ፡ ሠርተህ ፡ ባልንጀራህን ፡ አትጒዳ ፤ ከመከራ ፡ አትጣለው ።

210 ወልደ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አግኝቼው ፡
ርጥብ ፡ ሥጋውን ፡ በልቼው ፡

ደሙን ፡ ጠጥቼ ፡ ሥጋውን ፡
—ምነዋ ፡ እሞት ፡ ቢሆን ።

ሠ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አግኝቼው ፡ ደሙን ፡ ጠጥቼው ፡ አንዠቴን ፡ አር ሼው ፡ የምሞት ፡ ብሆን ፡ እንዴት ፡ በወደድሁ ።

ወ ፡ የጌታን ፡ ሥጋውንና ፡ ደሙን ፡ ተቀብዬ ፡ ለንስሐ ፡ ሞት ፡ በቅቼ ፡ መልካም ፡ ሞት ፡ ባደለኝ ።

211 ወልደ ፡ አምላክ ፡ እንኳ ፡ መሞቱ ፡
ለኛ ፡ ብሎ ፡ ነው ፡ ለፍጥረቱ ፡

በመለኮቱ ፡ ይነሣል ፤
—አብነቱን ፡ ያውቃል ።

ሠ ፡ ወልድ ፡ በወንጌል ፡ እኔ ፡ አብን ፡ ዐውቀዋለሁ ፡ እንዳለው ፡ አብና ፡ ወልድ ፡ እኩል ፡ ናቸው ።

ወ ፡ አብነቱን ፡ ያውቃል ፤ መድኀኒቱን ፡ አግኝቶታል ፤ ብልኀቱን ፡ ተረ ድቶታል ።

212 ወልጄ ፡ ነበር ፡ ብዙ ፡ ልጅ ፤
—አረም ፡ በዛብኝ ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ብዙ ፡ ልጆች ፡ ቢኖሩኝ ፡ ሥራው ፡ አልተካኺያደም ፤ ሰብ ሉን ፡ አረም ፡ ወረሰው ፤ አራሙቻ ፡ በላብኝ ፤ ተባይ ፡ አስቀረብኝ ።

ወ ፡ ሞት ፡ አጠቃኝ ፤ የወለድሁት ፡ አልባረክ ፡ አለኝ ፡ ወልጄ ፡ ላፈር ፡ መገበር ፡ ሆነ ።

213 ወንድሜ ፡ ጠፍቶኝ ፡ ስሄድ ፡
ነብር ፡ አግኝቶኝ ፡ ከመንገድ ፡

አልተመለስኩም ፡ ወዲያው ፡ ሄድኩ ፡
—እኔን ፡ ይብላኝ ፡ እያልኩ ።

ሠ ፡ ነብሩ ፡ ቢበላኝም ፡ ይብላኝ ፡ ብዬ ፡ ተጓዝሁ ፤ ፈርቼ ፡ አልተመለስ ኩም ፤ ወደዚያው ፡ ሄድኩ ፤ መንገዴን ፡ ቀጠልኩ ።

ወ ፡ ዋ ፡ ወንድሜ ፡ ሆይ ፡ እኔን ፡ ይብላኝ ፤ ዐፈር ፡ ልሁንልህ ፤ እኔ ፡ ስላ ንተ ፡ ልሙትልህ ።

214 ወደ ፡ ቦረና ፡ ሲሄዱ ፡
እጅግ ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ መንገዱ ፤

ብቅ ፡ ብለን ፡ ብናየው ፡
—አፋፉ ፡ ክፉ ፡ ነው ።

ሠ ፡ የትልቅ ፡ ገደል ፡ መዳረሻው ፡ መጥፎ ፡ ነው ፤ አፋፉ ፡ ያስፈራል ፤ ያሠጋል ።

ወ ፡ ነገረ ፡ ሠሪ ፡ አያድርስባችሁ ፤ አፈኛ ፡ ሰው ፡ መጥፎ ፡ ነው ።

215 ወደ ፡ አደባባይ ፡ ወጥተህ ፡
ከባለጋራህ ፡ ተሟግተህ ፡

ክርክር ፡ ገጥመህ ፡ ወደ ፡ ማታ ፡
—አለማፈር ፡ ነው ፡ ስትረታ ።

ሥ ፡ ተሟግተህ ፡ ስትረታ ፡ አትፈር ፤ ሲፈረድብህ ፡ አትዘን ።

ወ ፡ ቀን ፡ ሲጥል ፡ ጊዜ ፡ ሲያዋርድ ፡ አዱኛ ፡ ብላሽ ፡ ነው ፤ በሞት ፡ ጊዜ ፡
ንብረት ፡ ሀብት ፡ ወይም ፡ ማዕርግ ፡ አይከተልም ። (ዓለም) ፡ ሰው ፡
ሁሉ ፡ በመቃብር ፡ ፈርሶ ፡ በስብሶ ፡ ዐፈር ፡ ይሆናል ።

216 ወደ ፡ ዳንግላ ፡ ሲሄዱ ፡
ሩቅ ፡ ነው ፡ አሉ ፡ መንገዱ ፤

ደምበጫ ፡ ስደርስ ፡ የመሸብኝ ፡
—ገና ፡ ዳሞት ፡ አለብኝ ።

ሥ ፡ የዳሞት ፡ መንገድ ፡ ቀርቶኛል ፤ ገና ፡ እሱን ፡ መጓዝ ፡ አለብኝ ።

ወ ፡ ፍጡር ፡ ነኝ ፤ ገና ፡ መሞት ፡ አለብኝ ፤ የሞት ፡ ጽዋን ፡ እቀበላለሁ ፤
«ወትገብእ ፡ ውስተ ፡ መሬት» ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ ይፈጸምብኛል ።

217 ወዳጄ ፡ ነበር ፡ አካሌ ፡
ያኖረኝ ፡ ነበር ፡ እንዳመሌ ፤

አገሬን ፡ ብሎ ፡ ቢሞት ፡
—ዋኔ ፡ ተረዳሁት ።

ሥ ፡ ዋ ፡ መሞቱን ፡ ተረዳሁት ፤ ማረፉን ፡ ሰማሁ ።

ወ ፡ ሳላግዘው ፡ የቀረሁት ፡ ባለመቻሌ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የምረዳው ፡ ብሆን ፡
ኖሮ ፡ ባልተከየሁም ፡ ነበር ።

218 ወድቃ ፡ ተሰብራ ፡ ያለውሉ ፡
—ጊሩት ፡ ደቃለች ፡ አሉ ።

ሥ ፡ ወድቃ ፡ ደቃለች ፡ ተሰባብራለች ፡ አሉ ።

ወ ፡ ጊሩት ፡ «ደቅ» ፡ ከሚባል ፡ ስፍራ ፡ አለች ፤ ከዚያ ፡ ትኖራለች ።

219 ወገኑን ፡ በጣም ፡ ያኰራል ፡
በሰውነቱ ፡ ዐማኑኤል ፤

የጌታ ፡ ልጅ ፡ ነው ፡ ባባቱ ፡
—ለማኝ ፡ ናት ፡ እንጂ ፡ እናቱ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሥ ፡ ባባቱ ፡ ጌታ ፡ ነው ፤ እናቱ ፡ ግን ፡ ድኻ ፡ ነች ፤ ለማኝ ፡ ነች ።

ወ ፡ ያማኑኤል ፡ እናት ፡ ማርያም ፡ አዛኝ ፡ ርኅርኅት ፡ ተለማኝ ፡ ናት ፤
ታማልዳለች ።

220 ውዳሴ ፡ ማርያም ፡ ሲታደል ፡
—ብርሃንን ፡ ለኔ ፡ በል ።

ሠ ፡ ውዳሴ ፡ ማርያም ፡ ሲታደል ፡ «ብርሃን» ፡ የሚባለውን ፡ ክፍል ፡ ለኔ ፡ ስጠኝ ፤ እሱ ፡ እንዲደርሰኝ ፡ አድርግ ።

ወ ፡ ዐይኔን ፡ አብራልኝ ፤ ብርሃንን ፡ ስጠኝ ።

221 **ውሃ ፡ ሲሞላ ፡ አረምሞ ፡**
**መጠበቅ ፡ ያሻል ፡ ከዳር ፡ ቆሞ ፤**

**የሚያውቀው ፡ የለም ፡ ምን ፡ ቢሆን ፡**
**—የሚጠራበትን ፡ ቀን ።**

ሠ ፡ ንጹሕ ፡ የሚሆንበትን ፡ ሰዓት ፤ የማይፈርስበትን ፡ ጊዜ ፡ የሚያውቅ ፡ ሰው ፡ የለም ።

ወ ፡ ጊዜ ፡ ሞትን ፡ ማወቅ ፡ አይቻልም ፤ የሚመጣው ፡ ሳይታሰብ ፡ ድንገት ፡ ነው ።

222 **ውዳሴ ፡ ማርያም ፡ ስንማር ፡**
**አግኝተን ፡ ነበር ፡ ደግ ፡ ምስጢር ፤**

**ተገደፈ ፡ አሉኝ ፡ ተሳሳተ ፡**
**—አ ፡ አዳም ፡ መሬት ፡ አንተ ።**

ሠ ፡ ከውዳሴ ፡ ማርያም ፡ «አ ፡ አዳም ፡ መሬት ፡ አንተ» ፡ የሚለው ፡ ቃል ፡ ተረሳ ፤ ተዘነጋ ፤ እሱ ፡ ብቻ ፡ ተገደፈ ።

ወ ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ዐፈር ፡ መሬት ፡ መሆኑን ፡ ዘነጋው ፤ ሰው ፡ መሆኑን ፡ ረሳው ።

223 **ውዳሴ ፡ ማርያም ፡ ቃል ፡ ትምርት ፡**
**እንዳልጠቀመኝ ፡ አየሁት ፤**

**የጋላ ፡ ጸሎት ፡ ይገ፟ለሁ ፡**
**—በወዳጄ ፡ አዝናለሁ ።**

ሠ ፡ አምልኮ ፡ ባዕድ ፡ (ወዳጄ) ፡ በመደረጉ ፡ አዝናለሁ ።

ወ ፡ የምወደው ፡ ከድቶኝ ፡ አዝናለሁ ፤ ወዳጅ ፡ አልበረክትልህ ፡ ብሎኝ ፡ እተክዛለሁ ።

224 **ዋድላ ፡ ደላንታ ፡ በጌምድር ፡**
**ተርፏል ፡ አሉ ፡ ደጉ ፡ አገር ፤**

**ሸምቶ ፡ አይበላም ፡ ወይ ፡ ምነው ፡**
**—ሸዋ ፡ ተዘራ ፡ ሰው ።**

ሠ ፡ የሸዋ ፡ ገበሬ ፡ ከዘራው ፡ ካመረተው ፡ ሸምቶ ፡ አይበላም ፡ ወይ ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ወደ ፡ ሸዋ ፡ ተሰማራ ፤ ተሠራጨ ፤ ተበተነ ።

225 **ዐፄ ፡ ምኒልክ   መንፈሳይ ፡**
**እውነት ፡ መነኰሴ ፡ መሳይ ፡**

ይህችን ፡ ዋሾ ፡ ቃላባይ ፤
—አለምን ፡ ያዝካት ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ያለምንም ፡ ችግር ፡ ሳትለፋ ፡ ሳትደክም ፡ በቀላሉ ፡ በጅህ ፡ አደረግሃት ፡ ወይ ።

ወ ፡ መላ ፡ ኢትዮጵያን ፡ ገዛህ ፤ ዳር ፡ ድንበሩንም ፡ አቀናህ ፤ ተከፋፍሎ ፡ የነበረውንም ፡ አንድ ፡ አድርገህ ፡ ያዝከው ።

226 ዐፄ ፡ ምኒልክ ፡ ሲሞቱ ፡
ምነው ፡ አትሄዱ ፡ ከፍታቱ ፤

እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ክፋታችሁ ፡
—አለማስቀበራችሁ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ሞቶ ፡ ለምን ፡ ከልቅሶ ፡ አልደረሳችሁም ፡ እቀብር ፡ አልመጣችሁም ።

ወ ፡ ተድላና ፡ ደስታ ፡ ዓለም ፡ ማያ ፡ የነበሩ ፡ ዐፄ ፡ ምኒልክ ፡ ሞቱባችሁ ፤ ተቀበሩባችሁ ።

227 ዐፄ ፡ ምኒልክ ፡ ንጉሡ ፡
አባ ፡ ማቴዎስ ፡ ጳጳሱ ፡
ቃኘው ፡ መኰንን ፡ ራሱ ፡
ሂዱ ፡ ይላሉ ፡ ገሠገሡ ፤

እምብዛም ፡ አሽከር ፡ አልቀራቸው ፡
—ሁሉም ፡ ተከተሏቸው ።

ሠ ፡ አሽከሮቻቸው ፡ ዐጀቧቸው ፤ ተከተሏቸው ፤ ከበዋቸው ፡ አብረው ፡ ሄዱ ።

ወ ፡ ሁሉም ፡ ተከታትለው ፡ ሞቱ ፤ አልቈዩም ፤ ምንም ፡ ሰው ፡ አልቀራቸው ።

228 ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ ሞኙ ፡ ናቸው ፤
እኛም ፡ ሁላችን ፡ ናቅናቸው ።

ንጉሥ ፡ ቢሏቸው ፡ በማኸሉ ፡
—ወሰን ፡ ጠባቂ ፡ ልሁን ፡ አሉ ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ተራ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ዘበኛ ፡ ዳር ፡ ድንበሩን ፡ ልጠብቅ ፡ ወሰኑን ፡ ልቈጣጠር ፡ አሉ ።

ወ ፡ ያገራቸውን ፡ ወሰን ፡ ደማቸውን ፡ አፍሰው ፡ አስከበሩ ።

229 ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ ይዋሻሉ ፡
መጠጥ ፡ አልጠጣም ፡ እያሉ ፤

ሲጠጡ ፡ አይተናል ፡ በርግጥ ፡
—ራስ ፡ የሚያዞር ፡ መጠጥ ።

ሠ ፡ የሚያሰክር ፡ ራስ ፡ የሚያዞር ፡ ናላ ፡ የሚበጠብጥ ፡ መጠጥ ፡ ይጠጣሉ ።

ወ ፡ ተሰየፉ ፡ ተከለሉ ፤ አንገታቸው ፡ ተቈርጦ ፡ ራሳቸው ፡ እየዞረ ፡ እንዲታይ ፡ ሆነ ።

230 ዐይኔን ፡ ታውሬ ፡ ዘንድሮ ፡
የሚመራኝ ፡ ሰው ፡ ተቸግሮ ፡

አገሬ ፡ የገባሁ ፡ ሲመስለኝ ፡
—ወደ ፡ ዜት ፡ ወሰድከኝ ።

ሠ ፡ ወዳልፈለግሁበት ፡ ወዳላልሁበት ፡ ቦታ ፡ ወዴት ፡ መራኸኝ ፤ የት ፡ ወሰድከኝ ።

ወ ፡ የተመኘሁት ፡ ሳይሆንልኝ ፡ ቀርቶ ፡ «ዜት» ፡ የሚባለውን ፡ አገር ፡ ሾምከኝ ።

231 ዛሬማ ፡ ጠጅ ፡ ማን ፡ ጠጥቶ ፡
—ሁሉ ፡ ጠላ ፡ ቤት ፡ ገብቶ ።

ሠ ፡ ሁሉ ፡ ጠላ ፡ ጠጪ ፡ ሆነ ፤ ጠጅ ፡ የሚጠጣ ፡ ታጣ ፤ ጠላ ፡ ተወደደ ፤ መጠጡ ፡ እሱው ፡ ብቻ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ፍቅር ፡ ጠፋ ፤ ጠብ ፡ ብቻ ፡ ሆነ ፤ አምባጓሮ ፡ በዛ ፤ ሰላም ፡ ታጣ ።

232 ዛሬ ፡ የት ፡ ይገኛል ፡ መልካም ፡ ሽቶ ፡
—ደኅና ፡ ደኅናው ፡ ቀድሞ ፡ ጠፍቶ ።

ሠ ፡ መልካም ፡ ሽቱ ፡ ታጣ ፤ ደኅና ፡ ደኅናው ፡ አልተገኘም ።

ወ ፡ ጨዋ ፡ ሰው ፡ ጠፋ ፤ ደጋጎቹ ፡ ቀድሞ ፡ ቀሩ ፤ ዛሬ ፡ ደኅና ፡ ሰው ፡ የለም ፤ ቅን ፡ አይገኝም ።

233 የሀገራችን ፡ መንገድ ፡
ሌት ፡ ያለብርሃን ፡ አያስኬድ ፤

እስቲ ፡ ተቀመጥ ፡ ይንጋልህ ፤
—ቈይ ፡ ቀን ፡ ይውጣልህ ።

ሠ ፡ ይንጋልህ ፤ ፀሐይ ፡ ይውጣልህ ፤ ሌሊቱ ፡ ይለፍ ፤ ነገ ፡ በብርሃን ፡ ተጓዝ ፤ አድረህ ፡ ሂድ ።

ወ ፡ ታገሥ ፤ መልካም ፡ ዘመን ፡ ይምጣልህ ፤ ደኅና ፡ ቀን ፡ ይውጣልህ ፤ ይህ ፡ ጊዜ ፡ ይለፍልህ ፤ ሰዓትህን ፡ ጠብቅ ።

234 የልጃገረድ ፡ አውታታ ፡
አውራ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ተኝታ ፡

ተነሽ ፡ በሏት ፡ ምነው ፡
—ይህ ፡ ሁሉ ፡ አለማፈር ፡ ነው ።
ሠ ፡ ኀፍረት ፡ ማጣት ፤ ደፋር ፡ ዐይናውጣ ፡ ክቾ ፡ ደረቅ ፡ መሆን ፡ ነው ።
ወ ፡ ዓለም ፡ ኀላፊ ፡ ጠፊ ፡ መልክም ፡ ረጋፊ ፡ ነው ።

235 የኀመር ፡ ጌታ ፡ የዱሪ ፡
ኰሩ ፡ ነው ፡ አሉ ፡ ተዶራሪ ፤
እኛስ ፡ ሲገድል ፡ ያየነው ፡
—የሠራን ፡ ጌታ ፡ ነው ።
ሠ ፡ ሲገድል ፡ ያየነው ፡ የሠራን ፡ ጌታ ፡ ነው ። ( የሠራን ፡ ጌታ ፤ የፈረስ ፡ ስም) ።
ወ ፡ የሚገድለንም ፡ የሚያድነንም ፡ የፈጠረን ፡ ጌታ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

236 የሚሻለን ፡ ነው ፡ ብለው ፡
በየማኅበሩ ፡ ለፍተው ፡
—ደግ ፡ ሰው ፡ ቀረ ፡ ሳይበሉት ፤
—ለፍጻሜው ፡ ሲያስቡት ። (1) (በ. ማ.)
ሠ ፡ የተደገሰውን ፡ መሰናዶ ፡ ሳይበሉት ፡ ቀረ ፤ እንደታሰበው ፡ ሳይሆን ፡ ቀረ ፡ ተበላሸ ።
ወ ፡ ያ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ ከሞት ፡ ተረፈ ። ደጉ ፡ ከታሰበበት ፡ አደጋ ፡ አመለጠ ፤ ዳነ ።

237 የማርያም ፡ ልጅ ፡ ነኝ ፡ ብለህ ፡
—ወልድ ፡ በራስህ ፡ ተኵራህ ፡
አብ ፡ አይበልጥም ፡ ወይ ፡ አባትህ ፡
—ተለማኝ ፡ እናትህ ።
ሠ ፡ ወልድ ፡ በሥልጣንህ ፡ ኵራህ ፤ በራስህ ፡ ተማመንክ ።
ወ ፡ ራስህን ፡ በዘንግ ፡ ደበደቡህ ፤ ኵርዐተ ፡ ርእስ ፡ አክሊለ ፡ ሦክ ፡ አደረጉብህ ።
ሠ ፡ ከድኻ ፡ ከለማኝ ፡ እናትህ ፡ ከችግረኛዋ ፡ ወላጅህ ፡ አባትህ ፡ አይበልጥም ፡ወይ
ወ ፡ ማርያም ፡ ተለማኝ ፡ ነች ፡ ታማልዳለች ።

238 የማናውቀውን ፡ ሌብነት ፡
ልንሰርቅ ፡ ገብተን ፡ ከሰው ፡ ቤት ፡
ይቅርብን ፡ ጓዴ ፡ እንውጣ ፤
—የሚጠብቀን ፡ መጣ ።
ሠ ፡ ጠባቂው ፡ ዘበኛ ፡ መጣብን ፤ እንውጣ ፡ እንሽሽ ፤ እናምልጥ ።
ወ ፡ የጨነቀ ፡ የጠበበ ፡ የመከራ ፡ ቀን ፡ መጣ ፤ የሥቃይ ፡ ዘመን ፡ ደረሰ ።

(1) እነቢትወደድ ፡ ነጋሽ ፡ በዛብህ ፡ በ1943 ፡ ዓ. ም. ሹማምንቱን ፡ ሁሉ ፡ ገድለው ፡ አስወግደው ፡ ሥልጣን ፡ ለመያዝ ፡ የሴራ ፡ ማኅበር ፡ አዘጋጅተው ፡ ስለነበረ ፡ በጊዜው ፡ ተመልካች ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥቱን ፡ እግዚአብሔር ፡ እንደጠበቃቸው ፡ ሐሳቡን የገለጠበት ።

239 የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ ፈጣሪ ፡
ሰውን ፡ ሁሉ ፡ አናጋሪ ፤

የምሰድብህ ፡ በጭካኔ ፡
—ምናምን ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ እኔ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እኔ ፡ አንተን ፡ ከምናምን ፡ አልቈጥርህም ፤ ከሰው ፡ ቍጥር ፡ አላገባ ህም ፡ ከግምቴ ፡ በታች ፡ ነህ ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ ካንተ ፡ ሌላ ፡ ከቶ ፡ በማን ፡ ላምን ፡ በማንስ ፡ ላመ. ልክ ፡ እችላለሁ ፤ እደፍራለሁ ።

240 የሥነ ፡ ፍጥረት ፡ ነገር ፡
ዘሩ ፡ እንዳባቱ ፡ ነበር ፤

ቀኑ ፡ እያለቀ ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡
—ጐሹ ፡ አንበሳን ፡ ወለደ ።

ሠ ፡ ከጐሽ ፡ አንበሳ ፡ ተወለደ ፤ የሥነ ፡ ፍጥረት ፡ ሕግ ፡ ተፋለሰ ።
ወ ፡ ደጃች ፡ ጐሹ ፡ ጐበዝ ፡ ጀግና ፡ የሆነ ፡ ልጅ ፡ ወለደ ።

241 የሥጋ ፡ ሥሥት ፡ ምንድነው ፡
—መቍረጥ ፡ እንደ ፡ ጐቤ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ መቍረጥ ፡ ብርንዶ ፡ መብላት ፡ እንደ ፡ ጐበና ፡ ነው ፤ አበላል ፡ ማሳመር ፡ እንደ ፡ ርሱ ፡ ነው ።

ወ ፡ ተዋጊነት ፡ ቈራጥነት ፡ ደፋርነትና ፡ ጀግንነት ፡ ይኋችኋል ፡ እንደ ፡ ራስ ፡ ጐበና ፡ ነው ።

242 የየሩሳሌም ፡ ነጋዴ ፡
ጣለበት ፡ አሉ ፡ ወንበዴ ፤

ለገንዘቡማ ፡ ማን ፡ አዘነ ፡
—ወየው ፡ ነፍሱን ፡ ያዳነ ።

ሠ ፡ ሽቀጡ ፡ ገንዘቡ ፡ ቀርቶ ፡ ራሱን ፡ ነፍሱን ፡ ከሞት ፡ ያዳነ ፡ ከወንበዴ ፡ ያመለጠ ፡ ብርቱ ፡ ነው ።

ወ ፡ ሰጥቶ ፡ መጽውቶ ፡ በበጎ ፡ ሥራውና ፡ በሃይማኖቱ ፡ ነፍሱን ፡ ከዙ ነኔና ፡ ከገሃነመ ፡ እሳት ፡ የሚያድን ፡ ሰው ፡ ምስጉን ፡ ነው ።

243 የራስ ፡ መኰንን ፡ አታክልት ፡
አለማለሙን ፡ እስቲ ፡ እዩት ፤

ከመልካም ፡ ቦታ ፡ ቢተክለው ፡
—ለሁሉ ፡ እራት ፡ ሆነው ።

ሠ ፡ ሁሉ ፡ ተመገበው ፤ እራት ፡ አደረገው ፤ ኀላፊ ፡ አግዳሚው ፡ በላው ።

ወ ፡ የመኰንን ፡ ልጅ ፡ ለሁሉ ፡ ሀብት ፡ ንብረት ፡ ትዳር ፡ ሆነው ፤ ትንሽ ፡ ትልቁን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገው ፤ አከበረው ፤ አነሣው ፤ ቀን ፡ አወጣለት ።

244 የራስ ፡ ዐሊ ፡ ወጥ ፡ ቤት ፡
ቀንን ፡ ሠራችው ፡ ሌሊት ፤

ተፈተፈተ ፡ ተጠለቀ ፤
—ያ ፡ ሁሉ ፡ ጨው ፡ አለቀ ።

ሠ ፡ ማጣፈጫው ፡ አልተገኘም ፤ ጨዉ ፡ አለቀ ፤ መበያ ፡ ታጣ ።
ወ ፡ ሽማግሌው ፡ ሁሉ ፡ አለቀ ፤ ጨዋ ፡ የሆነው ፡ ሁሉ ፡ በሞት ፡ ተለየ ።

245 የሰው ፡ አገር ፡ ሰው ፡ በሽተኛ ፡
ተዉ ፡ አትነካኩት ፡ ዐርፎ ፡ ይኛ ፤

አትገላልጡት ፡ አልቦታል ፤
—አገርሽቶት ፡ ይሞታል ።

ሠ ፡ በገመምተኛነት ፡ በግርሻ ፡ ታሞ ፡ ይሞታል ።
ወ ፡ አገር ፡ ለመግዛትና ፡ ለመክበር ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ምኞት ፡ ያለውን ፡ እንዲ
ሁም ፡ ወደ ፡ ተወለደበት ፡ አገር ፡ ለመግባት ፡ የሚጓጓውን ፡ ሁሉ ፡
አታስታውሱት ፤ አታስቈጩት ፤ ተሳቆ ፡ ይሞታል ።

246 የሰው ፡ እንግዳ ፡ ሲመጣ ፡
ግባ ፡ ይሉታል ፡ ብላ ፡ ጠጣ ፤

ያንት ፡ መላክተኛ ፡ የመጣለት ፡
—ይዋል ፡ ይደር ፡ የለበት ።

ሠ ፡ ፈጣኑን ፡ መልክተኛ ፡ ዋል ፡ እደር ፡ ማለት ፡ አይቻልም ።
ወ ፡ ሞት ፡ ከመጣ ፡ መዋል ፡ ማደር ፡ አይቻልም ፤ ቅሌን ፡ ጨርቄን ፡ ማ
ለት ፡ የለም ።

247 የሰው ፡ ዕድሜ ፡ ለነገሩ ፡
በሰማንያ ፡ መቀጠሩ ፡

ይህነን ፡ ነገር ፡ ብናይ ፡
—እንደ ፡ ጥላ ፡ አይደለም ፡ ወይ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ይህ ፡ ሲመረመር ፡ ጠብ ፡ ክርክርን ፡ የሚፈጥር ፡ ነው ፤ ጥላቻንም ፡
የሚያስከትል ፡ ይሆናል ።
ወ ፡ የሰው ፡ ዕድሜ ፡ ምንም ፡ በሰማንያ ፡ ቢወሰን ፡ እንደ ፡ ጥላ ፡ ኀላፊ ፡
ጠፊ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ አበባ ፡ ረጋፊ ፡ ነው ።

248 የሴትን ፡ ነገር ፡ አምነህ ፡
መሄድህ ፡ ነው ፡ ወይ ፡ አብረህ ፤

እንዲህም ፡ አይደል ፡ መንገድ ፤
—እረ ፡ ተው ፡ አትሂድ ።

1 ሠ ፡ ተው ፡ አትሂድ ፡ ብሎ ፡ መጋበዝ ።
ወ ፡ ትሂድ ፡ ተዋት ፤ አትገላግሏት ፤ አታባብሏት ፡ አታንቈሻብሏት ።
2 ወ ፡ ጥቂት ፡ ሰንብት ፡ በሞት ፡ አትለየን ።

249 የቀለምን ፡ ዘር ፡ ታውቃለህ ፡
—ምነው ፡ «ና» ፡ የጠፋህ ።　　(ክ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ና ፡ የሚለው ፡ ፊደል ፡ እንዴት ፡ ጠፋህ ፤ በምን ፡ እሱ ፡ ተገደፈህ ፤ ተረሳህ ፤ ተዘነጋህ ።
ወ ፡ ምነው ፡ ጠፋህ ፡ መጥተህ ፡ አላየኸኝም ፤ ሳትጠይቀኝ ፡ ሰነበትህ ፤ ሳንገናኝ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ሆነ ።

250 የቀድሞ ፡ ዘመን ፡ ስሕተት ፡
በጾም ፡ ቀን ፡ ዓሣ ፡ መብላት ፤

ያሁን ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ አያውቅ ፡ መላ ፡
—በጣም ፡ ሽሮ ፡ ነው ፡ የሚበላ ።　　(ተ ፡ ተ) ፡

ሠ ፡ በጾም ፡ ቀን ፡ ዓሣ ፡ እንኳ ፡ አይቀምስም ፤ የሚመገበው ፡ በሽሮ ፡ ወጥ ፡ ብቻ ፡ ነው ።
ወ ፡ የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ ጾም ፡ መሻርና ፡ መግደፍ ፡ ያዘወትራል ፤ የጾም ፡ ነገር ፡ አይሆንለትም ።

251 የበደለኝን ፡ ኀረ ፡ ቤቴ ፡
አንቺ ፡ ታውቂዋለሽ ፡ እመቤቴ ፤

እንድትነግሪልኝ ፡ ይሁን ፡
—ስሞታ ፡ አደራሽን ።

ሠ ፡ ወቀሣውን ፡ እንዳትረሺ ፤ ስሞታውን ፡ አቅርቢልኝ ።
ወ ፡ እመቤቴ ፡ ማርያም ፡ ሆይ ፡ በሞትኩ ፡ ጊዜ ፡ ከመከራ ፡ ነፍስ ፡ አድኚኝ ።

252 የበጌምድር ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ ላስታ ፡
ይመላለሳል ፡ ጧት ፡ ማታ ፤

ተከዜን ፡ መቼ ፡ ይሻገራል ፤
—ገና ፡ መቄት ፡ ይቀራል ።

ሠ ፡ ከተከዜ ፡ ሲደርስ ፡ ገና ፡ መቄት ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ይቀረዋል ።
ወ ፡ መቅ ፡ መውረድ ፡ ዐዘቅት ፡ መውደቅ ፡ እመቃብር ፡ መግባት ፡ የት ፡ ይቀራል ፤ ግብአተ ፡ መሬት ፡ ለማን ፡ ይሻራል ፤ ከርደተ ፡ መቃብር ፡ ማን ፡ ያመልጣል ።

253 የተመተረውን ፡ ለዝግን ፡
ማን ፡ አፈሰሰው ፡ ይሆን ፤

አፍሢን ፡ በሰፌድ ፡ እፍ ፡ አንልም ፤
—ሥጋና ፡ ነፍስ ፡ አይሆንም ።

ሠ ፡ ሥጋን ፡ ማንፈስ ፡ ማበጠር ፡ ካፊር ፡ መለየት ፡ አይቻልም ፤ ችግር ፡ ነው ።

ወ ፡ የሥጋና ፡ የነፍስ ፡ ሥራ ፡ ለየብቻው ፡ ነው ፤ ሁሉንም ፡ በየመልኩ ፡ መያዝ ፡ ያስፈልጋል ።

254 የተራራው ፡ ገመገም ፡
ያስፈራ ፡ ነበር ፡ በጣም ፤

ዛሬስ ፡ መንገድ ፡ ሆኗል ፤
—ሰውም ፡ ያልፍበታል ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የእግር ፡ መንገድ ፡ አለው ፤ ሰው ፡ ይሄድበታል ፤ ወጪ ፡ ወራጁ ፡ ሕዝብ ፡ ያልፍበታል ።

ወ ፡ ተድላ ፡ ደስታው ፡ ሣቅ ፡ ጨዋታው ፡ በሁሉም ፡ ሰው ፡ ያልፋል ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ የተደሰተ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ማዘኑ ፡ አይቀርም ።

255 የተቈጠረው ፡ ምስክር ፡
ይንገር ፡ ካላችሁ ፡ ይንገር ፤

እኔ ፡ የማምናቸው ፡ ሁለቱን ፡
—እናትና ፡ ልጇን ።

ሠ ፡ እናትና ፡ ልጇን ፡ አምናቸዋለሁ ፤ ምስክርነታቸውንም ፡ እቀበላለሁ ።

ወ ፡ ማርያምንና ፡ ጌታን ፡ አምናለሁ ፤ በሁለቱ ፡ ላይ ፡ ተስፋ ፡ አለኝ ፤ እነሱን ፡ ተማጥኛለሁ ።

256 የተበደለ ፡ ባላገር ፡
ቀን ፡ እየገባ ፡ ይናገር ፤

እንዳትጫወት ፡ ከሎሌህ ፡
—ማታ ፡ አይድረስብህ ።

ሠ ፡ ሲመሽ ፡ አይድረስብህ ፤ ሲጨልም ፡ አይምጣብህ ።

ወ ፡ መከራ ፡ መዓት ፡ አያግኝህ ፤ ችግር ፡ አያጋጥምህ ፤ ሥቃይ ፡ አይጣልብህ ።

257 የተወለደ ፡ ከአዳም ፡
መሬት ፡ ያልገዛ ፡ የለም ፤

ግብሩን ፡ መገበር ፡ አቅቷቸው ፡
—ገና ፡ ብዙ ፡ ዕዳ ፡ አለባቸው ።

ሠ ፡ የመሬት ፡ ግብር ፡ ዕዳ ፡ አለባቸው ፤ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አልከፈሉም ።

ወ ፡ በምድር ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ የማይሠሩ ፡ ሁሉ ፡ በሰማይ ፡ መኰነን ፡ ደይን ፡
መግባት ፡ ይኖርባቸዋል ።

258 የትላንትናው ፡ ጦርነት ፡
ያ ፡ መልካም ፡ ጐበዝ ፡ ያለበት ፡

ተማረከ ፡ አሉኝ ፡ እሱም ፡ አብሮ ፡
—ምነው ፡ ባልተያዘ ፡ ኑሮ ።

ሠ ፡ ሰውዬው ፡ እጁን ፡ ሳይሰጥ ፡ ባይያዝ ፡ ቢያመልጥ ፡ ደግ ፡ ነበር ።
ወ ፡ ያልተሟላና ፡ ያልተሳካ ፡ ትዳር ፡ ሰውን ፡ ያስቸግራል ።

259 የኔ ፡ ቤት ፡ እዚህ ፡ ሳለልሽ ፡
ለምን ፡ ምድረ ፡ ግብጽ ፡ ወረድሽ ፤

ማልደሽ ፡ ይዘሽ ፡ ነይ ፡ ልጅሽን ፡
—ስሞት ፡ አደራሽን ።

ሠ ፡ በኔ ፡ ሞት ፡ እንዳትቀሪብኝ ፡ ልጅሽን ፡ ይዘሽ ፡ እንድትመጪ ።
ወ ፡ በጊዜ ፡ ሞቴ ፡ እንዳትረሽኝ ፤ አደራሽን ፡ እንድታማልጂኝ ።

260 የኔንም ፡ ጐጆ ፡ ቈጠሩሽ ፡
—እንደ ፡ ሰው ፡ አዳራሽ ።

ሠ ፡ ትንሿን ፡ ጐጆዬን ፡ እንደ ፡ ሰፊ ፡ እንደ ፡ ትልቅ ፡ ቤት ፡ ቈጠሩሽ ፤
ከፍ ፡ አድርገው ፡ ገመቱሽ ።
ወ ፡ አንዳንድ ፡ ሰው ፡ ተንኰለኛ ፡ ነገረ ፡ ሠሪ ፡ አላኳሽ ፡ አነካኪ ፡ ነው ።

261 የኛ ፡ መድኀኒት ፡ ዐይነቶች ፡
በብዙ ፡ አሉን ፡ ቅመሞች ፤

ነገር ፡ ግን ፡ እኔ ፡ ሳስበው ፡
—ሥራሥሩ ፡ መልካም ፡ ነው ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ ከዕፀዋት ፡ ሥር ፡ የተገኘ ፡ መድኀኒት ፡ ይፈውሳል ፤ ያድናል ።
ወ ፡ ሥራን ፡ ከመሥራትና ፡ ከማሠራት ፡ አለመቦዘን ፡ መትጋት ፡ ታታሪ ፡
መሆን ፡ መልካም ፡ ነው ።

262 የዓለም ፡ መልክ ፡ ዝንጕርጕር ፡
ነጭና ፡ ጥቊር ፡ እንደ ፡ ነብር ፤

አይቻታለሁ ፡ በሰልፍ ፡
—በምኒልክም ፡ ጊዜ ፡ ስታልፍ ።

ሠ ፡ በምኒልክም ፡ ዘመን ፡ ስትወጣ ፡ ስትወርድ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ስትል ፡
ስታልፍ ፡ ስታገድም ፡ አይቻታለሁ ።

ወ ፡ የዐፄ ፡ ምኒልክ ፡ ተድላና ፡ ደስታ ፡ እንኳ ፡ አለፈ ፤ ነበር ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ።

263 የዘመዶቼን ፡ ማለቅ ፡
ምነው ፡ እስካሁን ፡ ሳላውቅ ፤

አሁን ፡ በቀደም ፡ ሰማሁኝ ፤
—ዘንድሮን ፡ ባወጣኝ ።

ሠ ፡ ዘንድሮ ፡ አዘንኩ ፤ አለቀስኩ ፤ እንባ ፡ ወጣኝ ፤ ሐዘን ፡ ጸናብኝ ።
ወ ፡ የዘንድሮን ፡ በዳንኩ ፤ ይህን ፡ ዓመት ፡ በደኅና ፡ ባለፍኩ ፤ በጤና ፡ በዘለቅሁ ።

264 የዘመዶቼን ፡ አገር ፡
ለምኜ ፡ ነበር ፡ በሹም ፡ ሸር ፡

ከፍለው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የሰጡኝ ፡
—ሁሉም ፡ አልሆነልኝ ።

ሠ ፡ ያሰብኩትን ፡ የተመኘሁትን ፡ በሙሉ ፡ አላገኘሁም ፤ አልተሳካልኝም ፤ ምኞቴ ፡ አልተፈጸመልኝም ።
ወ ፡ ረዳትም ፡ ወገንም ፡ አላገኘሁም ፤ ሁሉም ፡ ተዉኝ ፤ ችላ ፡ አሉኝ ፤ ገሸሽ ፡ አደረጉኝ ።

265 የዛሬ ፡ ሳምንት ፡ ዐርብ ፡ ቀን ፡
ትልቅ ፡ ነጭ ፡ በግ ፡ አርደን ፡

የታመሙ ፡ መላው ፡ ዳኑ ፡
—በሥጋና ፡ በደሙ ።

ሠ ፡ ሕመምተኞች ፡ ሁሉ ፡ በበግ ፡ ሥጋ ፡ አገገሙ ፤ ጤናቸውን ፡ አገኙ ።
ወ ፡ የጌታችንን ፡ ሥጋና ፡ ደም ፡ የተቀበሉ ፡ ሁሉ፡ ድኅነተ ፡ ነፍስ ፡ አላቸው ፡ (ምስጢረ ፡ ቍርባን) ።

266 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ልጆች ፡
ነገር ፡ እያሉ ፡ ላይ ፡ ታች ፡

እኖራለሁ ፡ ብል ፡ ባገሬ ፡
—ምነው ፡ አደነኝ ፡ ሰው ፡ እንዳውሬ ።

ሠ ፡ ሰዉ ፡ አውሬ ፡ መስዬው ፡ ሊገድለኝ ፡ ሲከተለኝ ፡ ሲያድነኝ ፡ ዋለ ።
ወ ፡ አውሬ ፡ ሆኖ ፡ ሰው ፡ ሊያጠፋኝ ፡ ያባርረኛል ፤ ያሳድደኛል ፤ ፍዳዬን ፡ ያሳየኛል ።

267 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ምላስ ፡
ተስማምቷል ፡ አሉ ፡ ከጥርስ ፤

እኔ ፡ ሳልሰማው ፡ ቢያኝከኝ ፡
—ምንኛ ፡ አደቀቀኝ ።

ሠ ፡ ክፉኛ ፡ አኘከኝ ፤ አደቀቀኝ ፤ ደቈሰኝ ።

ወ ፡ አማኝ ፤ ቦጨቀኝ ፤ ስሜን ፡ አጐደፈው ፤ በነገር ፡ ሲያነሣኝ ፡ ሲጥለኝ ፡ ዋለ ።

268 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ ሥራ ፡
ማሩም ፡ ቅጠሉም ፡ አያኰራ ፤

ዕውቀቱስ ፡ ያንተው ፡ መሰለኝ ፡
—ባብነትህ ፡ አድነኝ ።

ሠ ፡ በመድኀኒትህ ፡ አክመኝ ፤ በጥበብህ ፡ አድነኝ ፤ በችሎታህ ፡ ፈውሰኝ ።

ወ ፡ በእግዚአብሔር ፡ አብነትህ ፡ በመለኮትነትህ ፡ በከሃሊነትህ ፡ አድነኝ ፤ ተቤዠኝ ።

269 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ ትሑት ፡
ተዋራጅ ፡ ሆኗል ፡ ለፍጥረት ፤

ግን ፡ አይታጣም ፡ አንዳንድ ፡
—ኰራም ፡ እያለ ፡ የሚሄድ ።

ሠ ፡ የሚታበይ ፡ የሚኰራ ፡ ሞልቷል ፤ እየተዘባነነ ፡ እየተንበጣረረ ፡ የሚሄድ ፡ አይታጣም ።

ወ ፡ በምናኔ ፡ ሰዉ ፡ ወደ ፡ ኮራ ፡ ገዳም ፡ ይሄዳል ፤ ባሕታዊ ፡ ተርኛል ።

270 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ገረድ ፡ ሎሌ ፡
አይታዘዝም ፡ እንዳመሌ ፤

አንቺ ፡ ብትለው ፡ ይሄዳል ፤
አንተ ፡ ያልከውም ፡ ይኖራል ።

ሠ ፡ ያላከበሩት ፡ አንቺ ፡ ያላሉት ፡ አሽከር ፡ ይቀመጣል ፤ ታማኝ ፡ ነው ፡ ጠግቦ ፡ አይሄድም ።

ወ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ አንተ ፡ ያልከውና ፡ የፈቀድከው ፡ ሁሉ ፡ ይኖራል ።

271 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ገበሬ ፡
መሬት ፡ አያውቅም ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፤

ጭንጫ ፡ ነው ፡ ብለህ ፡ አትተወው ፤
—እረሰው ፡ ዐፈር ፡ ነው ።

ሠ ፡ ዐፈር ፡ የሞላበትን ፡ ለሙን ፡ መሬት ፡ መላልሰህ ፡ እረሰው ፤ አዳብረው ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ ሰው ፡ ትቢያ ፡ ነው ፤ ይፈርሳል ፤ ይበሰብሳል ፤ ወደ ፡ ዐፈርነት ፡ ይለወጣል ።

272 የየሩሳሌም ፡ መንገድ ፡
ቅርብ ፡ ነው ፡ አሉኝ ፡ የረፉድ ፤

ለቀደሙኝ ፡ ነው ፡ የማዝነው ፤
—ወይኔ ፡ የማልቀረው ።

ሠ ፡ መሄዱ ፡ ቍርጥ ፡ ነው ፤ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የማልቀር ፡ ነኝ ፤ እንዲ
ያው ፡ በከንቱ ፡ አረፈድሁ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ሞት ፡ የማይቀርልኝ ፡ ነው ፤ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ዐፈር ፡ መሆን ፡
አለብኝ ።

273 የየሩሳሌም ፡ ሴት ፡
ጎልጎታ ፡ ላይ ፡ ሠርታ ፡ ቤት ፡

እግዚአብሔር ፡ ያጥናሽ ፡ አልናት ፡ ወይ ፡
—ወልዳ ፡ አልሞታትም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ወልዳ ፡ ሞቶባት ፡ የለም ፡ ወይ ፤ ለምን ፡ ከልቅሶዋ ፡ አንደርስም ።

ወ ፡ እግዚአብሔር ፡ ወልድ ፡ (የማርያም ፡ ልጅ) ፡ ለኛ ፡ ሲል ፡ ተሰቅሎ ፡
ሞቶ ፡ የለምን ።

274 የደጃች ፡ ውቤ ፡ አዳራሽ ፡
ተሠርቶ ፡ ነበር ፡ በሻሽ ፤

ያቀሉት ፡ ነበር ፡ ያንን ፡ ኑሮ ፡
—እዳስ ፡ ገቡ ፡ ዘንድሮ ።

ሠ ፡ ከዳስ ፡ መቀመጥን ፡ ጭራሮ ፡ አውተርትሮ ፡ ቅጠል ፡ ከልሎ ፡ መኖ
ርን ፡ ዘንድሮ ፡ ዠመሩ ።

ወ ፡ ችግር ፡ ማግኘት ፡ ከጕዳት ፡ መድረስ ፡ መጨነቅ ፡ መጠበብ ፡ ገና ፡
ዛሬ ፡ ደረሰባቸው ፤ ዘንድሮ ፡ ዕዳ ፡ ገቡ ።

275 የደጃች ፡ ጐሹ ፡ ሞግዚት ፡
እኽል ፡ አታቀምስ ፡ በጊዜያት ፤

ወዲያ ፡ ይተዋት ፡ ትቅርብዎ ፤
—እናትም ፡ አትሆንዎ ።

ሠ ፡ እንደ ፡ እናት ፡ አታስብልዎም ፤ ጕዳትዎን ፡ አታውቅልዎም ፤ የልብ
ዎን ፡ አታደርስልዎም ።

ወ ፡ ከናት ፡ የምትበልጥ ፡ አሳቢዎ ፡ ናት ፤ እናትም ፡ እንደሷ ፡ አትሆንም ።

276 የዱሮ ፡ ሰዎች ፡ ውሃ ፡ ዋና ፡
ላይ ፡ ላዩን ፡ ነበር ፡ በጤና ፤

የዛሬ ፡ ልጆች ፡ ይበልጣሉ ፤
—ውስጥ ፡ ለውስጥም ፡ ይሄዳሉ ።　　　(ብ ፡ ጌ ፡ ኀ) ፡

ሠ ፡ እባሕር ፡ ውስጥ ፡ ጠልቀው ፡ ይዋኛሉ ፤ ውስጥ ፡ ውስጡን ፡ በዋና ፡ መሄድ ፡ ይችላሉ ።

ወ ፡ በረቀቀ ፡ ሁናቴ ፡ መሥራት ፡ ይችላሉ ፤ ይሆንላቸዋል ።

277 የጌታዬ ፡ ቤት ፡ ዋንጮች ፡
ሁሉም ፡ ጥቋቊር ፡ ቀያዮች ፡

በዚህ ፡ ሰጥተውኝ ፡ ምን ፡ ሊጠቅመኝ ፡
—በተሰቀለው ፡ ድገመኝ ።

ሠ ፡ በተሰቀለው ፡ ዋንጫ ፡ ስጠኝ ፤ በሱ ፡ ሞልተህ ፡ ዐድለኝ ፡ በሌላ ፡ ዕቃ ፡ ብትሰጠኝ ፡ አይጠቅመኝም ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ለኛ ፡ ሲል ፡ በተሰቀለው ፡ አምላክ ፡ ደጋግመህ ፡ ስጠኝ ፤ መላልሰህ ፡ ዐድለኝ ።

278 የጌታችንን ፡ ጠባይ ፡
ያለኔ ፡ የሚያውቀው ፡ አለ ፡ ወይ ፤

ማታ ፡ ለግብር ፡ መልካም ፡ ሰው ፡
—ቀን ፡ ሲቈጣ ፡ ክፉ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ቀን ፡ ቀን ፡ ይቈጣል ፤ ሲመሽ ፡ ትዕግሥተኛ ፡ ነው ፤ ማታ ፡ እንደ ፡ ቀን ፡ አያስፈራም ።

ወ ፡ ዘመን ፡ ሲጣላ ፡ ጊዜ ፡ ሲጥል ፡ ክፉ ፡ ነው ፤ አያድርስ ፡ ነው ።

279 የጥቊር ፡ በሬ ፡ ሥባቱ ፡
ከሻኛው ፡ ነወይ ፡ ከጅራቱ ፤

ቢሆንም ፡ ከሻኛው ፡
—ከጅራት ፡ የለው ።

ሠ ፡ ከጭራው ፡ ከጅራቱ ፤ ሥብ ፡ የለውም ፤ ከኋላው ፡ በኩል ፡ አይወፍርም ፤ ሥባቱ ፡ ከሻኛው ፡ ላይ ፡ ነው ።

ወ ፡ ከዳተኛ ፡ እራት ፡ ቅርስ ፡ የለውም ፤ ራሱን ፡ አይችልም ፤ ገንዘብ ፡ አያጠራቅምም ።

280 የጨዋ ፡ ልጅ ፡ ተዋርዶ ፡
ዕንጨት ፡ ሰበራ ፡ ቈላ ፡ ወርዶ ፡

ሲያነደው ፡ ያድራል ፡ ሌሊቱን ፡
—ቀን ፡ የሰበረውን ።

ሠ ፡ በብርሃን ፡ ያዘጋጀውን ፡ ማገዶ ፡ ማታ ፡ ያነደዋል ።

ወ ፡ ቀን ፡ ጊዜ ፡ ጥሎት ፡ ዘመን ፡ አዋርዶት ፡ የደረሰበት ፡ ችግር ፡ ያበሳጨዋል ፤ ያስቈጨዋል ።

281 ያለሚቱ ፡ ነገር ፡ ይረሳ ፤
በቃኝ ፡ እንግዲህ ፡ አይነካ ፤

በዝምድናዋ ፡ ስመካ ፡
—እሷስ ፡ ሞታለች ፡ ለካ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ዓለሚቱ ፡ በምትባለው ፡ ዘመዴ ፡ ስመካ ፡ ለካ ፡ እሷ ፡ ሞታ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ሞት ፡ አትቀርም ፤ ሳያስቧት ፡ ድንገት ፡ ትመጣለች ፤ ዓለም ፡ ታልፍበታለች ።

282 ያለጊዜያቱ ፡ ቢሄድ ፡
አለፈ ፡ እያሉ ፡ በመንገድ ፡

ስውር ፡ እንኳ ፡ አይደል ፡ ታየ ፡ ባይን ፡
—ሰዎች ፡ አነሡት ፡ ጌታዬን ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ጌታዬን ፡ አሙት ፤ ስሙን ፡ በክፉ ፡ አነሡት ፡ ሲቦጭቁት ፡ ሲያነሡት ፡ ሲጥሉት ፡ ዋሉ ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንንን ፡ ከወደቀበት ፡ ሰዎች ፡ ደርሰው ፡ አነሡት ፤ አወይ ፡ ጌታዬ ፡ እንደ ፡ ቀላል ፡ ነገር ፡ ሰውነቱ ፡ በሳንሳ ፡ ተነሣ ።

283 ያሰባችሁት ፡ ለጋብቻ ፡
እንዲሆናችሁ ፡ አምቻ ፡

አይምሰላችሁ ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡
—ከብት ፡ እረኛ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ለጋብቻ ፡ የተመኛችሁት ፡ ሰው ፡ የከብት ፡ እረኛ ፡ መንጋ ፡ ጠባቂ ፡ ራሱን ፡ ያልቻለ ፡ ሰው ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ሀብት ፡ ገንዘብ ፡ ለሰው ፡ ሕይወት ፡ ጠባቂ ፡ ነው ፤ በሱ ፡ ከማናቸውም ጉዳትና ፡ ችግር ፡ ለመዳን ፡ ይቻላል ።

284 ያባቴን ፡ አገር ፡ ዱጋውን ፡
ባስከለከለው ፡ ማሩን ፡

አበሉት ፡ አሉኝ ፡ ዘመዶቼ ፤
—እርሻ ፡ ማረጌን ፡ ትቼ ።

ሠ ፡ የማሩን ፡ መሬት ፡ ማረሴን ፡ ትቼ ፡ አሳደርሁት ፤ ሳልዘራው ፡ ቀረሁ።

ወ ፡ መከበሪያዬ ፡ ማዕርጌ ፡ የነበረውን ፡ ግብርናዬን ፡ መተዌ ፡ ቈጨኝ፤ አራሽ ፡ መሆን ፡ ይሻለኝ ፡ ነበር ።

285 —ያ ፡ ክፉ ፡ ጕንፋን ፡ ባልያዘሽ ፡
እቴ ፡ ምን ፡ ያምር ፡ ድምጥሽ ።

ሠ ፡ ክፉ ፡ ጒንፋን ፡ ሳል ፡ ከየት ፡ አገኘሽ ፤ ባልተነደፍሽ ፡ ባልተለከፍሽ ፡ ድምጥሽ ፡ እንዴት ፡ ያምር ፡ ነበር ።

ወ ፡ መጥፎ ፡ ጨቅጫቃ ፡ ነዝናዣ ፡ የሆነ ፡ ባል ፡ እንዴት ፡ አጋጠመሽ ።

286 ያወራዋል ፡ ደባውን ፡
—ወግ ፡ አርጎ ፡ መግደሉን ።　(ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ በጨቤ ፡ ወግቶ ፡ መግደሉን ፡ ደባውን ፡ ያወራዋል ፤ ጒዳን ፡ አይደብቅም ፤ ገመናውን ፡ አይሸፍንም ።

ወ ፡ በነገረ ፡ ሠሪነት ፡ ሰውዬውን ፡ መጒዳቱን ፡ ሞያ ፡ አድርጎ ፡ ያወራል ።

287 ያ ፡ የሠላጢን ፡ ምድር ፡
ሳያጣላንም ፡ አይቀር ።

የሚከተኙ ፡ ከናባቴ ፡
—ያ ፡ የደብሩ ፡ መሬቴ ።

ሠ ፡ ከነአባቴ ፡ የሚያስተዳድረኝ ፡ የደብሩ ፡ ርስቴ ፡ የእልቅናው ፡ መሬቴ ፣ ነው ።

ወ ፡ ከነዘመዶቼ ፡ የምቀበርበት ፡ መሬት ፡ በየቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ አላጣም ።

288 ያደግሁባትን ፡ መሬት ፡
ማነው ፡ ሜዳ ፡ ናት ፡ ያላት ፤

ልናገር ፡ እኔ ፡ የማውቃት ፡
—አገሬ ፡ ጋራ ፡ ናት ።　(ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡ (መዲ ፡ ቍ ፡ 290)

ሠ ፡ የተወለድኩባት ፡ አገር ፡ ተራራማና ፡ ኰረብታማ ፡ ናት ፤ ጋራ ፡ ሞልቶባታል ፤ ሜዳ ፡ አይደለችም ።

ወ ፡ አገር ፡ የጋራ ፡ የወል ፡ እንጂ ፡ የግል ፡ አይደለችም ፤ ለተወለዱባት ፡ ሁሉ ፡ መጠጊያ ፡ ነች ።

289 ይህ ፡ ሁሉ ፡ ድግስ ፡ ተደግሶ ፡
እንዳንሰደብ ፡ ዝግን ፡ አንሶ ፤

ነፍሴ ፡ ለሥጋ ፡ አትሟሽ ፡
—ገና ፡ ፍሪዳ ፡ አለልሽ ።

ሠ ፡ ነፍሴ ፡ ወዳጇ ፡ ፍቅሬ ፡ ፍሪዳ ፡ ተዘጋጅቶልሻል ፡ ሥጋ ፡ አለልሽ ፡ ትበያለሽ ፤ ጮማ ፡ ትቈርጫለሽ ።

ወ ፡ ሞት ፡ ሆነኔ ፡ አለብሽ ፡ ነፍሴ ፡ ፍሪ ፤ ለኋለኛው ፡ ዘመን ፡ አስቢ ፤ ዕለተ ፡ ሞትን ፡ አስታውሺ ፤ ዕዳ ፡ አለብሽ ።

290 ይህን ፡ ስናገር ፡ በውን ፡
ያስተባብሉኛል ፡ እኔን ፤

መች ፡ እናያት ፡ ነበር ፡ አሁን ፡
—አገሬ ፡ ጋራ ፡ ባትሆን ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡ (መዲ ፡ ቍ ፡ 288)

ሠ ፡ አገሬ ፡ ተራራማ ፡ ባትሆን ፡ ኖሮ ፡ መቼ ፡ እንዲህ ፡ በሩቁ ፡ እናያት ፡ ነበር ።

ወ ፡ አገር ፡ የሕዝብ ፡ ባይሆን ፡ ኖሮ ፡ መቼ ፡ ሕዝብ ፡ ላገሩ ፡ ይሞት ፡ ነበር ፤ ሰውስ ፡ ላገሩ ፡ የማይሞት ፡ ከሆነ ፡ አገር ፡ ወዴት ፡ ይገኝ ፡ ነበር ።

291 ይህን ፡ ክፉ ፡ መንገድ ፡
እየመራኸኝ ፡ እንሂድ ፤

ቀስ ፡ ብለህ ፡ እለፍ ፡ በዚያ ፡ በኩል ፡
—በኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሞት ፡ አትቸኵል ።

ሠ ፡ በንጉሥ ፤ በኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ቀስ ፡ ብለህ ፡ ተራመድ ፡ አትሩጥ ፤ አትቸኵል ፤ ዝግ ፡ እያልክ ፡ ሂድ ።

ወ ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ በኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ላይ ፡ ቸኵለህ ፡ አትምጣ ፤ በሱ ፡ ሕይወት ፡ አትጣደፍ ።

292 ይህ ፡ አሳላፊ ፡ ረስቶኝ ፡
ጠጁን ፡ ጨረሰው ፡ ሳይሰጠኝ ፤

ይሁን ፡ ጠጁ ፡ እንኳ ፡ ይቅርብኝ ፡
—ደግሞ ፡ ጠላ ፡ ከለከለኝ ።

ሠ ፡ ጠጁ ፡ እንኳ ፡ ቢያልቅ ፡ ጠላ ፡ ነፈገኝ ፤ ሳይሰጠኝ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ እኔን ፡ ጠላኝ ፤ አልወደደኝም ፤ አላፈቀረኝም ፤ ከስጦታው ፡ ነፈገኝ ፤ ነሣኝ ።

293 ይህ ፡ የምናየው ፡ ቅጠል ፡
ካበባዎቹ ፡ መካከል ፡

ሰፋ ፡ ሰፋ ፡ ያለው ፡
—ለካ ፡ ሴት ፡ አዙሪ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ከአታክልቱ ፡ መካከል ፡ የምንመለከተው ፡ ቅጠል ፡ «ሴት ፡ አዙሪ»፡ የሚባለው ፡ ነው ፡ ሌላ ፡ ቅጠል ፡ አይደለም ።

ወ ፡ ለካ ፡ መልካም ፡ ሴት ፡ መዞሪያ ፡ መከበሪያ ፡ ናት ፤ ቤት ፡ ወግ ፡ ማዕርግ ፡ የሚያገኘው ፡ በሴት ፡ ነው ።

294 ይንገር ፡ አይንገር ፡ ምን ፡ ዐውቃለሁ ፡
—መላኩን ፡ ልኬዋለሁ ።

ሠ ፡ ይድረስ ፡ አይድረስ ፡ አላውቅም ፡ እንጂ ፡ መልክተኛውን ፡ ልኬዋለሁ ፤ ተላላኪ ፡ ሰድጃለሁ ።

ወ ፡ መልአኩን ፡ ተማጥኛለሁ ፤ አማልደኝ ፡ ብዬዋለሁ ።

295 ይከፋሃል ፡ ወይ ፡ በልብህ ፡
—እንደ ፡ ሰሎሞን ፡ ነህ ፡ ብልህ ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ሰሎሞንን ፡ ትመስላለህ ፡ በመልክህ ፡ አንድ ፡ ነህ ፡ ብልህ ፡ ቅር ፡ ያሰኝሃልን ።

ወ ፡ እንደ ፡ ሰሎሞን ፡ ዐዋቂ ፡ ብልኅ ፡ አስተዋይ ፡ የጥበብና ፡ የአእምሮ ፡ ሰው ፡ ነህ ፡ ብልህ ፡ ይከፋህ ፡ ይሆን ።

296 ይኸ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ ከወሊሶ ፡
የሚሄድ ፡ መስሎኝ ፡ ተመልሶ ፤

ከጃንሆይ ፡ ጋራ ፡ የመጣው ፡
—ለካ ፡ ላዳሩ ፡ ነው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ለካ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ ለማደር ፡ ነው ፡ የመጣው ፤ አይመለስም ።

ወ ፡ ለካ ፡ ጃንሆይን ፡ ተከትሎ ፡ የመጣው ፡ ለደጅ ፡ ጥናቱ ፡ ትዳሩን ፡ ንብረቱን ፡ የግል ፡ ጥቅሙን ፡ ለማሻሻል ፡ ሲል ፡ ነው ።

297 ይፈልጋል ፡ አሉ ፡ ሰበብ ፡
የታወቀ ፡ ነው ፡ ረኀብ ፡

እንዲህ ፡ ያለውን ፡ ጭካኔ ፡
—እረ ፡ ተው ፡ አልሁት ፡ እኔ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እንዲህ ፡ ያለውን ፡ ጭካኔ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ መሥራት ፡ ይቅርብህ ፡ ብዬ ፡ መከርኩት ፤ ተው ፡ ብዬ ፡ ለመንኩት ።

ወ ፡ እኔ ፡ ምግብ ፡ ሳላገኝ ፡ እኽል ፡ ሳልቀምስ ፡ ባዶ ፡ አፌን ፡ ዋልኩ ።

298 ዲማ ፡ ደብረ ፡ ወርቅ ፡ ሞጣ ፡ ሁሉ ፡
ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ ቀረቡ ፡ አሉ ፤

ሞት ፡ አልፈራ ፡ ሆነኔ ፡
—በድን ፡ ተፈጥሬ ፡ እኔ ።

ሠ ፡ የማላውቅ ፡ ገልቱ ፡ ነኝ ፤ ነገር ፡ አይገባኝም ፤ አዙሮ ፡ ማየት ፡ አልችልም ፤ በድን ፡ ነኝ ።

ወ ፡ «ድን» ፡ በሚባል ፡ ቦታ ፡ ተወልጃለሁ ፤ በዚያ ፡ አገር ፡ እኖራለሁ ።

299 ዳዊት ፡ ጊዜቼ ፡ ባሥር ፡ ብር ፡
አስቤ ፡ ነበር ፡ ለመማር ፤

አሁን ፡ ግን ፡ እንጃ ፡ መማሬን ፡
—ወደ ፡ አምላኪ ፡ እንኳ ፡ መድረሴን ።

ሠ ፡ ከዳዊት ፡ መዝሙር ፡ «አምላኪየ» ፡ ከሚባለው ፡ እንኳ ፡ ሳልደርስ ፡ ቀረሁ ።

ወ ፡ በንስሓ ፡ ካልተመለስኩ ፡ ምሕረትን ፡ የማገኝ ፡ ከአምላክ ፡ ፊት ፡ የምደርስ ፤ መንግሥተ ፡ ሰማያትን ፡ የምወርስ ፡ አይመስለኝም ።

300 ድኻ ፡ ድኻውን ፡ ስትገለው ፡
—መኰንኑን ፡ ተወው ።

ሠ ፡ መኳንንቱን ፡ ተወው ፡ ድኻውን ፡ እንጂ ፡ ትልቅ ፡ ትልቁን ፡ ሰው ፡ አትንካ ።

ወ ፡ ድኻውን ፡ አትኰንነው ፤ መንግሥተ ፡ ሰማያት ፡ አውርሰው ፤ ሲኦል ፡ አታግባው ፤ መንጸፈ ፡ ደይን ፡ አታውርደው ።

301 ድንጋይ ፡ ተጭኖኝ ፡ ከበላዬ ፡
ላወርደው ፡ ሳስብ ፡ ከገርባዬ ፡

የሚረዳኝ ፡ ሰው ፡ አጣሁኝ ፤
—ሁሉም ፡ እኔን ፡ ተጫኑኝ ።

ሠ ፡ ተደራረቡብኝ ፤ ተረባረቡብኝ ፤ እላዬ ፡ ላይ ፡ ተዘፈዘፉ ፤ በጣም ፡ ከበዱኝ ፤ ተጫኑኝ ።

ወ ፡ በነገር ፡ አጠቁኝ ፤ ተረዳዱብኝ ፤ በደሉኝ ።

302 ድግስ ፡ ደግሰን ፡ ለእንግዳ ፡
ታርዶ ፡ ነበረ ፡ ፍሪዳ ፤

በጣም ፡ አማረ ፡ ጮማው ፡
ተስማሚ ፡ ሆነ ፡ ለሰው ።

ሥጋ ፡ ለመብላት ፡ ስንጥር ፡
—ያጥንት ፡ ጨርሶ ፡ እንዳይቀር ።

ሠ ፡ ምንም ፡ እንኳን ፡ በጣም ፡ የምንፈልገው ፡ ሥጋውን ፡ ለመብላት ፡ ቢሆን ፡ አጥንቱም ፡ ይጋጣል ፡ ጨርሶ ፡ መቅረት ፡ የለበትም ፡ እንዳይጣል ።
ወ ፡ የጥንቱ ፡ ወግና ፡ ልማድ ፡ እንዳይቀር ፡ ያገር ፡ ባህል ፡ እንዳይረሳ ፡ መጣጣር ፡ ነው ።

303 ድግስ ፡ ደግሶ ፡ በብሎት ፡
እንዴት ፡ ያቀርባል ፡ እልበት ፤

እሱስ ፡ የሚጥመው ፡
—ረቡ ፡ ቀን ፡ ሲገኝ ፡ ነው ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እልበት ፡ በፍስክ ፡ ቀን ፡ አያስፈልግም ፤ አይበላም ፤ ወስፋት ፡ አይቀበለውም ።

ወ ፡ በንግድ ፡ በርሻ ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡ የሚገኘው ፡ ጥቅም ፡ የሚያስደስተው ፡ መልካም ፡ ቀን ፡ ደኅና ፡ ዘመን ፡ ሲኖር ፡ ነው ።

304 ገረዶ ፡ ለምዳ ፡ ጨዋታ ፡
እኔ ፡ ብጠራት ፡ ወዶት ፡ ሰምታ ፤

አለች ፡ ይሉኛል ፡ ከዚያ ፡ ላይ ፡
—ወይ ፡ ብላ ፡ አትመጣም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ አቤት ፡ አትልም ፡ ወይ ፤ ሰምታ ፡ አትመጣም ፡ ወይ ፤ ጥሪዬን ፡ ለምን ፡ አትቀበልም ።

ወ ፡ ሳዝን ፡ ስተክዝ ፡ ፈጥና ፡ ሰሚዋ ፡ «ወይ ፡ ብላ ፡ ማርያም» ፡ አትረዳ ኝም ፡ ወይ ፤ ጸሎቴን ፡ አትሰማኝም ፡ ወይ ።

305 ገረዶ ፡ ሄዳ ፡ በድንገት ፡
አሽከሬ ፡ ሆኖ ፡ ወጥ ፡ ቤት ፡

የምበላውን ፡ ሳይጠይቀኝ ፡
—ሥጋ ፡ ሠርቶ ፡ አስጨነቀኝ ።

ሠ ፡ የሥጋ ፡ ወጥ ፡ ሠርቶ ፡ እንዳልበላ ፡ አደረገኝ ፤ ሳይስማማኝ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ ለባሲ ፡ አድርጎ ፡ ፈጥሮ ፡ አስጨነቀኝ ፡ ሸማች ፡ አድርጎኝ ፡ ተቸገርሁ ።

306 ገበሬ ፡ ሲያርሰው ፡ መሬቱን ፡
መች ፡ ዐወቀና ፡ ጥቅሙን ፤
—ያለም ፡ መኖሪያ ፡ መሆኑን ።

ሠ ፡ ጠቃሚነቱን ፡ አልተረዳም ፤ ለምነቱን ፡ አላወቀም ።

ወ ፡ ገበሬ ፡ ግብርና ፡ የዓለም ፡ ኑሮ ፡ መደገፊያ ፡ የተድላና ፡ ደስታ ፡ ማ ግኛ ፡ መሆኑን ፡ አልተገነዘበውም ።

307 —ገንዘቤ ፡ ጨርሶ ፡ ከጠፋማ ፡
ምን ፡ ያኖረኛል ፡ እከተማ ።

ሠ ፡ ገንዘቤ ፡ ካለቀ ፡ እከተማ ፡ ምን ፡ አደርጋለሁ ፤ ወደ ፡ ገጠር ፡ ወጥቼ ፡ በባላገር ፡ አልኖርምን ።

ወ ፡ «ገንዘቤ» ፡ ከሞተብኝ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ ምን ፡ ያደርግልኛል ፤ አልፈልገውም ።

308 ጉልበት ፡ ካለ ፡ አንተ ፡ ጓዶ ፡
መች ፡ ይጠፋል ፡ የርሻ ፡ ዘዶ ፤

በኋላ ፡ ኋላ ፡ እየተከተሉ ፡
—መሄድ ፡ እኮ ፡ ነው ፡ ዎ ፡ እያሉ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ዎ ፡ እያሉ ፡ በሬው ፡ ፈር ፡ እንዳይለቅ ፡ እየተጠባበቁ ፡ መከተል ፡ ነው ፡ ለርሻ ፡ ሌላ ፡ ዘዴ ፡ የለውም ።

ወ ፡ ዘመድ ፡ ወዳጅ ፡ ሲሞት ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ እያሉ ፡ እያለቀሱ ፡ ተራ ፡ በተራ ፡ በሞት ፡ መከታተል ፡ የማይቀር ፡ ነው ።

309 ጉንፋንስ ፡ ይሁን ፡ ይድናል ፤
—ሳል ፡ ሞትን ፡ ይሆናል ።

ሥ ፡ ሳል ፡ በሽታ ፡ ሞትን ፡ ያመጣልን ፤ ጉዳት ፡ ያስከትላልን ።

ወ ፡ ገና ፡ ሳልሞት ፡ ሳልቀበር ፡ እጄን ፡ ሳልንተራስ ፡ ይህ ፡ እንዴት ፡ ይሆ
ናል ።

310 ጌታ ፡ ሎሌውን ፡ ሲመክር ፡
ማታ ፡ ብቻውን ፡ ነበር ፡

ይኸ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ሲያየኝ ፡
—ምነው ፡ ቀን ፡ መታኸኝ ።

ሥ ፡ ምነው ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ቀጣኸኝ ፡ አዋረድኸኝ ፡ ገመናዬን ፡ ገላለጥህ
ብኝ ።

ወ ፡ ሰው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ በሚያይበት ፡ ዘመን ፡ እኔ ፡ ተጐሳቊልሁ ፡
ሰው ፡ ባገኘበት ፡ ወራት ፡ እኔ ፡ አጣሁ ፤ ነጣሁ ።

311 ግርማዊ ፡ ግርማዊት ፡
እግዜር ፡ ያጥናችሁ ፡ ቻሉት ፤
ከባድ ፡ ሐዘን ፡ ነው ፡ በውነት ፡
—የልጅ ፡ አባት ፡ ሲሞት ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሥ ፡ ብዙ ፡ ልጅ ፡ የወለደ ፡ ሲሞት ፡ ማዘን ፡ ማልቀስ ፡ የተገባ ፡ ነው ።

ወ ፡ የልጅ ፡ ዐዋቂ ፡ አስተዋይ ፡ መካሪ ፡ የነበረ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡
ሲሞት ፡ ያሳዝናል ፤ ጸጸቱ ፡ ትልቅ ፡ ነው ፤ ሐዘኑ ፡ ከሆድ፡ አይወጣም።

312 ጐንደር ፡ ወርጄ ፡ ቀስሼ ፡
ልብሰ ፡ ተክህኖ ፡ ለብሼ ፡

ታዩኛላችሁ ፡ እኔን ፡
—ነገ ፡ ገብቼ ፡ ሣጥን ።

ሥ ፡ ከመቅደስ ፡ ገብቼ ፡ ጥና ፡ ፊልብፊሌ ፡ ሳጥን ፡ ታዩኛላችሁ ።

ወ ፡ ሞቼ ፡ ከሣጥን ፡ ገብቼ ፡ ስቀበር ፡ ታዩኛላችሁ ።

313 ጐንደር ፡ ወርጄ ፡ ከመምህር ፡
መዋሥእት ፡ ዝማሬ ፡ ለመማር ፡

ዝማሬው ፡ እንኳ ፡ ቀናኝ ፤
—መዋሥእቱ ፡ ግን ፡ አስለቀሰኝ ።

ሥ ፡ መዋሥእት ፡ የሚባለው ፡ የዜማ ፡ ትምርት ፡ ከበደኝ ፤ አልገባም ፡
አለኝ ፤ ማጥናት ፡ አልቻልኩም ፤ ሰለቸኝ ።

ወ ፡ የሥጋ ፡ ወደሙ ፡ ነገር ፡ ገረመኝ ፡ ደነቀኝ ፡ አስለቀሰኝ ፤ ጥልቅ ፡ ምስ
ጢር ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ።

314 ጠላ ፡ ጠምቄ ፡ ለሰንበት ፡
አንሥቼው ፡ ነበር ፡ በቡዬት ፡

ዘወር ፡ ብዬ ፡ ባየው ፡ አጣሁት ፤
—ሰውን ፡ ጠጣው ፡ መሬት ።

ሠ ፡ ጠላውን ፡ ሰው ፡ ጠጣው ፡ ወይስ ፡ መሬት ፤ ምን ፡ ጨረሰው ፤ ማንስ ፡ ጨለጠው ።

ወ ፡ ሰውን ፡ ሞት ፡ ጨረሰው ፤ መቃብር ፡ ዋጠው ፤ መሬት ፡ በላው ።

315 ጠጅ ፡ እጠጣለሁ ፡ የቅንጦት ፤
ቡናም ፡ የሱስ ፡ መድኀኒት ፤

የጠጅን ፡ ነገር ፡ እነቅፋለሁ ፤
—የሱስ ፡ ያልከውን ፡ አምናለሁ ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ ለልማድ ፡ ለአምሮት ፡ ነው ፡ ያልከውን ፡ እቀበላለሁ ፤ ይህን ፡ ሐሳብህን ፡ እደግፋለሁ ፤ ሱስ ፡ ጠንካራ ፡ ነገር ፡ መሆኑ ፡ ይሰማኛል ፡ ይታወቀኛል ።

ወ ፡ የሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ሆይ ፡ ያዘዝከውን ፡ ያስተማርከውን ፡ አምናለሁ ፤ ቃልህን ፡ እቀበላለሁ ፤ ትእዛዝህንም ፡ እፈጽማለሁ ።

316 ጥንቱን ፡ ካገሬ ፡ ስወጣ ፡
ይገፎ ፡ ነበርኩኝ ፡ ትንሽ ፡ ቋንጣ ፤

ቀልጠፍ ፡ ብዬ ፡ ልመለስ ፡
—ሥጋዬን ፡ ሳልጨርስ ።

ሠ ፡ ለሥንቅ ፡ የያዝኩት ፡ ቋንጣ ፡ ፈጽሞ ፡ ሳያልቅ ፡ ወዳገሬ ፡ ልግባ ፡ ከወዳጅ ፡ ከዘመድ ፡ ልቀላቀል ።

ወ ፡ ሰውነቴ ፡ ጨርሶ ፡ ሳይጐዳ ፡ ሳይጐሳቈል ፡ ጕልበቴ ፡ ሳያልቅ ፡ ወዳገሬ ፡ ልሂድ ፤ ወደ ፡ ቀድሞ ፡ ቦታዬ ፡ ልመለስ ።

317 ጠሜን ፡ አደርኩኝ ፡ ደፋ ፡ ብዬ ፤
—ስንት ፡ ቀን ፡ ተጋድዬ ።

ሠ ፡ ስንት ፡ ቀን ፡ ለሆዴ ፡ ስል ፡ እጋደላለሁ ፤ ከብዙዎቹ ፡ አዛገሮች ፡ እጣላለሁ ፡ በማለት ፡ ጠሜን ፡ አደርኩ ።

ወ ፡ አዛኝ ፡ «ተጋድዬ» ፤ ስንት ፡ ቀን ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ መብል ፡ መጠጥ ፡ ስጠኝ ፡ እያልኩ ፡ እነዛነዛለሁ ፤ እጨቃጨቃለሁ ።

318 ፈረስ ፡ ሲገራ ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡
ራስ ፡ አቅንቶ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤

ለምን ፡ በልጓም ፡ ቀሰቀሰው ፤
—እንዲያው ፡ በመላለሰው ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ፈረሱን ፡ በልጓም ፡ ይዞ ፡ ባልገታው ፡ ሶምሶማ ፡ በለቀቀው ፡ ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ መለስ ፡ ቀለስ ፡ ባደረገው ።

ወ ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ የሚደርስበትን ፡ አያውቀውም ፤ በይሆናልና ፡ በመላ ፡ ይኖራል ።

319 ፍርስርስ ፡ አለ ፡ ቤቴ ፤
—ወይ ፡ ደገፉ ፡ ማጣቴ ።

ሠ ፡ ማስደገፊያ ፡ ባላ ፡ በማጣቴ ፡ ቤቴ ፡ ዘሞ ፡ ሊወድቅ ፡ ነው ፤ ድጋፍ ፡ ካላገኘሁ ፡ መፍረሱ ፡ ነው ።

ወ ፡ የሚረዳኝ ፡ በችግሬ ፡ ጊዜ ፡ የሚደግፈኝ ፡ ወገን ፡ አጋር ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ ዘመድ ፡ ስለሌለኝ ፡ ኑሮዬን ፡ ትዳሬን ፡ ማቃናት ፡ አልቻልኩም ፤ ንብረቴ ፡ መፍረሱ ፡ ነው ።

320 ፍርድ ፡ ልበስ ፡ የኔ ፡ ጌታ ፡
አሸከር ፡ አስነሣኝ ፡ ከገበታ ፡

እንኳን ፡ ለኔ ፡ ለሰው ፡
—ለሳት ፡ እራት ፡ አለው ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እሳት ፡ እንኳ ፡ የዕንጨት ፡ ማገዶ ፡ የብራብሮ ፡ እራት ፡ አለው ።

ወ ፡ እኔ ፡ በሥላሴ ፡ አምሳል ፡ የተፈጠርሁት ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ አሽከር ፡ ከገበታ ፡ አስነሥቶኝ ፡ እራት ፡ ልጣ ።

321 ፍቅር ፡ ደገደገ ፡ ምነው ፡ ከሳ ፡
በጽልሑት ፡ በቀል ፡ ነቀርሳ ፤

ማን ፡ ባመጣልኝ ፡ እምነት ፤
—እሱ ፡ ነበር ፡ መድኀኒት ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የምጠጣው ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ እምነት ፡ ማን ፡ ባመጣልኝ ፡ ለመድኀኒት ፡ ያኸል ፡ የሚሰጠኝ ፡ ሰው ፡ የት ፡ አገኛለሁ ።

ወ ፡ አሁን ፡ ታማኝ ፡ የሆነ ፡ ራሱ ፡ የማይበልጠው ፡ ሰው ፡ ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ የት ፡ ይገኛል ፤ ከቶ ፡ እምነት ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ የት ፡ አለ ።



ሁለተኛ ፡ ምዕራፍ ።

# ዘለሰኛ ።

1 ሁለት ፡ ወር ፡ ሑዳዴን ፡ አጥርተው ፡ ጠመው ፡
—በውሃ ፡ ገደፉ ፡ ሥጋውን ፡ ትተው ።

ሠ ፡ ጠመው ፡ ጠመው ፡ ቅቤና ፡ ሥጋ ፡ አላገኙም ፤ በውሃ ፡ ገደፉ ።
ወ ፡ በፋሲካ ፡ ምድር ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ ወሰዳቸው ፤ የትንሣኤ ፡ ለት ፡ በረፉ ።

2 ሁለት ፡ ጊዜ ፡ በላሁ ፡ እዚህ ፡ ቤት ፡ ገብቼ ፤
—ፊትም ፡ በወረራ ፡ ዛሬም ፡ ተመርቼ ። (1) (መዲ ፡ ቍ ፡ 149) ፡

ሠ ፡ ተደልድዬ ፡ ተመርቼ ፡ በላሁ ።
ወ ፡ ዐይን ፡ ስውር ፡ ሆኜ ፡ በሰው ፡ እጅ ፡ እየተመራሁ ፡ እጌታዬ ፡ ቤት ፡ ግብር ፡ ገባሁ ፤ ብርሃኔን ፡ አጥቼ ፡ ማየት ፡ ተሳነኝ ።

3 ሀብታሞቹ ፡ ሁሉ ፡ ጨርሰው ፡ ዘርተው ፡
—መኰንን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ዘር ፡ የተረፈው ።

ሠ ፡ የሚዘራው ፡ ያልተቸገረ ፡ የዘር ፡ ን ሩ ፡ ያላጣ ፡ መኰንን ፡ ብቻ ፡ ነው ።
ወ ፡ ስም ፡ የሚያስጠራ ፡ ለዙፋን ብቃ ፡ የተባረከ ፡ ልጅ ፡ ያገኘ ፡ እንደ ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ የለም ።

4 —ኻያ ፡ ኻያ ፡ ይላል ፡ ሁሉም ፡ በየቤቱ ፡
እኔ ፡ ቍጥሩ ፡ ጠፍቶኝ ፡ አንድና ፡ ሁለቱ ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ሰዎች ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ ማለት ፡ አቅቶኝ ፡ ኻያ ፡ ኻያውን ፡ አንድ ፡ እያሉ ፡ ይቈጥራሉ ፤ ኻያ ፡ ኻያ ፡ እያሉ ፡ ያሰላስላሉ ።
ወ ፡ በወላምኛ ፡ ቋንቋ ፡ ወዲህ ፡ ና ፡ እያሉ ፡ «ኻያ ፡ ኻያ» ፡ ይላሉ ፤ አሽከር ፡ አገልጋይ ፡ እያገኙ ፡ ተደስተዋል ።

5 ሁለቱን ፡ ታማለህ ፡ አንዱን ፡ ትገድላለህ ፤
—የሴት ፡ ልጅ ፡ ነህና ፡ ፍርድ ፡ ወዴት ፡ ታውቃለህ ።

ሠ ፡ መረን ፡ ያደግህ ፡ ማመዛዘን ፡ የማትችል ፡ ሴት ፡ ያሳደገህ ፡ ነህ ፤ ፍርድ ፡ አታውቅም ፤ ታደላለህ ።
ወ ፡ ከሴቶች ፡ ሁሉ ፡ የተባረከች ፡ ከሆነችው ፡ ከድንግል ፡ ማርያም ፡ የተወለድክ ፡ አምላክ ፡ ሆይ ፡ ለምን ፡ ሁለቱን ፡ አመህ ፡ አንዱን ፡ ትገድላለህ ፤ ፍርድህ ፡ አልተዛባምን ።

(1) ታላቁ ፡ ራስ ፡ ኀይሉ ፡ ባለሟላቸውን ፡ ደጃች ፡ ወልታን ፡ በሤረኛነት ፡ ጠርጥረዋቸው ፡ ኖሮ ፡ ነገሩን ፡ ሳያጣሩና ፡ ሳይመረምሩ ፡ ዐይናቸውን ፡ አጥፍተው ፡ በግዞት ፡ ካቈዩዋቸው ፡ በኋላ ፡ እውነቱ ፡ ተገልጦ ፡ ይቅርታ ፡ ተደርጎላቸው ፡ በግብር ፡ ላይ ፡ ሳሉ ፡ ሐዘናቸውንና ፡ ጸጸታቸውን ፡ የገለጹበት ።

6 ሁል ፡ ጊዜ ፡ በሥጋት ፡ በዱር ፡ ከመኖር ፡
—ቆቅስ ፡ ብትመረቅ ፡ ይሻላት ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ብትመረቅ ፡ ብትባረክ ፡ ብትለምድ ፡ የቤት ፡ ዶሮ ፡ ብትሆን ፡ አውሬነቷ ፡ ቢቀር ፡ ይሻለት ፡ ነበር ።

ወ ፡ ቆቋ ፡ ብትታረድና ፡ ተቀቅላ ፡ መረቅ ፡ ብትሆን ፡ መልካም ፡ ነበር ።

7 ሁል ፡ ጊዜ ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡ በልቤ ፡ እመኛለሁ ፤
—አንድም ፡ ማዘን ፡ የለኝ ፡ ወይኔት ፡ አገኛለሁ ።

ሠ ፡ የቤት ፡ መሥሪያ ፡ ዕንጨት ፡ ተቸገርሁ ፤ ቋሚ ፡ ማእዘን ፡ አጣሁ ።

ወ ፡ ምንም ፡ ለሰው ፡ የሚያዝን ፡ ታጣ ፤ የሚጾም ፡ የሚጸልይ ፡ አልተገኘም ፤ ማዘን ፡ መተከዝ ፡ ተረሳ ።

8 ለሀብታም ፡ ጥድ ፡ ሰጥቶ ፡ እልፍኙን ፡ ሲያስፋፋ ፡
—እየው ፡ መኰንኔ ፡ ለድኻው ፡ ቀንጠፋ ። (ዘ ፡ ወ ፡ ጸ) ፡

ሠ ፡ ለድኻው ፡ ቀንጠፋ ፡ የሚባል ፡ ዕንጨት ፡ ተሰጠ ፤ ጥድ ፡ ወይራ ፡ ዝግባ ፡ አልተገኘም ።

ወ ፡ መልካሙ ፡ ጊዜ ፡ አለቀ ፡ በመኰንን ፡ ዕረፍት ፡ የዓለም ፡ ማያው ፡ ዘመን ፡ አለፈ ።

9 ለላሞቹ ፡ እረኛ ፡ ማንን ፡ አርጋችኋል ፤
ለበጎቹ ፡ እረኛ ፡ ማንን ፡ አርጋችኋል ፤
—እንደኔ ፡ ልጅ ፡ በቅሎ ፡ ይጠፋባችኋል ።

ሠ ፡ የልጇ ፡ በቅሎ ፡ እንደ ፡ ጠፋ ፡ የናንተም ፡ እንዳይጠፋባችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፤ አጥብቃችሁ ፡ ጠብቁ ።

ወ ፡ እንደኔ ፡ ልጅ ፡ ፈጥኖ ፡ በሕፃንነቱ ፡ እንዳይቀጠፍባችሁ ፡ ተጠንቀቁ ፤ እዘኑ ፡ ለምኑ ።

10 ለልጅ ፡ ልጅ ፡ ለምልሞ ፡ እንዲህ ፡ የሚታየው ፡
—ይህ ፡ አትክልታችን ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ነው ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ከሁን ፡ በፊት ፡ ያልታየ ፡ ያልታወቀ ፡ ያልተለመደ ፡ አዲስ ፡ የመጣ ፡ አበባ ፡ ነው ።

ወ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ዋና ፡ ከተማ ፡ የንጉሠ ፡ ነገሥቱ ፡ መናገሻ ፡ መዲና ፡ ነው ።

11 ለመቃኑ ፡ ሥራ ፡ ተገኝቷል ፡ ጠራቢ ፤
—ለቅጥሩም ፡ እንደሆን ፡ አይታጣም ፡ ካቢ ።

ሠ ፡ ግንቢ ፡ አይጠፋም ፡ የሚክብ ፡ አይታጣም ፤ የግንብ ፡ ሠራተኛ ፡ ሞልቷል ።

ወ ፡ ለሚሬው ፡ ለዐድማው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ካቢ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ አይጠፋም ።

12 ለመታሰቢያ ፡ ነው ፡ እግዜር ፡ የሠራቸው ፤
—በሰማይ ፡ ኤልያስ ፡ በምድር ፡ ይድነቃቸው ።　(ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እግዚአብሔር ፡ መታሰቢያ ፡ አድርጎ ፡ ኤልያስን ፡ ይድነቃቸውን ፡ የፈጠራቸው ፡ ለታሪክ ፡ ነው ።

ወ ፡ ኤልያስ ፡ ወደ ፡ ሰማይ ፡ በመውጣቱ ፡ የምድር ፡ ሰዎች ፡ ይገረሙ ፤ ይደነቁ ።

13 ለማለዳ ፡ ቍርስስ ፡ ቡን ፡ ሲያውል ፡ አየነው ፤
—የሚያስቀና ፡ ለሰው ፡ የማታ ፡ እንጀራ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ሰውን ፡ ደስ ፡ የሚያሰኘው ፡ ለቍርስ ፡ የሚቀርበው ፡ ምግብ ፡ ሳይሆን ፡ በራት ፡ ሰዓት ፡ የሚያገኘው ፡ እንጀራ ፡ ነው ።

ወ ፡ በልጅነት ፡ በወጣትነት ፡ ከሚገኘው ፡ ተድላና ፡ ደስታ ፡ ይልቅ ፡ በስተርጅና ፡ ዐይን ፡ ሲፈዝ ፡ ጕልበት ፡ ሲደነግዝ ፡ የሚገኘው ፡ ሀብት ፡ እጅግ ፡ ጠቃሚ ፡ ነው ።

14 ለማረፊያ ፡ ብለው ፡ ንጉሥ ፡ ቢሰጡት ፡
—በዛብህ ፡ አፍቀራን ፡ ጕልት ፡ አደረጋት ። (1)

ሠ ፡ ራስ ፡ በዛብህ ፡ አፍቀራ ፡ የሚባለውን ፡ አገር ፡ ርስተ ፡ ጕልት ፡ ተተከሉ ።

ወ ፡ ራስ ፡ በዛብህ ፡ በግዞት ፡ አፍቀራ ፡ ላይ ፡ እንዳሉ ፡ ዐረፉ ፤ ከዚያ ፡ ተቀበሩ ።

15 ለምለሙን ፡ በልቼ ፡ እንዳልሞትብዎ ፡
—አይተው ፡ ዝም ፡ አይበሉኝ ፡ ተራሰው ፡ መስሎዎ ።

ሠ ፡ ደረቅ ፡ እንጀራ ፡ ስበላ ፡ ታንቄ ፡ እንዳልሞትብዎ ፡ ወጥ ፡ ያለበት ፡ በመረቅ ፡ የራሰ ፡ እንዳይመስልዎ ።

ወ ፡ ዕውቀት ፡ የሌለው ፡ ተራ ፡ ሰው ፡ እንዳልመስልዎ ።

16 ለምለሻ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ሁሉም ፡ ይመኙሻል ፤
—ተፈሪ ፡ ባል ፡ አለሽ ፡ ወዴት ፡ ያገኙሻል ።

ሠ ፡ የሚያስፈራ ፡ የሚያስከብር ፡ ባል ፡ አለሽ ። ማን ፡ ይደፍርሻል ? ማንስ ፡ ያገኝሻል ?

ወ ፡ ንጉሥሽ ፡ ዐፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ተፈሪ ፡ ነው ። ጠላት ፡ አያጠቃሽም ፤

17 ለምን ፡ ይዘሸዋል ፡ ዳዊቱን ፡ ለምስል ፤
—ከስብሐት ፡ ለአብ ፡ ወዲያ ፡ ይደገም ፡ ይመስል ።

ሠ ፡ ስብሐት ፡ ለአብ ፡ ከተባለ ፡ በኋላ ፡ ሌላ ፡ ጸሎት ፡ ላይደገም ፡ ለምን ፡ ዳዊቱን ፡ ያዝሸው ።

ወ ፡ ሊቁ ፡ ስብሐት ፡ ለአብ ፡ ከሞተ ፡ ሌላ ፡ አጠናቆ ፡ የሚደግመው ፡ ሰው ፡ የለም ፡ ዳዊቱን ፡ ለምን ፡ ያዝሸው ።

---

(1) ራስ ፡ በዛብህ ፡ ተግዘው ፡ አፍቀራ ፡ ከሚባለው ፡ አምባ ፡ ላይ ፡ በእስራት ፡ ሳሉ ፡ ስለ ፡ ሞቱ ፡ የተነገረ ።

18 ለምን ፡ ገለበጥሁት ፡ ወተቱን ፡ በጋን ፡
—ችዬ ፡ እገፋዋለሁ ፡ የማልለውን ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 798) ፡

ሠ ፡ ችዬ ፡ የማልንጠውን ፡ ወተት ፡ አሁን ፡ ለምን ፡ በጋን ፡ አደረግሁት ?
ወ ፡ ከማልገፋው ፡ ባላጋራ ፡ ለምን ፡ እታገላለሁ ፤ ብተወው ፡ አይሻልምን ?

19 ለሠሪው ፡ ለመስጠት ፡ ዐፈሩን ፡ ይገርለሁ ፤
—ገል ፡ ዐፈር ፡ መሆኑን ፡ ተረድቼዋለሁ ።

ሠ ፡ ሸክላ ፡ ከዐፈር ፡ የሚሠራ ፡ መሆኑን ፡ ዐወቅሁ ፤ ገል ፡ ከዐፈር ፡ የሚ ገኝ ፡ መሆኑን ፡ ተገነዘብሁ ።
ወ ፡ ገላችን ፡ በሞትን ፡ ጊዜ ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ መሆኑን ፡ ተረዳሁ ፤ ከንቱነታችን ፡ ገባኝ ።

20 ለማህለ ፡ ሥላሴ ፡ ከሆንኩት ፡ ወዳጅ ፡
—እንበ. ፡ ፈርሶ ፡ አልጠጣም ፤ እጥላለሁ ፡ ጠጅ ። (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ ጠጅ ፡ እንጂ ፡ ጠላ ፡ (ፈርሶ) ፡ አልጠጣም ፤ ሌላ ፡ መጠጥ ፡ አልፈቅ ድም ።
ወ ፡ ማህለ ፡ ሥላሴ ፡ ሞቶ ፡ እኔ ፡ ጠላ ፡ እየጠጣሁ ፡ አልደሰትም ።

21 —ለሥጋ ፡ ዐርብን ፡ ሸጦ ፡ ሆድን ፡ ከመሙላት ፡
—መለመን ፡ ይሻላል ፡ በጾም ፡ በጸሎት ። (በ ፡ ማ ፡ )

ሠ ፡ የሸማኔው ፡ ዕቃ ፡ ዐርቡ ፡ ተሸጦ ፡ ገንዘቡን ፡ ለምግብ ፡ ከማዋል ፡ መራብ ፡ መጠማት ፡ ይሻላል ።
ወ ፡ ለክርስቲያን ፡ የሚበጀው ፡ ጠንክሮ ፡ መጾሙ ፡ ነበር ፤ የዐርብን ፡ ጦም ፡ ሽሮ ፡ ሥጋ ፡ መብላት ፡ የሚገባ ፡ አይደለም ፤ የሚያጸይፍ ፡ ነው ።

22 ለርሻ ፡ ሄጄ ፡ ነበር ፡ ካባት ፡ ከናቴ ፡ አገር ፡
—ተመልሼ ፡ መጣሁ ፡ አጥቼ ፡ አንድ ፡ እንኳ ፡ ዘር ።

ሠ ፡ ከናትና ፡ አባቴ ፡ አገር ፡ ለርሻ ፡ ሄጄ ፡ ለዘር ፡ የሚሆን ፡ እኽል ፡ አጥቼ ፡ ተመለስኩ ።
ወ ፡ አገሬ ፡ ብሄድ ፡ ተወላጆቼ ፡ ሁሉ ፡ ሞተው ፡ አንድም ፡ ዘር ፡ አጥቼ ፡ ተመልሼ ፡ መጣሁ ።

23 ለሰሚው ፡ ዕጹብ ፡ ነው ፤ ላየውም ፡ ይደንቃል ።
—እንዴት ፡ አንድ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ በማበል ፡ ያልቃል ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በውሃ ፡ ሙላት ፡ አለቀ ፤ ፈረሰኛውን ፡ ማዕበሉ ፡ እያጣ ደፈ ፡ ወሰደው ።
ወ ፡ በሐሰት ፡ በስብቀት ፡ ሰው ፡ ተጐዳ ፤ በውሸት ፡ ከሞት ፡ አደጋ ፡ ደረሰ ።

24 ለሰሚው ፡ ደንቆታል ፡ ላየውም ፡ ፍጥረት ፡
—ተሸክሞ ፡ ወስዶ ፡ አልጋውን ፡ መስጠት ።

ሠ ፡ የሚተኛበትን ፡ አልጋውን ፡ መልቀቅ ፡ ተገቢ ፡ አልነበረም ።
ወ ፡ አልጋውን ፡ ማስወሰድ ፡ አገሩን ፡ ግዛቱን ፡ መተው ፡ ይገርማል ።

25 ለቀጣሪው ፡ ፈተልኩ ፡ ለዳኛው ፡ ቀረብኝ ፤
—በል ፡ ታሰር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ምን ፡ አለብኝ ።

ሠ ፡ ባለመስጠቴና ፡ ባለማስደሰቴ ፡ ከመታሰር ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ምን ፡ ይደርስብኛል ።
ወ ፡ ሞቶ ፡ ከመገነዝ ፡ ሌላ ፡ ምን ፡ ይመጣብኛል ፡ ብዬ ፡ እሠጋለሁ ።

26 ለተገፋ ፡ ሁሉ ፡ ፍርድ ፡ እንዳይታጣ ፡
—ድመት ፡ ሌሊት ፡ አይሂድ ፡ አይጥም ፡ ቀን ፡ አይምጣ ።

ሠ ፡ ዐይጥ ፡ ቀን ፡ ከጕድጓድ ፡ አይውጣ ፤ በብርሃን ፡ አይምጣ ።
ወ ፡ የማይጥም ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ አይምጣ ፤ መጥፎ ፡ ዘመን ፡ አያሳየን ።

27 ለኔም ፡ ከነቢያት ፡ አንዱ ፡ ደረሰኝ ፤
—ዕንባቆም ፡ ብለውም ፡ ዐይኔን ፡ እንቢ ፡ አለኝ ።　(ወ ፡ ሀ) ።

ሠ ፡ እንባዬ ፡ አልቆም ፡ አለኝ ፤ ቢወርድ ፡ ቢወርድ ፡ ማቆሚያ ፡ ጠፋበት ።
ወ ፡ ዕንባቆምም ፡ ብዬ ፡ ከነቢያት ፡ ስም ፡ ብጠራውም ፡ ልጁ ፡ ከሞት ፡ ሊድን ፡ አልቻለም ።

28 ለኔስ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ በባላገር ፡ ያለሽ ፤
—ማነው ፡ የጁ ፡ ወስዶ ፡ መርጦ ፡ ያስቀመጠሽ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 427 ፡ 576) ፡

ሠ ፡ በየጁ ፡ መርጦ ፡ ከሚባለው ፡ ከተማ ፡ ያስቀመጠሽ ፡ ማነው ።
ወ ፡ የወደደሽ ፡ በቍንጅናሽ ፡ የመረጠሽ ፡ ማነው ።

29 ለኔ ፡ እየመሰለኝ ፡ ቤቴን ፡ የሠራሁ ፡
—ባላውቀው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ለካ ፡ አፈርሳለሁ ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ቤቴን ፡ የሠራሁ ፡ እየመሰለኝ ፡ አፈርሰዋለሁና ፡ አእምሮዬ ፡ ጠፍቷልን ።
ወ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ እየተታለልሁ ፡ አይሰማኝም ፡ እንጂ ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ በመቃብር ፡ እፈርሳለሁ ፤ እበሰብሳለሁ ።

30 ለኔ ፡ የት ፡ ታወቀኝ ፡ ጠላቴስ ፡ ወዳጁ ፤
—እንዲያው ፡ ቍቁ ፡ ሲባል ፡ ሁሉም ፡ መጡ ፡ ደጁ ።

ሠ ፡ ሁሉም ፡ ከያለበት ፡ አንድ ፡ ሳይቀር ፡ እደጁ ፡ መጣ ።
ወ ፡ ጠላቴ ፡ ወዳጅ ፡ መስሎ ፡ ጕዳቴን ፡ አይቶ ፡ ለመደሰት ፡ ተቀላቅሎ ፡ እደጁ ፡ መጣ ።

31 ለነዚያ ፡ ፋሽስቶች ፡ መድኀኒት ፡ ስጧቸው ፤
—የሚያስቀምጥ ፡ ሳይሆን ፡ የሚያስመልሳቸው ።

ሠ ፡ ለኒያ ፡ ሰዎች ፡ የሚያስቀምጥ ፡ ሳይሆን ፡ ለትውከት ፡ ብቻ ፡ የሚረዳ ፡ መድኀኒት ፡ በሰጧቸው ፤ የሚያስመልስ ፡ ቋቅ ፡ የሚያሰኝ ፡ ነገር ፡ በሰጧቸው ።

ወ ፡ እንግዲህ ፡ እነዚህን ፡ ፋሽስቶች ፡ በብርቱ ፡ ወግታችሁ ፡ አስወጧቸው ፤ ወደ ፡ አገራቸው ፡ መልሷቸው ።

32 ለካስ ፡ ቄስ ፡ በሬ ፡ ነው ፡ እየጠጣ ፡ ውሃ ፡ እየበላ ፡ ሣር ፡
—ሲሞት ፡ ፈቶት ፡ ሄደ ፡ ያን ፡ ሁሉ ፡ አገር ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ለሞተው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ጸሎተ ፡ ፍትሐት ፡ አድርሶለት ፡ ሄደ ፤ እየፈታ ፡ ሙታኑን ፡ ሸኛቸው ።

ወ ፡ የከብት ፡ እልቂት ፡ ሕዝቡን ፡ በችጋር ፡ ፈታው ፤ ብዙ ፡ ሰው ፡ በረኃብ ፡ ሞተ ።

33 ለለት ፡ እራት ፡ እንኳ ፡ ትንሽ ፡ ሥንቅ ፡ አልያዝህ ።
—ምን ፡ በላህና ፡ ነው ፡ ውድማ ፡ የቀረህ ።

ሠ ፡ ለምንድነው ፡ ለምሳ ፡ ያልመጣኸው ፤ ምን ፡ በልተህ ፡ ዋልክ ።

ወ ፡ ከውድማ ፡ የቀረኸው ፡ ምን ፡ አግኝተህ ፡ ይሆን ፤ ምን ፡ አውሬ ፡ በልቶህ ፡ ነው ፡ እቤትህ ፡ ያልመጣኸው ።

34 ለዳኛ ፡ ሳይነግሩ ፡ ምስክር ፡ ሳይጠሩ ፡
—ስሜነኞች ፡ ከብቴን ፡ ቀምተውኝ ፡ ቀሩ ። (1)

ሠ ፡ ያለፍርድ ፡ ከብቴን ፡ ወሰዱብኝ ፤ ያለብይን ፡ ሀብቴን ፡ ዘረፉኝ ።

ወ ፡ ስሜነኞች ፡ ባሌን ፡ ከብቴን ፡ ገደሉብኝ ፡ ያለምክንያት ፡ ደበደቡት ።

35 ለድኻም ፡ ለሀብታም ፡ እንዳይጐድል ፡ ፍርዱ ፡
—እናንት ፡ መኳንንቶች ፡ እንደ ፡ ራስ ፡ ፍረዱ ። (ግ ፡ ው) ፡

ሠ ፡ ነግ ፡ በኔ ፡ ብላችሁ ፡ እውነተኛውን ፡ ትክክለኛውን ፡ ነገር ፡ ፍረዱ ፤ አታድሉ ።

ወ ፡ እንደ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ እውነተኛ ፡ ሁኑ ፤ ቃላችሁን ፡ አታጓድሉ ፤ ታማኝ ፡ ሁኑ ።

36 ለጠጁ ፡ ነበረ ፡ ብቸና ፡ መሂዴ ፤
—ዲማ ፡ ሥጋ ፡ አላጣም ፡ ታረዱ ፡ ዘመዴ ።

ሠ ፡ ዘመዶቼ ፡ ፍሪዳ ፡ ካረዱ ፡ ሥጋ ፡ አገኛለሁ ፤ አላጣም ።

ወ ፡ ዘመዶቼ ፡ በሰይፍ ፡ ተከለሉ ፡ አንገታቸውን ፡ ለስለት ፡ ሰጡ ።

37 ለፈረስ ፡ ለበቅሎ ፡ ይተርፍ ፡ የነበረ ፤
—ዛሬስ ፡ ለሰው ፡ ያኽል ፡ ይቸግር ፡ ዠመረ ።

---

(1) ከብቴ ፡ የሚባል ፡ የበጌምድር ፡ ሰው ፡ ስሜን ፡ ሄዶ ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ ልጆች ፡ ወልዶ ፡ ሲኖር ፡ በሚስቱ ፡ ርስት ፡ ምክንያት ፡ ከዘመዶቿ ፡ ጋራ ፡ ሲከራከር ፡ ቈይቶ ፡ በመጨረሻው ፡ ስለ ፡ ገደሉት ፡ ሚስቱ ፡ በሐዘን ፡ ተነድፋ ፡ ገዳዮቹም ፡ ዘመዶቿ ፡ መሆናቸውን ፡ በልቧ ፡ ዐውቃ ፡ የገጠመችው ።

ሠ ፡ ለፈረስ ፡ ለበቅሎ ፡ ይሰጥ ፡ የነበረው ፡ እኽል ፡ ዛሬ ፡ ጠፋ ፤ ሊገኝ ፡ አል
ተቻለም ፤ ተወደደ ።

ወ ፡ ያ ፡ ለከብት ፡ ይተርፍ ፡ የነበረው ፡ እኽል ፡ ለሰው ፡ ምግብ ፡ እንኳን ፡
ታጣ ፤ ረኃብ ፡ ሆነ ፤ ችጋሩ ፡ ጠና ።

38 ሊቃውንት ፡ ዐዋቆች ፡ ከሆናችሁማ ፡
—በሉ ፡ ቀን ፡ ፍጠሩ ፡ ሳይመጣ ፡ ጨለማ ።

ሠ ፡ ፀሓይን ፡ አውጡ ፤ ብርሃንን ፡ አምጡ ፤ ጨለማውን ፡ አስወግዱ ፤ ሌሊ
ቱን ፡ አርቁ ።

ወ ፡ ደኅና ፡ ዘመን ፡ አምጡ ፤ ይኽን ፡ ክፉ ፡ ሰዓት ፡ አሳልፉ ፤ ወደ ፡ መል
ካም ፡ ወረት ፡ ለውጡ ፤ አሸጋግሩት ።

39 ሊነጣልኝ ፡ ነበር ፡ ሸማ ፡ እጥበት ፡ መሄዴ ፤
—ተመልሼ ፡ መጣሁ ፡ አነሰና ፡ እንዶዴ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 498) ፡ አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ እንዶድ ፡ አነሰኝ ፤ ማጠቢያ ፡ አጣሁ ፤ ልብስ ፡ ማጽጃ ፡ ተቸገርኩ ።

ወ ፡ እንዶዴ ፡ እሚባለው ፡ አገር ፡ አልሄድም ፤ አነሰኝ ፤ ሌላ ፡ አገር ፡ ይለ
ወጥልኝ ።

40 ላንተ ፡ ለወንድሜ ፡ የልቤን ፡ ልንገርህ ፤
—ትምርቱ ፡ ካልገባኝ ፡ ጭሬ ፡ ልብላ ፡ እንግዲህ ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ በግብርና ፡ በርሻ ፡ ልተዳደር ፤ እየቈፈርኩ ፡ መሬቴን ፡ እያለማሁ ፡
ልኑር ።

ወ ፡ ጸሓፊ ፡ ሆኜ ፡ ልኑር ፤ የጽፈት ፡ ቤት ፡ ሠራተኛ ፡ ልሁን ።

41 ላንች ፡ ቀረብህ ፡ እንጂ ፡ የሎሌ ፡ ያገር ፡ ጣዕም ፤
—እኔን ፡ አንገልትቶ ፡ ይገዛኝ ፡ አላጣም ።

ሠ ፡ ወግ ፡ ማዕርግ ፡ አይኑረኝ ፡ እንጂ ፡ እኔን ፡ እያንገላታ ፡ የሚገዛኝ ፡ የሚ
ያስተዳድረኝ ፡ አይጠፋም ።

ወ ፡ አንገል ፡ እሚባል ፡ አገር ፡ ብትተወኝም ፡ ባገልግሎቴ ፡ የሚፈልገኝ ፡
አላጣም ፤ ላንተ ፡ ይብላኝ ፡ እንጂ ፡ ሠርቼ ፡ የማድር ፡ ነኝ ።

42 ሌሊት ፡ ከጭቃ ፡ ላይ ፡ ፈረስ ፡ ቢጥልህ ፡
ወንድሜ ፡ አትናደድ ፡ ማንም ፡ አላየህ ፤
—ይልቁን ፡ ተጠንቀቅ ፡ ቀን ፡ እንዳይጥልህ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ በሚያይበት ፡ ጊዜ ፡ እንዳትወድቅ ፡ ተጠንቀቅ ፤ እንዳያድጥህ ፡
በብርሃን ፡ እያየህ ፡ ሂድ ።

ወ ፡ ዘመን ፡ እንዳያዋርድህ ፡ ክፉ ፡ ጊዜ ፡ እንዳይገጥምህ ፡ እዘን ፤ ፈጣሪ
ህን ፡ ለምን ።

43 ሌላውስ ፡ በሽታ ፡ ምንም ፡ አላለኝ ፤
—ደሞ ፡ አህያ ፡ ረግጦኝ ፡ ታምሜአለሁኝ ።

ሠ ፡ አህያ ፡ ረግጦኝ ፡ አሞኛል ፤ መራመድ ፡ አቅቶኛል ።

ወ ፡ ደሞ ፡ የሚባለው ፡ ሰው ፡ ዳንዴው ፡ ደብድቦኝ ፡ አሞኛል ።

44 ሌላ ፡ ዕቃ ፡ ከሰው ፡ ቤት ፡ ምን ፡ አስዋሳችሁ ፤
—በቤት ፡ ሙሉ ፡ እናንተ ፡ እያለ ፡ ዕቃችሁ ።

ሠ ፡ ቤት ፡ ሙሉ ፡ ዕቃ ፡ እያላችሁ ፡ ለምን ፡ ትዋሳላችሁ ፤ የሰው ፡ ገንዘብ ፡ ምን ፡ ያደርግላችኋል ።

ወ ፡ መላው ፡ ቤተ ፡ ሰቦቻችሁ ፡ አለቁ ፤ ምንም ፡ የተረፈ ፡ ሰው ፡ የለም ።

45 ልሠራለት ፡ ነበር ፡ ለወንድሜ ፡ ሸማ ፤
—ምን ፡ አደርጋለሁኝ ፡ ዐርብ ፡ ከጠፋማ ።

ሠ ፡ የሸማኔው ፡ ዕቃ ፡ መኑ ፡ ከጠፋ ፡ ምን ፡ ሊደረግ ፡ ይቻላል ።

ወ ፡ ዐርብ ፡ ቀን ፡ ሞተ ፤ በዚሁ ፡ ዕለት ፡ ዐረፈ ።

46 ልቅሶ ፡ ነበረብኝ ፡ ደርሼ ፡ መጣሁ ፤
—በጣም ፡ የተጐዳች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አየሁ ።

ሠ ፡ ሐዘንና ፡ ልቅሶ ፡ የበዛባት ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ አየሁ ።

ወ ፡ የተበደለ ፡ የተገፋ ፡ ሰው ፡ አንድም ፡ አላየሁ ።

47 ልብሳቸው ፡ ተቋጥሮ ፡ ሳይሠራላቸው ፡
—እየተጋለጡ ፡ ምታቱ ፡ ፈጃቸው ።

ሠ ፡ ምች ፡ ግርፋት ፡ አጠቃቸው ፤ ቀን ፡ ትኵሳት ፡ ንዳድ ፡ በዛባቸው ።

ወ ፡ ምታት ፡ ጣላቸው ፤ ተልከስካሽ ፡ ዞረባቸው ፤ ጥላ ፡ ወጊ ፡ አጠቃቸው ።

48 ልዕልት ፡ ማሕፀንቱን ፡ ትቶ ፡ በልጅነት ፡
—እንደ ፡ ምን ፡ ይሄዳል ፡ ፍታት ፡ በሌለበት ።

ሠ ፡ እንዴት ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ሚስቱን ፡ ትቶ ፡ ሳይፈታ ፡ ሰማኒያ ፡ ሳያወርድ ፡ ይጠፋል ።

ወ ፡ ልውል ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ ጸሎተ ፡ ፍትሐት ፡ በማይደረግበት ፡ በሕማማት ፡ ሰሞን ፡ ዐረፉ ፤ አሳዛኝ ፡ ሞት ፡ ሞቱ ።

49 ልዕልት ፡ ማሕፀንተ ፡ አምላክ ፡ ያስችልዎ ፤
—ፋሲካን ፡ የሚያኽል ፡ ቀረ ፡ በዓልዎ ።

ሠ ፡ በጣም ፡ ይናፈቅ ፡ የነበረ ፡ ፋሲካን ፡ የሚያኽል ፡ በዓልዎ ፡ ቀረ ፤ ሳይደሰቱበት ፡ አለፈ ።

ወ ፡ እንደ ፡ ፋሲካ ፡ ያስደስት ፡ የነበረ ፡ ባልዎ ፡ ዐረፈ ፤ አሳዛኝ ፡ የሆነ ፡ ሞትን ፡ ሞተ ፤ ባጭር ፡ ተቀጨ ።

50 ልዕልት ፡ ተናኘም ፡ ልንገርዎ ፡ ዜና ፤
የሐዘን ፡ ውሽንፍር ፡ ብርዱ ፡ በኛ ፡ ጸና ።

ይልቁን ፡ ለርስዎ ፡ ይስጥልን ፡ ጽናት ፤
—በተለይም ፡ ናቸው ፡ እትናት ፡ እትት ። (ተ ፡ ተ) ፡

ሠ ፡ ቀኑ ፡ በጣም ፡ በርዶ ፡ ውሽንፍር ፡ በዛበት ፤ ልዕልት ፡ ርስዎንም ፡ ሳይበርድዎት ፡ እትት ፡ ሳያሰኝዎት ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ በሞት ፡ የተለዩዎት ፡ እቴጌ ፡ ለርስዎ ፡ በተለይ ፡ እትዎም ፡ እናትዎም ፡ ነበሩ ፤ በመካከላችሁ ፡ ትልቅ ፡ መግባባትና ፡ መተዛዘን ፡ ነበር ።

51 ልዑል ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጥናዎ ፤
—በሞት ፡ ከተለዩት ፡ ወንድም ፡ እናትዎ ።

ሠ ፡ ልዑል ፡ በሞት ፡ ለተለዩት ፡ ወንድምዎ ፡ እግዚአብሐር ፡ ያጥናዎ ፤ ሐዘኑን ፡ ያስችልዎ ።

ወ ፡ የሞቱት ፡ ወንድምዎ ፡ እንደ ፡ እናት ፡ ነበሩ !

52 ልጅም ፡ ዐዋቂውም ፡ በጅህ ፡ የበላ ፡ ነው ፤
—ዐፈር ፡ ብላ ፡ ብሎ ፡ የረገመህ ፡ ማነው ።

ሠ ፡ «ዐፈር ፡ ብላ» ፡ ብሎ ፡ የረገመህ ፡ ወደ ፡ አምላክ ፡ ያሳቀለህ ፡ ማነው ፤ ሞትህን ፡ ጥፋትህን ፡ የተመኘው ፡ ማን ፡ ይሆን ።

ወ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ውረድ ፡ ዐፈር ፡ ሁን ፡ ያለህ ፡ ማነው ፤ አንተን ፡ ደጉን ፡ ምን ፡ አገኘህ ።

53 ልጄ ፡ በምሽቱ ፡ አትዠምር ፡ አዝመራ ፤
—በጊዜ ፡ ነው ፡ እኮ ፡ ሥራ ፡ የሚሠራ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ሥራ ፡ የሚከናወነው ፡ ቀን ፡ በብርሃን ፡ ነው ፤ ሌሊት ፡ ሥራ ፡ ለመሥራት ፡ አይቻልም ።

ወ ፡ ጕልበትና ፡ ሥልጣን ፡ ሳለህ ፡ ላገርህ ፡ ሥራ ፤ በጊዜህ ፡ ተጠቀምበት ፤ ሌት ፡ ተቀን ፡ ለወገንህ ፡ ድከም ።

54 ልጄን ፡ ፀሓይ ፡ መቶት ፡ በመንገዱ ፡ ላይ ፡
—ጠውልጓል ፡ ይላሉ ፤ ሰው ፡ እሸት ፡ ነወይ ።

ሠ ፡ ልጅህ ፡ ፀሐይ ፡ ሞቆት ፡ ጠውልጓል ፡ የሚሉኝ ፡ ሰው ፡ እንደእሸት ፡ በሐሩር ፡ የሚጠወልግ ፡ ማድረጋቸው ፡ ነውን ?
ወ ፡ ለካ ፡ የሰው ፡ መቆም ፡ ውሸት ፡ ነው ፤ ሕይወቱ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

55 ልጄ ፡ ጠርቶኝ ፡ ነበር ፡ በትንሽ ፡ ደግሶ ፤
—መና ፡ ገባሁ ፡ እንጂ ፡ አልተገኘም ፡ ፈርሶ ።

ሠ ፡ ጠላ ፡ ( ፈርሶ ) ፡ አልተገኘም ፤ በባዶ ፡ ቤት ፡ ገባሁ ።

ወ ፡ ልጄን ፡ ሞቶ ፡ አገኘሁት ፡ በከንቱ ፡ ደከምሁ ፡ በሕይወቱ ፡ ሳላገኘው ፡ ቀረሁ ።

56 ልጅዎን ፡ ይምከሩ ፡ እቴጌ ፡ መነን ፤

ልጅዎን ፡ ይቈጡ ፡ እቴጌ ፡ መነን ፤
—በጣም ፡ አስለቀሰው ፡ ትንሽ ፡ ትልቁን ። (መ ፡ ለ) ፡

ሠ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁን ፡ አጠቃው ፤ ሕፃን ፡ ሽማግሌውን ፡ አሳዘነው ፤ ሕዝ ቡን ፡ በደለው ።

ወ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ መላው ፡ ሕዝብ ፡ በሞቱ ፡ መሪር ፡ ሐዘን ፡ አደረገለት።

57 ልጅዋ ፡ እያለቀሰች ፡ ሰው ፡ አስቸግራለች ፤
—አሳብ ፡ የሌላት ፡ ሴት ፡ አዚያው ፡ ውላ ፡ አደረች ።

ሠ ፡ ኻያ ፡ አራት ፡ ሰዓት ፡ እዚያው ፡ ቈየች ፤ ቀኑንም ፡ ሌሊቱንም ፡ እዚ ያው ፡ አሳለፈችው ።

ወ ፡ ውላ ፡ ከሚባል ፡ ቦታ ፡ አዳር ፡ አደረገች ፤ ውል ፡ ተዋዋለች ፤ ስምም ነት ፡ አደረገች ፤ ቃል ፡ ገባች ።

58 ልጠይቀው ፡ ብሄድ ፡ ላስተዛዝነው ፡
—ዱር ፡ ለብሶ ፡ አሳለፈኝ ፡ ጐንደር ፡ ክፉ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ተሸሽጎ ፡ ተደብቆ ፡ ሣር ፡ ቅጠል ፡ ለብሶ ፡ አሳለፈኝ ።

ወ ፡ ደን ፡ ውድማ ፡ ለብሶ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆኖ ፡ የሚኖርበት ፡ ጠፍቶ ፡ አገኘሁት ።

59 ልጠይቅህ ፡ ላስታ ፡ እኔን ፡ ብትጠላ ፤
—ስለ ፡ ምን ፡ አረድኸው ፡ ጫጎን ፡ ሣር ፡ በበላ ። (1) ( ዘለ ፡ ቍ ፡ 1125 ) ፡

ሠ ፡ በምን ፡ ምክንያት፡ እንስሳውን፡ ጫጎን፡ አረድከው፤ ምን፡ አስቀየመህ።

ወ ፡ ስለምንህ ፡ ሳስጠነቅቅህ ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ አርደህ ፡ በልተህ ፡ ታስ ቈጣኛለህ ፤ ታስጨክነኛለህ ።

60 ሐምሌ፡ ድንጋይ፡ ይዟል፡ ነሐሴ፡ ሰይፍ፡ መዟል፡

መስከረም ፡ ጦር ፡ ይዟል ፡ ሰው ፡ ሊገሉላችሁ ፤
—አትገላግሉም ፡ ወይ ፡ ያላችሁ ፡ ያላችሁ ።

ሠ ፡ ከጠቡ ፡ ስፍራ ፡ የነበራችሁ ፡ አትገላግሉም ፡ ወይ ፤ ለምን ፡ ዝም ፡ ብላችሁ ፡ ታያላችሁ ።

ወ ፡ ሀብት ፡ ያላችሁ ፡ ሰጥታችሁ ፡ አበድራችሁ ፡ ነፍስ ፡ አታድኑም ፡ ወይ ፤ ለምን ፡ ዝም ፡ ብላችሁ ፡ ታያላችሁ ።

61 ሀያጅ ፡ ተሳፋሪ ፡ ሰዎች ፡ ከሆናችሁ ፡
—እረ ፡ ለመቼው ፡ ቀን ፡ ቤት ፡ ትሠራላችሁ ።

ሠ ፡ የማታድሩ ፡ የማትውሉ ፡ ከሆነ ፡ መቼ ፡ ልትቀመጡበት ፡ ቤት ፡ ትሠ ራላችሁ ።

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ጫጎ ፡ የሚባል ፡ ባንገቱ ፡ ቃጭል ፡ የተደረገለት ፡ አንድ ፡ በሬ ፡ ነበራቸው ፤ በየሄደበት ፡ ሁሉ ፡ ያገኘውን ፡ ይበላ ፡ ነበርና ፤ የላስታ ፡ ሕዝብ ፡ ደ ፍሮ ፡ አርዶ ፡ ስለ ፡ በላው ፡ ንጉሡ ፡ በመበሳጨት ፡ የተናገሩት ።

ወ ፡ ሞት ፡ የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ ድካሙ ፡ ሁሉ ፡ ከቶ ፡ ምን ፡ ዋጋ ፡ አለው ።

62 ሂደን ፡ ውለን ፡ ነበር ፡ ከዚያ ፡ አደባባይ ፤
—በደመና ፡ መጣን ፡ ፀሐይን ፡ ሳናይ ።

ሠ ፡ ደመና ፡ ከልሎን ፡ ፀሐይ ፡ ሳይመታን ፡ መጣን ፤ ሐሩር ፡ አላገኘንም ።
ወ ፡ ልዕልት ፡ ፀሐይ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴን ፡ ሳናገኝ ፡ በሐዘን ፡ ተመለስን ።

63 ሕመምተኛ ፡ እያለ ፡ ሰው ፡ እንዳይሸሻችሁ ፡
—ቀጥ ፡ ብላችሁ ፡ ቁሙ ፤ አተኙ ፡ ባልጋችሁ ።

ሠ ፡ አልጋችሁ ፡ ላይ ፡ አትዘረሩ ፤ አትጋደሙ ፤ መኝታ ፡ ይቅርባችሁ ።
ወ ፡ ሞልቃቃ ፡ አትሁኑ ፤ ብልግና ፡ ይቅርባችሁ ፤ በመንግሥታችሁ ፡ ባልጋችሁ ፡ አትለግሙ ።

64 መለስ ፡ ቀለስ ፡ ብላ ፡ አየችው ፡ ቀሚሷን ፤
—ረሳችውና ፡ ባፈር ፡ መለወሷን ።

ሠ ፡ ልብሷን ፡ ጭቃ ፡ ዐፈር ፡ እንደ፡ ነካባት ፡ አላወቀችውም ፤ አላየችውም።
ወ ፡ ከዐፈር ፡ መፈጠሯን ፡ ዘነጋችው ፤ ፈራሽ ፡ በሰባሽ ፡ መሆኗ ፡ አልታወሳትም ።

65 መልሰን ፡ አንሠራት ፡ ችሎታ ፡ የለን ፤
—መቅደሳችን ፡ ፈርሳ ፡ እናለቅሳለን ።

ሠ ፡ መቅደሳችን ፡ ፈርሳ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያናችን ፡ ተንዳ ፡ በማየታችን ፡ እናዝናለን ።
ወ ፡ መቅደሰ ፡ ወርቅ ፡ ዐፈር ፡ ሆነች ፤ ስለ ፡ ተለየችን ፡ እናለቅሳለን ።

66 መልሱን ፡ ስጡት ፡ እንጂ ፡ ለምን ፡ ዝም ፡ አላችሁ ፤
—ተጣርቶ ፡ ተጣርቶ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ሄደላችሁ ።  (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ሲጣራ ፡ ውሎ ፡ አቤት ፡ የሚለው ፡ የሚሰማው ፡ ሰው ፡ ስላጣ ፡ ተመለሰ ።
ወ ፡ ሰውየው ፡ ያለ ፡ የሌለውን ፡ ገንዘብ ፡ ጨርሶ ፡ ተቸግሮ ፡ በድኽነት ፡ ሞተ ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለየ ።

67 መልከ ፡ መልካም ፡ ሆነች ፡ እመት ፡ ነጻነት ፤
—ጠቅል ፡ ጠራርጎላት ፡ የፊቷን ፡ ጥላት ።

ሠ ፡ እፊቷ ፡ ላይ ፡ የነበረው ፡ ጥላት ፡ ተጠራርጎላት ፡ አምሮባታል ፤ ሰውነት ፡ አግኝታለች ።
ወ ፡ የቀድሞ ፡ ባለጋራዋን ፡ ጠቅል ፡ ፈጅቶላት ፡ ካገር ፡ አስወጥቶላት ፡ በነጻነት ፡ ትኖራለች ።

68 መልካሚቱ ፡ ቅጠል ፡ ያልነካት ፡ ፀሐይ ፡
—ያች ፡ አረግ ፡ ሬሳ ፡ መሆኗ ፡ ነወይ ።

ሠ ፡ ያች ፡ ቅጠል ፡ አረግ ፡ ሬሳ ፡ ናት ፤ ወይስ ፡ አይደለችም ።
ወ ፡ ያች ፡ አረግ ፡ የመሰለች ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ሴት ፡ ዐፈር ፡ ትቢያ ፡ መሆኗ ፡ ነውን ፤ ከቶ ፡ ሞት ፡ ላይቀርላት ፡ ነው ።

69 መልካም ፡ ሸጠን ፡ መጣን ፡ ዋጋ ፡ አወጡ ፡ ራስ ፤
—ለመኳንንቱ ፡ ብር ፡ ለወታደር ፡ ልብስ ።

ሠ ፡ ራስ ፡ ደኅና ፡ ዋጋ ፡ ሰጡ ፤ ሸቀጡን ፡ ከፍ ፡ ባለ ፡ ገንዘብ ፡ ገዙ ፤ እኛም ፡ በመልካም ፡ ስለ ፡ ሸጥን ፡ ደስ ፡ አለን ።
ወ ፡ ራስን ፡ አሳልፈን ፡ ሰጥተን ፡ ብርና ፡ ልብስ ፡ አገኘን ።

70 መልካም ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ ድልድል ፡ ተሰናድቶ ፡
—ማዘን ፡ ብቻ ፡ ጠፋ ፡ ሁሉ ፡ ተከማችቶ ።

ሠ ፡ የግድግዳ ፡ ማእዘን ፡ ታጣ ፤ ቋሚ ፡ ዕንጨት ፡ ጠፋ ።
ወ ፡ መተዛዘን ፡ መደጋገፍ ፡ መረዳዳት ፡ ቀረ ፤ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ የሚያስብ ፡ ጠፋ ።

71 መማሩንስ ፡ ዳዊት ፡ ዠምሬ ፡ ነበረ ፤
—ከአምላኬ ፡ ሳልደርስ ፡ ልቤ ፡ ሰንፎ ፡ ቀረ ።

ሠ ፡ አምላኬ ፡ ከሚባለው ፡ የዳዊት ፡ ምዕራፍ ፡ ሳልደርስ ፡ ቀረሁ ።
ወ ፡ ኀጢአተኛ ፡ ሆኜ ፡ ንስሓ ፡ ባለመግባቴ ፡ ከፈጣሪዬ ፡ ተለየሁ ።

72 መሠረቱን ፡ አይቶ ፡ ግንቡን ፡ የጐንደር ፡
—አስፋው ፡ አለ ፡ ጠቅል ፡ ሊያበላ ፡ ግብር ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ጠቅል ፡ ግብር ፡ ማብሊያው ፡ እንዳይጠበው ፡ አዳራሹን ፡ አሰፋው ፤ አንጣለለው ፤ በወዲያም ፡ በወዲህም ፡ ታዛ ፡ ጨመረበት ።
ወ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ ኃይሌ ፡ ልጁን ፡ «አስፋው» ፡ ብሎ ፡ ጠራው ፤ በስሙ ፡ ሥራውን ፡ መራ ፡ አስፋፋው ።

73 መሣሪያውን ፡ ጠምዶ ፡ እያረሰ ፡ ሰው ፡
—ባል ፡ አልነበረም ፡ ወይ ፡ ሚካኤል ፡ ምነው ።

ሠ ፡ ሰው ፡ የሚካኤል ፡ ለት ፡ ሲያርስ ፡ ሲቈፍር ፡ ዋለ ፤ በዓሉን ፡ ሻረ ።
ወ ፡ ፋሽስት ፡ የየካቲት ፡ ሚካኤል ፡ ለት ፡ በአካፋና ፡ በዶማ ፡ ጨፈጨፈን ፤ በእሳት ፡ አቃጠለን ፤ ትልቅ ፡ ግፍ ፡ ዋለብን ።

74 መሥራት ፡ አይችግርም ፡ ጕልበታሞች ፡ ካሉ ፡
—ዎ ፡ እያሉ ፡ መሄድ ፡ ነው ፡ እየተከተሉ ።

ሠ ፡ በሬን ፡ ውጣ ፡ ውረድ ፡ እያሉ ፡ ከፈሩ ፡ እንዳይዛባ ፡ እየተከላከሉ ፡ ማረስ ፡ ነው ።
ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ ብሎ ፡ አልቅሶ ፡ እየሸኙ ፡ ወዲያው ፡ እየተከታተሉ ፡ መሞት ፡ ነው ።

75　መስፍን ፡ የመስፍን ፡ ልብስ ፡ መልበስ ፡ ሲገባው ፡
—ትንሽ ፡ መጠቃቀም ፡ ነበረ ፡ ሥራው ።　　(ዳ ፡ ፋ) ፡

ሠ ፡ ሥራው ፡ ጨርቃጨርቁን ፡ መስፋት ፡ መጠቃቀም ፡ ነበር ።
ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ የተቸገረ ፡ መርዳት ፡ ያዘነ ፡ ማረጋጋት ፡ የሚወድ፡ ትልቅ ፡ ትንሹን ፡ ደጋፊ ፡ ነበር ።

76　መሪር ፡ ነው ፡ ሐዘኔ ፡ ከባድ ፡ ነው ፡ በውነት ፤
አባባ ፡ ትልቁ ፡ ይህ ፡ የርስዎ ፡ ሞት ፤
አባባዬ ፡ ሲያልፉ ፡ ቁሜ ፡ ያየሁት ፡
—የልጅ ፡ ልጅ ፡ ሆኜ ፡ ነው ፡ የተታለልኩት ። (ዘለ ፡ ቊ ፡ 942) ፡ (ሐ ፡ ወ ፡ ማ ፡ ሥ) ፡

ሠ ፡ የተታለልሁት ፡ ልጅነት ፡ ይዞኝ ፡ ነፍስ ፡ ባለማወቄ ፡ ነው ።
ወ ፡ በአያቴ ፡ ሞት ፡ በጣም ፡ አዘንኩ ፤ ሞታቸው ፡ አንዥቴን ፡ በላው ፤ አንገበገበኝ ፤ አስለቀሰኝ ።

77　መሬቱ ፡ በሙሉ ፡ በቅሎበታል ፡ ሙጃ ፤
—ዘሩን ፡ ዘርተን ፡ መጣን ፡ መብቀሉንም ፡ እንጃ ።

ሠ ፡ አሳርሰን ፡ ዘር ፡ በትነን ፡ መጣን ።
ወ ፡ «ዘር ፡ ይሁን» ፡ ሞቶ ፡ ከመቃብር ፡ ውለን ፡ ግብአተ ፡ መሬት ፡ አድር ሰን ፡ መጣን ።

78　መርጠሽ ፡ ከልጆችሽ ፡ ባስቀረሽላቸው ፤
—ሁለቱን ፡ አንድ ፡ ዘንድ ፡ ለምን ፡ ሰደድሻቸው ።

ሠ ፡ እናታቸው ፡ ሁለቱን ፡ ልጆቿን ፡ ለምን ፡ ላንድ ፡ ዐይነት ፡ መልክት ፡ አንድነት ፡ ሰደደቻቸው ።
ወ ፡ ሁለቱ ፡ ልጆቿ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሞቱ ፤ ሁለቱንም ፡ ባንድ ፡ ቀን ፡ ቀበ ረች ።

79　መርፌው ፡ አይሰበር ፡ ክሩ ፡ አይበጠስ ፤
—ጠቃሚ ፡ ነውና ፡ የሁሉንም ፡ ልብስ ።

ሠ ፡ መርፌና ፡ ክሩ ፡ ልብስ ፡ መስፊያ ፡ መጠቃቀሚያ ፡ ነው ።
ወ ፡ ደጋፊ ፡ ረዳት ፡ ሁሉንም ፡ እንደ ፡ ችግሩ ፡ የሚሸኝ ፡ ሰው ፡ ነበር ።

80　መስተዋት ፡ አልገዛ ፡ እጄ ፡ ባዶ ፡ ነው ፤
—በሰው ፡ መስተዋት ፡ ነው ፡ ፊቴን ፡ የማየው ።

ሠ ፡ ፊቴን ፡ የምመለከተው ፡ በተውሶ ፡ መስተዋት ፡ ነው ።
ወ ፡ መጠላቴንና ፡ ሁናቴዬን ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ አየዋለሁ ፤ ባቀባበላ ቸው ፡ እረዳዋለሁ ።

81　መሸ ፡ በሩን ፡ ዝጉት ፡ ከቀረ ፡ ልማዴ ፤
—ተከፍቶ ፡ ማደሩን ፡ አይወደውም ፡ ሆዴ ።

ሥ ፡ ቤቱ ፡ ክፍቱን ፡ ማደሩን ፡ አልወድም ፤ ሳይዘጋ ፡ መቅረቱን ፡ አልፈ ቅድም ።

ወ ፡ ተበድሎ ፡ አዝኖ ፡ መኖር ፡ አይሆንልኝም ፤ ተጨቍኖ ፡ መኖር ፡ አል ችልም ።

82 መሸ ፡ ያን ፡ ወንድሜን ፡ ሳልገናኘው ፤
—ሞት ፡ ቢሆን ፡ አይቀርም ፡ ቀጠሯችን ፡ ነው ።

ሥ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ በቀጠሮው ፡ አይቀርም ፤ መምጣት ፡ አለበት ።

ወ ፡ ሞት ፡ በተቀጠበችው ፡ ቀን ፡ በሰዓቱ ፡ ይመጣል ፤ አይቀርም ።

83 መቍጠሪያዎን ፡ ይዞ ፡ ቆሻል ፡ አሽከርዎ ፤
—ጌታዬ ፡ ይነሡ ፡ ጊዜ ፡ አለፈብዎ ።

ሥ ፡ የጸሎት ፡ ሰዓት ፡ አለፈ ፤ የምሕላ ፡ ማድረሻ ፡ ጊዜ፡ መተላለፉ ፡ ነውና፡ ይነሡ ።

ወ ፡ መልካም ፡ ዘመንዎ ፡ አለቀ ፤ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚያዩበት ፡ ሰዓት ፡ አለፈ ።

84 መቃብርን ፡ ድኻ ፡ አላችሁት ፡ ወይ ፤
—ይኸው ፡ ዛሬ ፡ ራሱን ፡ ችሎ ፡ የለም ፡ ወይ ።

ሥ ፡ ይኸው ፡ የሌላን ፡ ርዳታ ፡ ሳይጠይቅ ፡ ራሱን ፡ ደግፎና ፡ ችሎ ፡ ይኖር ፡ የለም ፡ ወይ ።

ወ ፡ ባለክብሩን ፡ የራስ ፡ ማዕርግ ፡ ያለውን ፡ ታላቅ ፡ ሰው ፡ መቃብር ፡ ይዞት ፡ የለም ፡ ወይ ።

85 መቅረቱ ፡ ታወቀ ፡ የድኻው ፡ አዝመራ ፤
—በዚህ ፡ በግንቦት ፡ ወር ፡ መኰንን ፡ ተዘራ ። (መ ፡ አ) ፡

ሥ ፡ መኰንን ፡ ካዘመረ ፡ ከዘራ ፡ አንቸገርም ፤ ያበድረናል ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ሞተ ፤ ፋንታውን ፡ ተወጣው ።

86 መቅደላ ፡ አፋፉ ፡ ላይ ፡ ጩኸት ፡ በረከተ ፤
—የሴቱን ፡ አናውቅም ፤ ወንድ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሞተ ።

ሥ ፡ ከወንዶች ፡ መካከል ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ ሞተ ፤ ብዙ ፡ ሰው ፡ አደጋ፡ አላገኘውም ።

ወ ፡ ወንዱ ፡ ጀግናው ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ እንደ ፡ አንድ ፡ ተራ ፡ ሰው ፡ መቅደላ ፡ ላይ ፡ ሞተ ።

87 መተማ ፡ እወርዳለሁ ፡ ክረምቱስ ፡ ከወጣ ፡
—ራብ ፡ ጠንቶብኛል ፡ ቀለቤን ፡ ላመጣ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 184 ፡ 267) ፡

ሥ ፡ የእኽል ፡ ቀለብ ፡ ለመሰፈር ፡ የወር ፡ አበል ፡ ለማምጣት ፡ መተማ ፡ እወርዳለሁ ።

ወ ፡ መተማ ፡ ላይ ፡ በጦርነት ፡ የሞተውን ፡ የልጄን ፡ የቀለቤን ፡ ዐፅም ፡ ሄጄ ፡ ላምጣ ።

88 መቼ ፡ ተዠመረ ፡ እንዲህ ፡ ያል ፡ ሥርዐት ፤
—መቅደስ ፡ ይገባል ፡ ወይ ፡ ያልተካነ ፡ ሞት ።

ሠ ፡ ክህነት ፡ የሌለው ፡ ሥልጣን ፡ ያልተቀበለ ፡ ሰው ፡ እመቅደስ ፡ ለመግ ባት ፡ ይችላል ፡ ወይ ።

ወ ፡ ሞት ፡ እንዴት ፡ ወይዘሮ ፡ መቅደሰን ፡ ሳይታሰብ ፡ ወሰዳት ።

89 መች ፡ አየሸውና ፡ አንችም ፡ እንደ ፡ ሌላ ፤
—የት ፡ አንዠት ፡ ይበላል ፡ እሸቴ ፡ ቀጸላ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 452) ፡

ሠ ፡ መቼ ፡ ያንዠት ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ፤ እሱን ፡ ለመብላት ፡ አይፈቅድም ።

ወ ፡ የሸቴ ፡ ሞት ፡ የእኅቱን ፡ አንዠት ፡ በላው ፤ ሐዘኑ ፡ አንገበገባት ።

90 መች ፡ እንዲህ ፡ ነበረ ፡ የቤታችን ፡ ለቅሶ ፤
—ባይወጣ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሰዉ ፡ ተጨርሶ ።

ሠ ፡ ሰዉ ፡ በሙሉ ፡ አልወጣም ፤ ጨርሶ ፡ አልከተተም ።

ወ ፡ ሰዎችን ፡ ወገናችን ፡ በሞት ፡ አልቋል ፤ የተረፈ ፡ የለም ።

91 መንኜ ፡ እሄዳለሁ ፡ ፈራሁኝ ፡ ኰነኔ ፤
—በድን ፡ አልፌ ፡ ነው ፡ የመጣሁት ፡ እኔ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 822) ፡

ሠ ፡ የሰውን ፡ ሬሳ ፡ እየተራመድሁ ፡ ነው ፡ የመጣሁት ።

ወ ፡ «ድን» ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ በኩል ፡ አልፌ ፡ ነው ፡ የመጣሁት ።

92 መንገሻ ፡ ለምን ፡ ነው ፡ ተገልጠው ፡ ያየዎ ፤
—አንኮበር ፡ እያለ ፡ ራስ ፡ ማሰሪያዎ ።

ሠ ፡ ራስዎን ፡ የሚሸፍኑበት ፡ ሻሽ ፡ እያለዎ ፡ ለምን ፡ ተጋለጡ ።

ወ ፡ የራሶች ፡ ማሰሪያ ፡ አንኮበር ፡ እያለ ፡ ለምንድነው ፡ ፊትዎን ፡ የሚ ያየው ።

93 መከራ ፡ ሲመጣ ፡ አይነግርም ፡ ዐዋጅ ፤
—ሲገሠግሥ ፡ አድሮ ፡ ቀን ፡ ይጥላል ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ ሌሊት ፡ ገሥግሦ ፡ ሄዶ ፡ ቀን ፡ አደጋ ፡ ይጥላል ፤ ሲነጋ ፡ ጠላትን ፡ ያ ጠቃል ።

ወ ፡ ሰውን ፡ ዘመን ፡ ያዋርደዋል ፤ ጊዜ ፡ ይጥለዋል ።

94 መኪና ፡ ነው ፡ አሉ ፡ አንተማ ፡ ንግድህ ፤
—እኔ ፡ እለብሰዋለሁ ፡ አንተ ፡ እየሰፋህ ።

ሠ ፡ ልብስ ፡ መስፋት ፡ መጥቀም ፡ ታውቃለህ ።

ወ ፡ ንብረትህ ፡ እየሰፋ ፡ እየዳበረ ፡ ይሂድ ፤ ሀብትህ ፡ ይብዛ ፡ ገንዘብህ ፡ ይበርክት ።

95 መካሪዬ ፡ በዛ ፡ ቤት ፡ ሥራ ፡ እሚለው ፤
—ምን ፡ ያታክተኛል ፡ አሁን ፡ ላፈርሰው ።

ሠ ፡ ላፈርሰው ፡ ምን ፡ አለፋኝ ፡ ብዬ ፡ ቤት ፡ መሥራቱን ፡ ተውሁት ፤ ያሰብሁት ፡ ሐሳብ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ሰው ፡ ዐፈር ፡ ለመሆን ፡ ለምን ፡ ተሠራ ፤ ፍጻሜው ፡ ይህ ፡ ከሆነ ፡ ለምን ፡ ተፈጠረ ።

96 መካን ፡ ይበዛዋል ፡ ሶርያ ፡ ሮምያ ፤
—ወላድ ፡ እጅግ ፡ አየሁ ፡ በኢትዮጵያ ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ በኢትዮጵያ ፡ ብዙ ፡ ወላድ ፡ ሴቶች ፡ አየሁ ።

ወ ፡ መውለድ ፡ ይሏችኋል ፡ እንደ ፡ ምኒልክን ፡ እናት ፡ እንደ ፡ እጅግ ፡ አየሁ ፡ ነው ።

97 መክተህ ፡ ጋሻህን ፡ ይዘህ ፡ ጣፋውን ፡
—አታድነውም ፡ ወይ ፡ አገር ፡ ራስህን ።

ሠ ፡ ተከላክለህ ፡ እጅህን ፡ እግርህን ፡ መላ ፡ ሰውነትህን ፡ አታድንም ፡ ወይ ።

ወ ፡ አገር ፡ ሆይ ፡ ራስህ ፡ ገዥህ ፡ ሲጠፋ ፡ ተራድተህ ፡ ጠላትህን ፡ አትመልስም ፡ ወይ ።

98 መኰንን ፡ መጻፊያህ ፡ ቀስተኒቻ ፡ ይሁን ፤
—መቃ ፡ ብር ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ ያጠፋል ፡ ቀለምህን ።

ሠ ፡ የመቃ ፡ ብር ፡ ጽፈትን ፡ ያጠፋል ፤ አያሳምርም ፤ ሥነ ፡ ጽሑፍን ፡ ያበላሻል ።

ወ ፡ በመቃብር ፤ ውስጥ ፡ መልክና ፡ ውበት ፡ ይጠፋል ፤ ሰውነት ፡ ይፈርሳል ፤ ይበሰብሳል ።

99 መኰንንስ ፡ ቢሆን ፡ ከቤቱ ፡ ባልወጣ ፤
—ንጉሥ ፡ የመሰለ ፡ ዘውድ ፡ የጫነ ፡ መጣ ። (1)

ሠ ፡ ዘውድ ፡ የተቀዳጀ ፡ አክሊል ፡ ያደረገ ፡ ሰው ፡ መጣ ።

ወ ፡ ራስ ፡ ዘውዴ ፡ ጦር ፡ አስከትቶ ፡ ታጥቆ ፡ ለውጊያ ፡ መጣ ።

100 መኰንንነቱን ፡ አናውቀውም ፡ እኛ ፤
—ለድኻ ፡ ብር ፡ አፍሳሽ ፡ ይኸን ፡ አንጥረኛ ።

ሠ ፡ የብር ፡ ጌጣጌጥ ፡ በመሥራት ፡ ድኻን ፡ የሚያገለግል ፡ ነበር ።

ወ ፡ ለድኻ ፡ ገንዘቡን ፡ የሚበትን ፡ ችግረኛን ፡ የሚጐበኝ ፡ ነበር ።

101 መኰንን ፡ ደከመው ፡ መጣበት ፡ እርጅና ፤
—መሬት ፡ ይዞ ፡ ሲቀር ፡ አይተነዋልና ። (ብ ፡ ወ ፡ ጊ ፡ ወ ፡ ዮ) ፡

---

(1) ለጦር ፡ የተዘጋጁ ፡ መሆናቸውን ፡ የሚገልጽ ፡ በረቀቀ ፡ ዘይቤ ፡ (አነጋገር) ፡ የተጻፈ ፡ ደብዳቤ ፡ ደጃች ፡ ዘውዴ ፡ ለራስ ፡ ጉግሳ ፡ በላኩ ፡ ጊዜ ፡ ሚስታቸው ፡ ወይዘሮ ፡ ድንቅነሽ ፡ የመልክቱን ፡ ፍሬ ፡ ነገር ፡ የገለጡበት ።

ሠ ፡ መኰንን ፡ አረጀ ፤ ዐቅም ፡ አነሰው ፤ መሬት ፡ ይዞ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ከመኪና ፡ ወድቆ ፡ አልተነሣም ፤ እዚያው፡ ሞቶ ፡ ቀረ ።

102 መኳንንቱ ፡ ሁሉ ፡ ተከናንቦ ፡ ተኛ ፤
—እያየ ፡ ሄደ ፡ አሉ ፡ እንዳለው ፡ ወሬኛ ። (1)

ሠ ፡ መኳንንቱ ፡ ሁሉ ፡ ተኝቶ ፡ ሳለ ፡ ተደብቆ ፡ የሄደው ፡ ወሬኛ ፡ የተናገረው ፡ እውነት ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ።

ወ ፡ እንደ ፡ ወሬኛ ፡ የሚባለው ፡ ዐይኑ ፡ ሳይጠፋ ፡ ቀረ ፡ አመለጠ ።

103 መኳንንቱ ፡ ሁሉ ፡ ወዴት ፡ ሄደዋል ፤
—ያውና ፡ ተከፍቶ ፡ ቤቱ ፡ ይታያል ።

ሠ ፡ ቤቱ ፡ አልተዘጋም ፤ ክፍት ፡ ሆኖ ፡ ይታያል ።

ወ ፡ መኳንንቱ ፡ ሁሉ ፡ አልቆ ፡ ቤተ ፡ መንግሥቱ ፡ ባዶ ፡ ሆኖ ፡ ሐዘን ፡ ሞልቶበት ፡ ይታያል ።

104 መወድስ ፡ ተቀኙ ፡ ካህናቶች ፡ በያምባው ፤
—መኰንን ፡ ነው ፡ ብለው ፡ ሥላሴ ፡ የገባው ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ)፡

ሠ ፡ ሥላሴ ፡ ቅኔ ፡ ይገባዋል ፤ መቍጠር ፡ መቀኘት ፡ ይችላል ።

ወ ፡ የልዑል ፡ መኰንን ፡ አስከሬን ፡ ከቅድስት ፡ ሥላሴ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ገብቶ ፡ ተቀመጠ ።

105 መድኀኒት ፡ ማር ፡ አይደል ፡ እንዴት ፡ ይጣፍጣል ፤
—ያሞት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ከሁሉ ፡ ይመራል ።

ሠ ፡ ያ ፡ ሐሞት ፡ ይመራል ፤ ይጐመዝዛል ፤ እንደ ፡ ማር ፡ አይጣፍጥም ።

ወ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ካለው ፡ አሰቃቂ ፡ ነገር ፡ ሁሉ ፡ እንደ ፡ ሞት ፡ መሪር ፡ ስሜት ፡ በኀሊና ፡ ላይ ፡ የሚፈጥርና ፡ የሚቀርጽ ፡ የለም ።

106 መድኀኒት ፡ ፈልጉ ፡ ሰዎች ፡ እባካችሁ ፤
—እናንተም ፡ እናንተም ፡ እናንተም ፡ ታማችሁ ።

ሠ ፡ ሁላችሁም ፡ ሕመምተኞች ፡ ናችሁ ፤ መድኀኒት ፡ ፈልጉ ።

ወ ፡ ሁላችሁም ፡ ታምታችኋል ፤ ተጠርጥራችኋል ፤ አልታመናችሁም ።

107 መድኀኒት ፡ ጠጥተው ፡ ቤት ፡ ውለዋል ፡ አሉ ፤
ላሽከሮቻቸውም ፡ ጠጅ ፡ ስጡ ፡ ይላሉ ፡
—ፊትም ፡ በብርሌ ፡ ኋላም ፡ በፍንጃሉ ።

ሠ ፡ ላሽከሮቻቸው ፡ ጠጁን ፡ በብርሌውም ፡ በፍንጃሉም ፡ እንዳሉት ፡ ባገኙት ፡ ዕቃ ፡ ናኙት ።

---

(1) ታላቁ ፡ ራስ ፡ ኀይሉ ፡ መኳንንቶቻቸውን ፡ ሜራ ፡ ሲያደርጉ ፡ አግኝተዋቸው ፡ ዐይናቸውን ፡ እያወለቁ ፡ በዋሻ ፡ እንዲታሰሩ ፡ ሲያደርጉ ፡ እንዳለ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ አምልጦ፡ ስለ ፡ ሄደ ፡ የተገጠመ ።

ወ ፡ በወህኒ ፡ ቤት ፡ በፍንጅ ፡ ታስረው ፡ ተቀምጠዋል ።

108 መገላገሉንስ ፡ ተገላግላ ፡ ነበር ፤
—ተመልሳ ፡ ከዳች ፡ ዕርቅ ፡ ያልፈጀው ፡ ነገር ።

ሠ ፡ ዕርቅ ፡ የሌለበት ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ያልተደረገበት ፡ ውል ፡ መፍረሱ ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ ሳትገላገል ፡ በወሊድ ፡ ዐረፈች ፤ ምጥ ፡ ገደላት ።

109 መጠንቀቅ ፡ ይገባል ፡ ለቤተ ፡ ክሲያን ፡ ዕቃ ፤
—ታሳዝነኛለች ፡ ዕጣኒቱ ፡ ወድቃ ።

ሠ ፡ ዕጣኗ ፡ ወድቃ ፡ አታንሣትምን ፤ ለምን ፡ ዝም ፡ ብለህ ፡ ትመለከታለህ ።

ወ ፡ ሕፃኒቱ ፡ ልጅ ፡ ሞተች ፤ ከዐፈር ፡ ተደባለቀች ።

110 መጠሙን ፡ ይጠማል ፡ ሁሉ ፡ ያዳም ፡ ልጅ ፤
—የጊዜውን ፡ መድረስ ፡ የሚያውቅ ፡ የለም ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ የጠም ፡ መግደፊያውን ፡ እኽል ፡ ውሃ ፡ መቅመሻውን ፡ ሰዓት ፡ የሚያውቅ ፡ ሰው ፡ የለም ።

ወ ፡ ጊዜ ፡ ሞቱን ፡ መረዳት ፡ የሚችል ፡ ፍጡር ፡ የለም ፤ ዛሬ ፡ ወይም ፡ ነገ ፡ ይምጣ ፡ አናውቅም ።

111 መጫወቱን ፡ ትተህ ፡ ቆመህ ፡ ከመንገድ ፡
—ተማር ፡ ይልቅ ፡ አንተ ፡ እንድትወደድ ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ እንድትከበር ፡ እንድትወደድ ፡ ብትፈልግ ፡ በትምህርት ፡ በርታ ፤ በዕውቀት ፡ የጐለመስክ ፡ ሁን ።

ወ ፡ ተማር ፡ የበለጥህ ፡ ጣፋጭ ፡ ነህ ፤ ከጣፋጭ ፡ ነገሮች ፡ ሁሉ ፡ ትመረጣለህ ።

112 ሚ ፡ መጠን ፡ ሳይባል ፡ የመጣሁ ፡ ቀድሜ ፤
—ሥጋውና ፡ ደሙ ፡ አለቀብኝ ፡ ቆሜ ።

ሠ ፡ ሥጋና ፡ ደሙን ፡ ለመቀበል ፡ መጥቼ ፡ ሳላገኝ ፡ ቆሜ ፡ ቆሜ ፡ ተመለስኩ ።

ወ ፡ የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ ወደሙ ፡ ሳልቀበል ፡ ዕድሜዬ ፡ አለቀ ፤ ጊዜ ፡ ሞቴ ፡ መጣ ።

113 ሚስትም ፡ አላገባ ፡ አሊዝም ፡ ንብረት ፤
—እንግዲህ ፡ የት ፡ ላገኝ ፡ የባላገር ፡ ሴት ። (1)

(1) በልጅነቱ ፡ ወራት ፡ ሥራ ፡ የማይወድ ፡ በቅልውጥ ፡ ያደገ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ነበር ፤ እግዚአብሔር ፡ ሳይደግስ ፡ አይጣላምና ፡ አንዲት ፡ ጠንካራ ፡ የሆነች ፡ ሚስት ፡ አጋጥሞት ፡ በኑሮው ፡ እየደገፈችው ፡ ስትኖር ፡ ይህች ፡ ሴት ፡ በድንገት ፡ በሞት ፡ ተለየችው ፤ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ እሷን ፡ የመሰለች ፡ የማያገኝ ፡ መሆኑን ፡ በማወቅና ፡ ተስፋ ፡ በመቍረጥ ፡ የገጠመው ።

ሠ ፡ ከተማ ፡ ያላወቀች ፡ የባላገር ፡ ሴት ፡ እንግዲህ ፡ ወዴት ፡ ላግኝ ።
ወ ፡ ያገሬ ፡ የወንዜ ፡ የባላባት ፡ ልጅ ፡ የሆነች ፡ ትልቅ ፡ ወገን ፡ ያላት ፡ ሴት ፡ ከወዴት ፡ አገኛለሁ ።

114　ሚዶና ፡ መስተዋት ፡ ይስጡኝ ፡ የኵል ፡ ቀለም ፤
—እንዳንች ፡ ያል ፡ ወይዘሮ ፡ ቶሎ ፡ አይተውም ፡ ዓለም ።

ሠ ፡ እንዳንች ፡ ያለ ፡ ቈንጆ ፡ ዓለምን ፡ አይንቅም ፤ መመነን ፡ አይችልም ፤
ወ ፡ እንዳንች ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ በልጅነት ፡ መሞት ፡ አይገባውም ፡ ነበር ፤ ወየው ፡ ወየው ፡ በወጣትነትሽ ፡ ሞትሽ ።

115　ማለቁን ፡ ዐውቃለሁ ፤ አንችም ፡ ነግረሽኛል ፤
—ቀድሞ ፡ አንችው ፡ ቅመሽው ፡ ለኔም ፡ ይበቃኛል ። (አ ፡ ገ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ቅመሽው ፤ የምግቡን ፡ ጣዕም ፡ በምላስ ፡ አጣጥመሽ ፡ ለማወቅ ፡ ሞክሪ ።
ወ ፡ አስቀድሞ ፡ አንችው ፡ ራስሽ ፡ ቅመሽ ፡ ጨርሰሽዋል ።

116　ማረጌ ፡ ከቀረ ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ እሻለሁ ፤
—አልፈልግም ፡ ዓለም ፡ መንኜ ፡ እሄዳለሁ ።

ሠ ፡ ክብሬ ፡ ከጐደለ ፡ ከሥልጣን ፡ ከታገድኩ ፡ መኖር ፡ አልመኝም ።
ወ ፡ ማዕርጌ ፡ የሚባለው ፡ ከሞተ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ አልኖርም ፤ እመንናለሁ ።

117　ማረፊያዬን ፡ አላውቅ ፡ ተጕገጬ ፡ ተጕገጬ ፤
—እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ እንዲህ ፡ ተወዝውዤ ።

ሠ ፡ የምደርስበትን ፡ ቦታ ፡ አላውቅም ፤ ሄጄ ፡ ሄጄ ፡ የማርፍበት ፡ የት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አልተረዳሁትም ።
ወ ፡ የመሞቻዬን ፡ ሰዓት ፡ አላውቀውም ፤ ጊዜ ፡ ሞቴን ፡ ለመረዳት ፡ አልቻልሁም ።

118　ማር ፡ ቀምሼ ፡ አላውቅም ፡ እኔ ፡ ወንድማችሁ ፤
—ያገሬ ፡ ወጣቶች ፡ ተማሩ ፡ እባካችሁ ።　(ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ እባካችሁ ፡ ከማሩ ፡ ስጡኝ ፤ ከወለላው ፡ አቅምሱኝ ።
ወ ፡ ትምህርትን ፡ ዕውቀትን ፡ አስፋፉ ፤ ጥበብን ፡ ጠንክራችሁ ፡ ተማሩ ።

119　ማር ፡ እሸት ፡ ተቈርጦ ፡ ቀርቦ ፡ በገበታ ፤
—ሰፈፍ ፡ የለውም ፡ ወይ ፡ ላሽከሮቹ ፡ ጌታ ።

ሠ ፡ ከዳ ፡ ገጋ ፡ የማይገኝበት ፡ ንጹሕ ፡ ወለላ ፡ ማር ፡ ነውን ።
ወ ፡ ጌታቸው ፡ አሽከሮቹን ፡ ቅር ፡ የማያሰኝ ፡ እንከን ፡ የሌለው ፡ ደግ ፡ ነወይ ።

120　ማሽላና ፡ ስንዴ ፡ ባንድ ፡ አብረን ፡ ስንቈላ ፡
—እያረረ ፡ ሣቀ ፡ የባሕር ፡ ማሽላ ።　(ዮ ፡ ን) ፡

ሠ ፡ ማሽላ ፡ ሲቈሉት ፡ ይፈካል ።

ወ ፡ ጠላት ፡ ውስጥ ፡ ውስጡን ፡ እያረረ ፡ እየተናደደ ፡ ላይ ፡ ላዩን ፡ ይሥቃል ፤ ደስ ፡ ያለው ፡ ይመስላል ።

121 ማታ ፡ ዘነበና ፡ ፀሓይ ፡ ጠልቃብን ፡
—መኰንን ፡ ማለፊያው ፡ መልካችን ፡ ጠፋን ።

ሠ ፡ መሸጋገሪያው ፡ መልካው ፡ ጠፋብን ።

ወ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የምናይበት ፡ ጌታችን ፡ መኰንን ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ሞተ ፤ ከፊታችን ፡ ጠፋ ።

122 ማዘን ፡ ከፍ ፡ አርጋችሁ ፡ ቈርቈሮ ፡ ቤት ፡ ሥሩ ፤
—ወትሮ ፡ የምናውቀው ፡ አለቀ ፡ ያሣሩ ።

ሠ ፡ ለቤት ፡ ክዳን ፡ የሚሆነው ፡ ሰንበሌጥ ፡ አለቀ ።

ወ ፡ የመከራው ፡ ጊዜ ፡ አለፈ ፤ የጭንቁ ፡ ዘመን ፡ ተወገደ ።

123 ማዘን ፡ ይገባናል ፡ ስለ ፡ ዐፄ ፡ በካፋ ፤
—ዘውዱ ፡ ተማረከ ፡ ራስ ፡ ወርቁም ፡ ጠፋ ።

ሠ ፡ የማዕርግ ፡ ልብሱ ፡ ዘውዱ ፡ ራስ ፡ ወርቁ ፡ በሙሉ ፡ ተዘረፈ ።

ወ ፡ ሁለቱ ፡ መኳንንት ፡ ዘውዱና ፡ ወርቁ ፡ እጃቸውን ፡ ሰጡ ፤ ጦሩ ፡ ተፈታ ።

124 ማዱ ፡ ሳይነሣ ፡ ሂዱ ፡ ሳይሏችሁ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ መጣችሁ ፤
—ስብሐት ፡ ቢቀር ፡ ደግ ፡ ነው ፡ ብላችሁ ።

ሠ ፡ ስብሐት ፡ ለአብ ፡ የሚባለው ፡ ጸሎት ፡ እንዲደርስ ፡ አልፈቀዳችሁም ፤ ቢቀር ፡ ቢታጐል ፡ ወዳችኋል ።

ወ ፡ አለቃ ፡ ስብሐት ፡ ደግ ፡ ቸር ፡ ለጋስ ፡ ነው ፡ አላችሁ ።

125 ማድጋውን ፡ ሁሉ ፡ ታስቈጥራላችሁ ፤
—አለቃችሁ ፡ እንጂ ፡ ማን ፡ ወሰደባችሁ ።

ሠ ፡ ዕቃችሁ ፡ አለ ፤ አልተነካባችሁም ፤ አልተዘረፋችሁም ።

ወ ፡ አልቃችኋል ፤ ዘር ፡ አልተረፋችሁም ፤ የዘመድ ፡ ድኻ ፡ ሆናችኋል ።

126 ምሳ ፡ ሳያበሉ ፡ ጦም ፡ አውለውን ፡
—ዐይብ ፡ በእንቅብ ፡ ሰጡን ፡ እራታችንን ።

ሠ ፡ ዐይብ ፡ ለምግብ ፡ በእንቅብ ፡ ሙሉ ፡ አቀረቡልን ፤ እጅ ፡ እጅ ፡ እስኪለን ፡ አበሉን ።

ወ ፡ ዐይብ ፡ በእንቅብ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ እራት ፡ በላን ፤ ተጋበዝን ።

127 ምነው ፡ ሽልማቱን ፡ ለሰው ፡ መስጠትዎ ፡
—እያለ ፡ ዱባለ ፡ የለፋ ፡ አሽከርዎ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ የደከመ ፡ በቅንነት ፡ ያገለገለ ፡ የለፋ ፡ አሽከርዎ ፡ እያለ ፤ ለምንድ ነው ፡ ሽልማቱን ፡ ለሌላ ፡ ሰው ፡ የሰጡት ።

ወ ፡ አሽከርዎ ፡ ዱባለ ፡ ተደበደበ ፤ ለፋ ፤ ተረገጠ ።

128 ምነው ፡ አንኮበሮች ፡ እንዲህ ፡ ተሳሳቱ ፡
—ጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ዐፈር ፡ ውስጥ ፡ ወስደው ፡ የከተቱ ።

ሠ ፡ ንጹሕ ፡ ወርቅ ፡ ዐፈር ፡ ውስጥ ፡ መቅበር ፡ ተገቢ ፡ አይደለም ፤ ሞኝ ነት ፡ ነው ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ጥሩ ፡ ወርቅ ፡ ሞተች ፤ ተቀበረች ።

129 ምነው ፡ አይመጣልኝ ፡ የፈረሱ ፡ ምስል ፤
ምነው ፡ አይመጣልኝ ፡ የጐራዴው ፡ ምስል ፤
ምነው ፡ አይመጣልኝ ፡ የጠመንዣው ፡ ምስል ፤
—የዚህ ፡ ቤት ፡ ከዚያ ፡ ቤት ፡ የሚቀር ፡ ይመስል ። (1)

ሠ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ከጎረ ፡ ቤት ፡ ሳይወያይ ፡ ሳይነጋገር ፡ መቼ ፡ ይቀራል ።

ወ ፡ እዚህ ፡ ቤት ፡ የመጣ ፡ ሞት ፡ ከዚያም ፡ ቤት ፡ መግባቱ ፡ ይቀራልን ።

130 ምነው ፡ ያዬ ፡ አሽከሮች ፡ ሲያለቅሱ ፡ ያመሹ ፡
—አቡን ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ የገደለው ፡ ጐሹ ። (2) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 137) ፡

ሠ ፡ የገደለው ፡ አቡኑን ፡ እኮ ፡ ነው ፤ የሞተው ፡ ጳጳስ ፡ አይመስላችሁምን ።

ወ ፡ ጀግንነቱን ፡ ያስመሰከረው ፡ መራውን ፡ የተወጣው ፡ «አቡና» ፡ ከሚ ባለው ፡ ቦታ ፡ እኮ ፡ ነው ።

131 ምነው ፡ ጎረ ፡ ቤቴ ፡ ፍሪዳ ፡ አረድክብኝ ፡
—የተዚህ ፡ ቀደሙ ፡ ሥጋ ፡ ዕዳ ፡ እያለብኝ ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ የተገዛበት ፡ ገንዘብ ፡ አለብኝ ፤ የቅርጫ ፡ ዕዳ ፡ ሒሳብ ፡ አልከ ፈልሁም ።

ወ ፡ የሥጋ ፡ ፍዳ ፡ ይጠብቀኛል ፤ በሰማይ ፡ ቤት ፡ መሠቃየት ፡ ይኖር ብኝ ፡ ይሆናል ።

132 ምነው ፡ ግፍ ፡ አይፈራ ፡ አይጠጠት ፡ ሞት ፡
—ልጆቿን ፡ አስታቅፎ ፡ ፈቶ ፡ ሲሰዳት ።

ሠ ፡ ሞት ፡ ግፈኛ ፡ ነው ፤ ቤት ፡ ሙሉ ፡ የወለደችውን ፡ ሚስቱን ፡ ፈቶ ፡ ልጆቿን ፡ አስታቅፎ ፡ አበረራት ፤ ባዶ ፡ እጅዋን ፡ ሰደዳት ።

ወ ፡ የልጆች ፡ እናት ፡ የነበረችው ፡ ዐረፈች ፤ ሕፃናቶቿን ፡ በትና ፡ ሄደች ፤ አሳዛኝ ፡ ሞት ፡ አገኛት ።

---

(1) ራስ ፡ በዛብህ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ከራስ ፡ ሚካኤል ፡ የተወለዱትን ፡ ያዬ ፡ ምኒልክን ፡ የልጅ ፡ ልጅ ፡ ወይዘሮ ፡ ዘነበ ፡ ወርቅን ፡ አግብተው ፡ ጐዣምን ፡ ሲገዙ ፡ ሳለ ፡ ተከ ሰው ፡ አፍቀራ ፡ ላይ ፡ በግዞት ፡ ስለ ፡ ሞቱና ፡ እንደ ፡ ማዕርጋቸው ፡ እንደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ልማድ ፡ ጌጡ ፡ ወጥቶ ፡ ባለመለቀሱ ፡ እናታቸው ፡ ያለቀሱት ።

(2) የደጃች ፡ ዘውዴ ፡ ልጅ ፡ ደጃች ፡ ጐሹ ፡ አቡና ፡ በሚባል ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ጦርነት ፡ አድ ርገው ፡ ብዙ ፡ አረመኔ ፡ ስለ ፡ ፈጁ ፡ የተገጠመ ።

133 ምነዋ ፡ ተኰሰኝ ፡ ጣይቱ ፡ ገላሽ ፤
እንዴት ፡ ነደሽ ፡ ይሆን ፡ ዐድዋ ፡ ላይ ፡ ላየሽ ፤
—እኔም ፡ በጣም ፡ ሞቀኝ ፡ አጥብቀሽ ፡ ተኰሽ ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ጣይዋ ፡ ገረረች ፤ በጣም ፡ ሞቀች ፤ አተኰሰች ።

ወ ፡ ስመ ፡ ጥሩዋ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ በዐድዋ ፡ ጦርነት ፡ ታላቅ ፡ ዠብዱ ፡ ሠራች ፤ መልካም ፡ ስምን ፡ ለሀገር ፡ አተረፈች ፤ ሰራዊቱን ፡ አበረታ ታች ፤ አዋጋች ።

134 ምነዋ ፡ ጐዣሜ ፡ ባሌን ፡ ጥሎ ፡ መጣ ፡ ትለኛለህ ፡ አሉ ፤
—ምንትዋብ ፡ አዳልን ፡ ምነው ፡ እኔ ፡ ሁሉ ። (1)

ሠ ፡ ምነው ፡ ሁሉም ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ ብቻ ፡ መውደቁ ።

ወ ፡ ምነው ፡ ታሙኛላችሁ ፡ እኔስ ፡ ልጄን ፡ ምንትዋብ ፡ አዳልን ፡ አጥቼ ፡ የለምን ?

135 ምኒልክ ፡ መኋዙን ፡ የምትጠይቁኝ ፡
—ፊትም ፡ አላለፈ ፡ ኋላም ፡ አይገኝ ።

ሠ ፡ ቀድሞም ፡ አልሄደ ፤ ከወደ ፡ ኋላም ፡ አይመጣም ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ አ ላለፈ ።

ወ ፡ ዐፄ ፡ ምኒልክን ፡ የሚያኽል ፡ ንጉሥ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አልነበረም ።

136 ምኒልክ ፡ ተክላችን ፡ ወዴት ፡ ጠፋ ፡ ካገር ፡
—ሸዋ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ታይቶባቸው ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ሸዋና ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ አትክልት ፡ ለምቶ ፡ አብቦ ፡ ታይቶ ፡ ነበር ፤ የመፀው ፡ አበባ ፡ ሞልቶባቸው ፡ ነበር ።

ወ ፡ ዐፄ ፡ ምኒልክ ፡ ባዲስ ፡ አበባ ፡ ሾመው ፡ ሸልመው ፡ ተፈርተው ፡ ይኖሩ ፡ ነበር ።

137 ምናምኑ ፡ ሁሉ ፡ የለከፈውን ፡
—አቡን ፡ አስባረከው ፡ ጐሹ ፡ ጋሻውን ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 130) ፡

ሠ ፡ አቡን ፡ እንዲባርከው ፡ አደረገ ፤ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ አስጠራበት ፤ በመስቀል ፡ አስዳሰሰው ።

ወ ፡ አቡና ፡ ላይ ፡ ጋሻውን ፡ ሠራበት ፤ ወንድነቱን ፡ ገለጠበት ።

138 ምንም ፡ ምን ፡ ሳይበድል ፡ ሳይናገር ፡ ሰው ፡
—ሰደቡት ፡ ይላሉ ፡ ዘርፋፋ ፡ ብለው ።

ሠ ፡ ጐታታ ፡ ዝርክርክ ፡ አሏቸው ።

ወ ፡ ዘር ፡ ወጣልን ፤ አስተዋይ ፡ ንጉሥ ፡ ነገሠልን ፡ ዘራችን ፡ ፋፋ ፡ ይላሉ።

---

(1) የጐዣም ፡ ሕዝብ ፡ ዘመዶቻችንን ፡ ከሰው ፡ አገር ፡ ወስዶ ፡ ፈጀብን ፡ እያሉ ፡ ቢያሻ ቸው ፡ ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ምነዋ ፡ እኔስ ፡ ልጄን ፡ ምንትዋብ ፡ አዳልን ፡ ገ ብሬ ፡ የለምን ፡ ብለው ፡ የተሰማቸውን ፡ መሪር ፡ ሐዘን ፡ የገለጹበት ።

139　ምንም ፡ ሳይቸግረው ፡ ተቀምጦ ፡ በተድላ ፡
—እንዴት ፡ ሲሮጥ ፡ ሄዶ ፡ ይሞታል ፡ በዱላ ።

ሠ ፡ ሳይቸግረው ፡ ሄዶ ፡ እንዴት ፡ በሽመል ፡ በቈመጥ ፡ ተደብድቦ ፡ ይሞ ታል ።

ወ ፡ እንዴት ፡ ሳይቸግረው ፡ «ዱላ» ፡ ከሚባል ፡ አገር ፡ ሄዶ ፡ ይሞታል ።

140　ምንም ፡ ቢደግፉት ፡ ቢይዙት ፡ በባላ ፡
—ከዘመመ ፡ ወዲህ ፡ ቤት ፡ የለውም ፡ መላ ።

ሠ ፡ ቤት ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ከዘመመ ፡ ወዲያ ፡ በባላ ፡ ቢይዙት ፡ ቢደግፉት ፡ ተመልሶ ፡ ይወድቃል ፤ አይቀናም ፤ ውሎ ፡ አድሮ ፡ መውደቁ ፡ አይ ቀርም ።

ወ ፡ ቀን ፡ ከጐደለ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ እግዚአብሔር ፡ ከጣለ ፡ የሚደረገው ፡ ጥረት ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ነው ፤ የተቀጠበውን ፡ ነገር ፡ መመለስ ፡ አይ ቻልም ።

141　ምንም ፡ ባንቀበር ፡ ባንገባ ፡ መሬት ፡
—አያሳፍረንም ፡ የለንም ፡ ማለት ።

ሠ ፡ አለን ፡ ብለን ፡ አንተማመንም ፤ ማታ ፡ ታይተን ፡ ጧት ፡ ጠፊዎች ፡ ነን ።

ወ ፡ አጥተናል ፡ ደኽይተናል ፡ ብንል ፡ አያሳፍረንም ፤ በማጣታችን ፡ አንሰቀቅም ።

142　ምንም ፡ ብንጐመዥ ፡ ለመቍረጥ ፡ ብንጓጓ ፡
እንዴት ፡ ይጣፍጣል ፡ ያለአዋዜ ፡ ሥጋ ።　(ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ያለአዋዜ ፡ አይጣፍጥም ፤ ያለድቍስ ፡ አይበላም ፤ አፍርንጅ ፡ ያስፈልገዋል ።

ወ ፡ ጠላት ፡ አልዋዜን ፡ መግደል ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ፤ በጣም ፡ ያጓጓል ።

143　ምንም ፡ እኽል ፡ ጠፍቶ ፡ ቍራሽ ፡ ቢቸግር ፡
—ራስ ፡ በሰው ፡ ግብር ፡ አይደርሱም ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ግብር ፡ አይበሉም ፤ ግብዣ ፡ አይወዱም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ደጉ ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ በሰው ፡ ነገር ፡ መግባትና ፡ ማሳዘን ፡ አይወ ዱም ፡ ነበር ።

144　ምንም ፡ ደስ ፡ ቢልህ ፡ ለጊዜው ፡ አሁን ፡
—ወንድሜ ፡ እንዳትረሳው ፡ መረገጥህን ።

ሠ ፡ መደብደብህን ፡ መመታትህን ፡ አስታውስ ።

ወ ፡ ሞተህ ፡ በመቃብር ፡ በእግር ፡ መጠቅጠቅህን ፡ መረምረምህን ፡ ተገንዘብ ።

145 ምን ፡ ይጠጣ ፡ ይሆን ፡ የነገው ፡ እንግዳ ፡
ጠጁ ፡ በየፊቱ ፡ ጨርሶ ፡ ተቀዳ ።

ሠ ፡ ጠጁ ፡ በየገበታው ፡ በየማእዱ ፡ ተቀዳ ፡ ታደለ ፤ በየመሶቡ ፡ ተሰጠ ።
ወ ፡ ጠጅ ፡ አጠጪ ፡ ጌታ ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ሕዝቡ ፡ እንባ ፡ በንባ ፡ ተራጨ ።

146 ምን ፡ ቸግሯችኋል ፡ ዕድሉ ፡ ቢ.ቃና ፡
—ነጋሪ ፡ ታለው ፡ ሰው ፡ አይጐዳምና ።

ሠ ፡ የሚነግርለት ፡ የሚያስታውስለት ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ አይጐዳም ፤ ቶሎ ፡ ጉዳዩ ፡ ይፈጸምለታል ።
ወ ፡ ስፊ ፡ ግዛት ፡ ያለው ፡ ባለነጋሪት ፡ ጌታ ፡ አይቸገርም ፤ ሀብታም ፡ ከሆነ ፡ የተመኘውን ፡ ያገኛል ።

147 —ምን ፡ አረግ ፡ ብለህ ፡ ነው ፡ ተቀጥፋ ፡ እያየሃት ፡
—አጐበሩን ፡ ሠርተህ ፡ ያውተረተርህላት ።
ሠ ፡ ተቀጥፋ ፡ እያየሃት ፡ አጐበር ፡ መሥራትህ ፡ ለምንድነው ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ትችላለህ ፡ ማጽደቅ ፡ ይሆንልሃልን ?
ወ ፡ ሐረግ ፡ የመሰለችው ፡ ቈንጆ ፡ በሞት ፡ ተቀጠፈች ፤ ደመወዜ ፡ በወጣትነቷ ፡ ዐረፈች ።

148 —ምንዳዬ ፡ ቈየብኝ ፡ እያለች ፡ ስታዋይ ፡ ለሰው ፡
—አገር ፡ ጥላ ፡ ሄደች ፡ ሳትቀበለው ። (1) (አ ፡ ተ ፡ ሚ ፡ )

1 ሠ ፡ ቀለቤ ፡ ዘገየብኝ ፤ የእኽል ፡ አበሌ ፡ አልተሰጠኝም ፤ ደመወዜ ፡ ቈየ ።
ወ ፡ ምንዳዬ ፡ የሚባለው ፡ ከሄደበት ፡ አገር ፡ ሳይመጣ ፡ ቈየ ፤ ዘገየብኝ ።
2 ሠ ፡ የጠየቀችውን ፡ ሳታገኝ ፡ ካገር ፡ ወጥታ ፡ ርቃ ፡ ሄደች ።
ወ ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ያለ ፡ የምትናፍቀውን ፡ ልጅዋን ፡ ሳትቀበለው ፡ ሳታየው ፡ ዐረፈች ።

149 ምንኛ ፡ መሰለ ፡ አዳል ፡ ሰዎቹን ፤
—ጦር ፡ ሲሠራ ፡ ብሩን ፡ ሊወጋ ፡ ጐሹን ። (2)

ሠ ፡ ጐሽ ፡ ሊገድል ፡ ጦር ፡ ከብር ፡ ሠራ ።
ወ ፡ ብሩ ፡ ደጃች ፡ ጐሹን ፡ ሊወጋ ፡ ጦር ፡ ያዘጋጃል ።

150 ምንኛ ፡ ረዘመ ፡ የኔማ ፡ ቁመት ፡
—ባጥ ፡ አያስገባኝም ፡ እዚያም ፡ ቤት ፡ እዚያም ፡ ቤት ።

ሠ ፡ ቁመቴ ፡ በመርዘሙ ፡ ጣራው ፡ በማጠሩ ፡ በር ፡ አላስገባም ፡ አለኝ ።
ወ ፡ ባጣ ፡ ብቸገር ፡ የሚያስጠጋኝ ፡ የሚረዳኝ ፡ አጣሁ ፤ እጄን ፡ የሚዘረጋልኝ ፡ አላገኘሁም ።

---

(1) ያዛኸ ፡ ተረፈ ፡ ወልደ ፡ ገብርኤል ፡ ባለቤት ፡ ወይዘሮ ፡ መርዓት ፡ ሥላሴ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ ልጃቸው ፡ ምንዳዬ ፡ የሚባለው ፡ ለትምርት ፡ አሜሪካ ፡ አገር ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ እንደ ፡ ናፈቁት ፡ ሳያዩት ፡ ስለ ፡ ሞቱ ፡ የተገጠመ ።

(2) ራስ ፡ አዳል ፡ በጦር ፡ ብልኀትም ፡ ሆነ ፡ በጀግንነት ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ የነበሩትን ፡ ደጃች ፡ ጐሹንና ፡ ደጃች ፡ ብሩን ፡ መስለው ፡ ስለ ፡ ተገኙ ፡ የተገጠመ ።

151 ምን ፡ ዝም ፡ ያሰኘዋል ፡ እያለ ፡ ንጉሡ ፡
—ቈማጣ ፡ አሉኝ ፡ ብሎ ፡ አይከስም ፡ ወይ ፡ እሱ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 1099 ) ፡

ሠ ፡ ቈማጣ ፡ ተባልኩ ፡ የሌለብኝን ፡ ተሰደብኩ ፡ ብሎ ፡ ለምን ፡ አልከሰሰም ።

ወ ፡ «ቆማ» ፡ ከሚባል ፡ አገር ፡ በግዞት ፡ አስቀመጡኝ ፤ ረሱኝ ።

152 ምን ፡ ያለ ፡ ነሐሴ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡
—በረደን ፡ ብንለው ፡ አጋጋመ ፡ እሳት ።

ሠ ፡ ቢበርደን ፡ እሳት ፡ አነደደ ፡ አፋፋመ ፤ ዕንጨት ፡ አቀጣጠለ ።

ወ ፡ ነገሩን ፡ አጋነነ ፡ አሻሻቀ ፤ ጸቡ ፡ እንዲከር ፡ አደረገ ።

153 ምን ፡ ያስጨንቅሃል ፡ በሹም ፡ ሽር ፡ ጒዳይ ፡
—አንተማ ፡ እንደራሴ ፡ አይደለህም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ምስለኔዬ ፡ ወኪሌ ፡ ሹሜ ፡ አይደለህምን ።

ወ ፡ እንደኔ ፡ ነህ ፤ አንተና ፡ እኔ ፡ አንድ ፡ ነን ።

154 ምን ፡ ያደርጋል ፡ ጠላ ፤ ምን ፡ ያደርጋል ፡ ጠጅ ፤
—ጠላትን ፡ መጋበዝ ፡ ቡን ፡ አርጎ ፡ ነው ፡ እንጅ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እንግዳን ፡ መሸኘት ፡ ቡና ፡ አፍልቶ ፡ አስተናግዶ ፡ ነው ።

ወ ፡ ጠላትን ፡ እያጋደሙ ፡ እየረበረቡ ፡ መጨፍጨፍ ፡ ተምች ፡ መምታት ፡ ያሻል ፤ መዘንጋት ፡ አይገባም ።

155 ምን ፡ ያጣላችኋል ፡ በመሬት ፡ ጒዳይ ፤
—አሁን ፡ ዘር ፡ ሲጠፋ ፡ ይቀር ፡ የለም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ የሚዘራው ፡ ሲታጣ ፡ የዘር ፡ እኽል ፡ ሲቸግር ፡ ቅብቅቡ ፡ ይከርም ፡ ሑዳዱ ፡ ያድር ፡ የለምን ፤ ምን ፡ ያደርግላችኋል ።

ወ ፡ የሰው ፡ ዘር ፡ ሲጠፋ ፡ መሬት ፡ ባዶዋን ፡ ትቀራለች ፤ የሚኖርባት ፡ ታጣለች ።

156 —ምንድነው ፡ ይህ ፡ አገር ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ደመና ፡
እንደኛ ፡ አገር ፡ ፀሓይ ፡ አይገኝምና ። (መዲ ፡ ቍ ፡ 6 ፡ ዘለ ፡ ቍ ፡ 804 ፡ 1127 ) ፡

1 ሠ ፡ ሁል ፡ ጊዜም ፡ ጉም ፡ ጭጋግ ፡ ነው ፤ ፀሓይ ፡ አይታይበትም ፤ የጠራ ፡ ቀን ፡ የለም ።

ወ ፡ ለሞተ ፡ ሰው ፡ ፍርድ ፡ አይታይለትም ፤ ደሙ ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ ይቀራል።

2 ሠ ፡ እንደኛ ፡ አገር ፡ ያለ ፡ ሙቀት ፡ ብርሃን ፡ አይገኝም ።

ወ ፡ ፍትሕ ፡ ያለበት ፡ እንደኛ ፡ አገር ፡ የለም ።

157 ምንድነው ፡ ጨኸቱ ፡ ከዚያ ፡ ላይ ፡ መንደር ፤
—ያፋጁታል ፡ ንጉሥ ፡ እንደ ፡ ወታደር ።

ሥ ፡ ንጉሥ ፡ ሕዝቡን ፡ ያጋድሉታል ፤ ያስተላልቁታል ፤ ርስ ፡ በርሱ ፡ ያፋጁታል ።

ወ ፡ ያ ፡ ደት ፡ ንጉሥ ፡ ሞቶ ፡ ሕዝቡን ፡ አስለቀሰው ፤ እንባ ፡ በንባ ፡ አ ደረገው ።

158 ምንድን ፡ ሊያበሉን ፡ ነው ፡ ፍሪዳ ፡ ያረዱ ፡
—ራስ ፡ መላስዎን ፡ ሸዋ ፡ የሰደዱ ። (ግ ፡ ው)፡

ሥ ፡ የበሬውን ፡ ምላስ ፡ ወደ ፡ ሸዋ ፡ ከላኩ ፡ ምን ፡ ሊያበሉን ፡ ነው ፤ ምላ ስና ፡ ሰንበር ፡ የሌለበት ፡ ሥጋ ፡ አያስደስትም ።

ወ ፡ ትክክለኛውን ፡ ዳኛ ፡ ፍርድ ፡ ዐዋቂውን ፡ ወደ ፡ ሸዋ ፡ ካስወሰዱ ፡ ማን ፡ ሊዳኘን ፡ ነው ።

159 ምን ፡ ጊዜ ፡ ነግዳ ፡ ምን ፡ ጊዜ ፡ አገኘችው ፡
—ከቤተ ፡ ክሲያን ፡ ጓሮ ፡ መሬት ፡ የገዛችው ።

ሥ ፡ የገዛችው ፡ መሬት ፡ ያገኘችው ፡ ምድር ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ አጠ ገብ ፡ ነው ።

ወ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጓሮ ፡ ተቀበረች ፤ በሦስት ፡ ክንድ ፡ መሬት ፡ ተወሰነች ።

160 ምን ፡ ጠላት ፡ መጣና ፡ በሌሊት ፡ ጠራው ፤
—ለመሬት ፡ እንደሆን ፡ ቀድሞም ፡ የጁ ፡ ነው ።

ሥ ፡ መሬቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቀድሞም ፡ አንጡራ ፡ ርስቱ ፡ ነው ፤ ለምን ፡ እፍርድ ፡ ቤት ፡ ተፈለገ ።

ወ ፡ ርስቱ ፡ ቤቱ ፡ ከሚገኝበት ፡ የጁ ፡ ከሚባል ፡ አገር ፡ ሞቶ ፡ ተቀበረ ።

161 ምድሬ ፡ ውሃ ፡ ጠጣ ፡ ቅብቅቤም ፡ አደረ ፤
—ዘር ፡ አንተ ፡ አለህ ፡ ቢሉ ፡ መጥቼ ፡ ነበረ ።

ሥ ፡ አንተ ፡ ካለህ ፡ አልቸገርም ፡ በማለት ፡ የዘር ፡ እኽል ፡ እንድታበ ድረኝ ፡ መጣሁ ።

ወ ፡ ያለኸኝ ፡ ዘመድ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ነህ ፤ ሌላ ፡ የለኝም ።

162 ምድርን ፡ ጠላ ፡ መጥመቅ ፡ ማን ፡ አስተማረው ፡
—እየጠራ ፡ አጠጣው ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ሰው ።

ሥ ፡ እየጠራ ፡ መጠጥ ፡ መጋበዝ ፡ ማንበሽበሽ ፡ ይወዳል ።

ወ ፡ መቃብር ፡ ሰውን ፡ ጨርሶ ፡ ወሰደው ፤ አሟጠጠው ።

163 ሞቱን ፡ የሰማሁት ፡ በግንቦት ፡ በሠኔ ፡
—አላውራ ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ አለመናገሬ ።

ሥ ፡ አላወራም ፡ ምስጢር ፡ አላወጣም ፡ ነገር ፡ አላባክንም ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ ሳልናገር ፡ የቀረሁት ።

ወ ፡ መሪ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሳይኖር ፡ ጉዳቴን ፡ ለማን ፡ አቤት ፡ ልበል ፤ ችግሬን ፡ ለማን ፡ ልንገረው ።

164 ሞት ፡ በየሰዉ ፡ ቤት ፡ ሲገባ ፡ ሲወጣ ፡
—እኔም ፡ ቤት ፡ አልቀረ ፡ በፈንታዬ ፡ መጣ ።

ሠ ፡ በተራዬ ፡ ደረሰኝ ፤ ዕድል ፡ ፈንታዬን ፡ ተወጣሁት ።
ወ ፡ በፈንታዬ ፡ ሞት ፡ ሐዘን ፡ እኔም ፡ ቤት ፡ ገባ ፤ የመከራዬ ፡ ጊዜ ፡ ደረሰ ።

165 ሞት ፡ ይቅር ፡ ይላሉ ፡ ሞት ፡ ቢቀር ፡ አልወድም ፤
—ድንጋዩም ፡ ዐፈሩም ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ አይከብድም ።

ሠ ፡ መቃብር ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ የበለጠ ፡ አያስጨንቅም ፤ አያሠቅቅም ።
ወ ፡ ዐፈሩ ፡ ድንጋዩ ፡ የሰውን ፡ ፊት ፡ ያኽል ፡ አይከብድም ።

166 ሞት ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ መስሎ ፡ ባሕታዊ ፡ ምእመን ፡
—ዕጣን ፡ ይዞ ፡ ሄደ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክሲያን ።

ሠ ፡ ዕጣን ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ብፅዐት ፡ ሰጠ ፤ መባ ፡ አበረከተ ።
ወ ፡ ሞት ፡ ሕፃኑን ፡ ልጅ ፡ ገደለው ፤ ጨቅላውን ፡ ወሰደው ።

167 ሞት ፡ ፊደል ፡ ተምሮ ፡ ያነባል ፡ ስንል ፡
—እንኳን ፡ ሊያነብና ፡ ገና ፡ ያግዛል ።

ሠ ፡ የፊደሉን ፡ ዘር ፡ ይቈጥራል ፤ ግእዙን ፡ ካዕቡን ፡ ለመለየት ፡ ይጣጣራል ።
ወ ፡ ሞት ፡ በየጊዜው ፡ ያዳምን ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ያግዛል ።

168 ሞጣም ፡ ቀራንዮም ፡ ሁሉም ፡ ደብር ፡ ነው ፤
—በየሱስ ፡ ንገረኝ ፡ ያለቀውን ፡ ሰው ።

ሠ ፡ የሞተውን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ የተለየውን ፡ የሙታንን ፡ ቍጥር ፡ እባክህ ፡ በየሱስ ፡ ብለህ ፡ ንገረኝ ፡ አስረዳኝ ።
ወ ፡ በየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ ስም ፡ የሞተውን ፡ ስለ ፡ ሃይማኖቱ ፡ ሕይወቱን ፡ ያሳለፈውን ፡ ሰው ፡ ብዛት ፡ እስቲ ፡ ንገረኝ ፤ ሰማዕታቱ ፡ ስንት ፡ ናቸው ።

169 ሞጣ ፡ ቀራንዮ ፡ ምነው ፡ አይታረስ ፤
ደምበጫ ፡ ደብረ ፡ ወርቅ ፡ ምነው ፡ አይታረስ ፤
—በሬ ፡ ሳላይ ፡ መጣሁ ፡ ከዚያ ፡ እስከዚህ ፡ ድረስ ።

ሠ ፡ የተጠመደ ፡ በሬ ፡ ሳላይ ፡ መጣሁ ፤ በመንገድ ፡ የሚያርስ ፡ አልነበረም ፤ ሞፈር ፡ ቀንበር ፡ አላየሁም ።
ወ ፡ አስከሬን ፡ እየረመረምሁ ፡ የሰው ፡ ሬሳ ፡ እየረገጥሁ ፡ መጣሁ ።

170 ሞጣ ፡ ቀራንዮ ፡ ሞልቶ ፡ ካህናቱ ፡
—እነራስ ፡ በዛብህ ፡ ሳይፈቱ ፡ ሞቱ ።

ሠ ፡ የቁም ፡ ፍትሐት ፡ ሳይደርስላቸው ፡ ምሕላ ፡ ሳይደረግላቸው ፡ ሞቱ ።
ወ ፡ ከወህኒ ፡ ቤት ፡ ሳይወጡ ፡ ከግዞት ፡ ሳይለቀቁ ፡ እንደ ፡ ታሰሩ ፡ ሞቱ ፤ ዐረፉ ።

171 ሞጣ ፡ ቀራንዮ ፡ ጽላሎና ፡ ጐንጂ ፡
—እረ ፡ ሰውና ፡ ሰው ፤ ሰውና ፡ ሰው ፡ እንጂ ። (1)

ሠ ፡ ሰውና ፡ ሰው ፡ አልተስማማም ፤ ርስ ፡ በርሱ ፡ ተባላ ፤ አንዱ ፡ ላንዱ ፡ የማይተኛ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ሰውን ፡ ገድሎ ፡ ግንብ ፡ ገነባበት ፤ በሬሳው ፡ ላይ ፡ ቤት ፡ ሠራበት ።

172 ሞፈርና ፡ ቀንበር ፡ መቼ ፡ ጠፉብኝ ፤
—የላይዳው ፡ ችግር ፡ ነው ፡ ካገር ፡ ያስወጣኝ ።

ሠ ፡ «ላይዳ» ፡ አይገኝም ፤ ችግር ፡ ነው ፡ የሚያውስ ፡ የለም ።

ወ ፡ የሰማይ ፡ ቤት ፡ ፍዳ ፡ ያሠቅቃል ፡ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ያስፈራል ።

173 ሠርቼ ፡ ሠርቼ ፡ አዳራሽ ፡ ከልፍኝ ፡
—በማለቂያው ፡ ጊዜ ፡ ላፈርሰው ፡ ሆንኩኝ ።

ሠ ፡ ሠርቼ ፡ ሠርቼ ፡ ሊያልቅ ፡ ሲል ፡ ላፈርሰው ፡ ነው ፤ ለፍቼ ፡ ለፍቼ ፡ መና ፡ ልቀር ፡ ነው ።

ወ ፡ በመጨረሻው ፡ ዐፈር ፡ ለመሆን ፡ ተፈጠርሁ ፤ በፍጻሜዬ ፡ ጊዜ ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ እለወጣለሁ ፤ ዕድሜዬ ፡ ሲያልቅ ፡ ትቢያ ፡ እሆናለሁ ።

174 ሠዓሊዎች ፡ መልኬን ፡ ሳይመለከቱኝ ፡
ሥጋ ፡ በሌለው ፡ ሰው ፡ በዐፅም ፡ መሰሉኝ ፤
—ከግር ፡ እስከ ፡ ራሴ ፡ ጥቍር ፡ አለበሱኝ ።

ሠ ፡ መላ ፡ ሰውነቴን ፡ ጥቍር ፡ ልብስ ፡ ጀቡኑኝ ፤ አጐናጠፉኝ ፤ አከናነቡኝ ።

ወ ፡ አሳዘኑኝ ፤ አበሳጩኝ ፤ አናደዱኝ ፤ አስከፉኝ ።

175 ሣጥኑን ፡ ስትመቱ ፡ ምስማር ፡ እያያችሁ ፤
—ያን ፡ የኔን ፡ ብርጭቆ ፡ ትሰብሩታላችሁ ።

ሠ ፡ ብርጭቆዬን ፡ እንዳትሰብሩብኝ ፡ አስተውላችሁ ፡ ተጠንቅቃችሁ ፡ ምቱ ።

ወ ፡ ድንጋዩን ፡ ዐፈሩን ፡ ቀስ ፡ እያላችሁ ፡ መልሱ ፤ የተወዳጁ ፡ ልጄን ፡ አስከሬን ፡ አታጕላሉት ።

176 ሣጥን ፡ ሳልገዛልሽ ፡ አወይ ፡ ድኽነቴ ፡
—አለምን ፡ አለምን ፡ ቀበርኩሽ ፡ እናቴ ።

ሠ ፡ ያለሰሌን ፡ ያለሣጥን ፡ ቀበርኩሽ ፤ ያለምናምን ፡ ዕርቃን ፡ ሥጋሽን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ አወረድሁሽ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ እናቴ ፡ ዓለሜ ፡ ተድላ ፡ ደስታዬ ፡ የማይቀር ፡ ሆነና ፡ ቀበርኩሽ ።

---

(1) ጐንጂ ፡ ጽላሎ ፡ በሚባል ፡ ቦታ ፡ የሚኖር ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ለንግድ ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ አገር ፡ ሄዶ ፡ ሳለ ፡ ሰዎች ፡ ገድለውት ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ግንብ ፡ ስለ ፡ ገነቡበት ፡ በሐዘን ፡ የተነደፈችው ፡ ሚስቲቱ ፡ የሚታሙትን ፡ ሰዎች ፡ ባየች ፡ ቍጥር ፡ ይህንን ፡ ታለቅስ ፡ ነበር ።

177 ሥራ ፡ ፈቶ ፡ ዋለ ፡ ትናንት ፡ ሸማኔው ፡
—ያ ፡ ቀለምሽ ፡ ነወይ ፡ የተበላሸው ።

ሠ ፡ ያ ፡ ቀለምኻ ፡ ጠፋ ፡ ወይ ፤ ቀለምሽ ፡ ተበላሸ ፡ ወይ ።

ወ ፡ ያ ፡ መልክሽ ፡ ውበትሽ ፡ ወደ ፡ ዐፈርነት ፡ ተለወጠ ፡ ወይ ፤ ደም ፡ ግባትሽ ፡ ተበላሸ ፡ ወይ ፤ መቃብር ፡ አጠፋው ፡ ወይ ።

178 ሥዕላችን ፡ ቆሞ ፡ ቢታይ ፡ እንደ ፡ ሕልም ፡
—ያለን ፡ ሰው ፡ ብንመስል ፡ ምንም ፡ የለንም ።

ሠ ፡ ከስተናል ፤ ጠቍረናል ፤ ምንም ፡ ሰውነት ፡ የለንም ፤ አይመስሉ ፡ መስለናል ፤ ውቃቢ ፡ ርቆናል ።

ወ ፡ ሀብት ፡ የለንም ፤ ድኽነት ፡ ተጭኖናል ፤ ቅርስ ፡ አጥተናል ።

179 ሥዩም ፡ ልጅ ፡ ወለደ ፡ አጥብቆ ፡ ደስ ፡ አለው ፤
—አሳዳጊው ፡ ግና ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ነው ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ምንም ፡ ሥዩም ፡ ቢወልደው ፡ ልጁን ፡ የሚያሳድገው ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ የሚያበቃው ፡ የሥላሴ ፡ ኃይል ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ነው ።

ወ ፡ ለክብር ፡ ለማዕርግ ፡ ለሹመት ፡ ለሽልማት ፡ የሚያበቃው ፡ በሥልጣን ፡ የሚያሳድገው ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ነው ።

180 ሥጋ ፡ ሥጋ ፡ ሸተትክ ፡ ለምን ፡ ትለኛለህ ፤
—ይኸን ፡ ርጥብ ፡ ሥጋ ፡ ለብሼው ፡ እያየህ ።

ሠ ፡ የሥጋ ፡ ቤት ፡ ሠራተኛ ፡ የቄራ ፡ ሥጋ ፡ ተሸካሚ ፡ በመሆኔ ፡ ሥጋ ፡ ሥጋ ፡ እሸታለሁ ፤ የሥጋ ፡ ጠረን ፡ በላዬ ፡ ላይ ፡ አለ ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ ለባሲ ፡ ፍጡር ፡ ነኝ ፤ ባሕርዬ ፡ ሥጋዊነት ፡ አለበት ።

181 ሥጋሽን ፡ ጠጅሽን ፡ ትሰጫለሽ ፡ ለሰው ፤ (ወደዘፈን ፡ የሚዛወር)
—አንቺ ፡ የማትሣሺው ፡ ለጠላሽ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ሥጋና ፡ ጠጅ ፡ ትሰጫለሽ ፤ ጠላሽን ፡ ግን ፡ ትነፍጊያለሽ ፤ አታቀምሽም ፤ አንቺ ፡ የጠላ ፡ መቸር ፡ አይሆንልሽም ።

ወ ፡ ለሚጠላሽ ፡ ለማይወድሽ ፡ ሰው ፡ አትሣሽም ፤ አታዝኒም ፤ ጨካኝ ፡ ነሽ ።

182 —ሥጋ ፡ ሥጋ ፡ ብሎ ፡ ሲነገር ፡ ዐዋጅ ፡
—ፈራሁ ፡ ተንቀጠቀጥሁ ፡ ደነገጥሁኝ ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ሥጋ ፡ አምጡ ፡ ተብሎ ፡ ተደጋግሞ ፡ ቢጠየቅ ፡ ባለመኖሩ ፡ ተጨነቅሁ ፤ ተቸገርሁ ።

ወ ፡ አስብበት ፡ ሠግተህ ፡ ኑር ፡ ተጠንቀቅ ፡ ተዘጋጅተህ ፡ ነቅተህ ፡ ተቀመጥ ፡ ተባልሁ ።

183 ሥጋ ፡ ቤቱ ፡ እያለ ፡ እየታየ ፡ ባይን ፡
—ሥጋ ፡ አምጣ ፡ ይለዋል ፡ የጠጅ ፡ አዛዡን ።

ሠ ፡ ፍሪዳ ፡ አቅርቦ ፡ ሥጋ ፡ አስመጣና ፡ አስቈርጥ ፡ ይለዋል ።

ወ ፡ አስብ ፤ አስተውል ፤ ትእዛዜን ፡ ፈጽም ፤ የምልህን ፡ ተጠንቅቀህ ፡ ስማ ።

184 ሥጋ ፡ አማረኝ ፡ አለች ፡ የቀለቤ ፡ እናት ፡
—መተማ ፡ አትሄድም ፡ ወይ ፡ ከታረደበት ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 87 ፡ 267) ፡

ሠ ፡ በሬ ፡ ከታረደበት ፡ ሥጋ ፡ ከሚገኝበት ፡ ለምን ፡ አትሄድም ።

ወ ፡ ልጅዋ ፡ ቀለቤ ፡ በሰይፍ ፡ እተከለለበት ፡ አገር ፡ እመተማ ፡ አትሄድም ፡ ወይ ፤ ልጁ ፡ ከሞተበት ፡ አትደርስም ፡ ወይ ።

185 ሥጋ ፡ እበላ ፡ ብዬ ፡ የቈረጥኩትን ፡
—ላሳያችሁ ፡ መጣሁ ፡ እኔማ ፡ ጣቴን ።

ሠ ፡ የተቈረጠውን ፡ ጣቴን ፡ ላሳያችሁ ፡ መጣሁ ፤ እዩት ፡ ተመልከቱት ።

ወ ፡ ማጣቴን ፡ መቸገሬን ፡ ድኽነቴን ፡ ልነግራችሁ ፡ ላዋያችሁ ፡ መጣሁ።

186 ሥጋ ፡ እበላ ፡ ብዬ ፡ ገና ፡ በተመኘሁ ፡
—አሁን ፡ ኸምን ፡ ጊዜው ፡ ምላስ ፡ ገብቶ ፡ አገኘሁ ።

ሠ ፡ እሥጋው ፡ ውስጥ ፡ ምላስ ፡ ጨመረበት ፤ አሁን ፡ ሥጋ ፡ ብቻ ፡ አልነበረምን ፤ ምላሱን ፡ ማን ፡ ቀላቀለው ።

ወ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ለሥጋዬ ፡ አድልቼ ፡ ብሳሳት ፡ ከምን ፡ ጊዜው ፡ ያሙኝ፡ ይቦጭቁኝ ፡ ዠመር ፤ ለማይጠቅም ፡ ነገር ፡ ከሰው ፡ አፍ ፡ መግባቴ ፡ ያሳዝናል ።

187 ሥጋውን ፡ ሰጡና ፡ ቢላዋውን ፡ ነሡ ፤
ዕንጨቱ ፡ ከሄደ ፡ በምን ፡ ይብሰል ፡ ገብሱ ።

ሠ ፡ ዕንጨቱ ፡ ከተወሰደ ፡ ገብሱ ፡ በምን ፡ ይቈላል ፤ በምንስ ፡ ይዘጋጃል ።

ወ ፡ ዕንጨቱ ፡ ደኑ ፡ ከሄደ ፡ መሬቱ ፡ ብቻ ፡ ምን ፡ ያደርግልኛል ፤ ሥጋ ፡ ሰጥቶ ፡ ቢላዋ ፡ እንደ ፡ መንሣት ፡ ያለ ፡ ይሆናል ።

188 ራስ ፡ ይፍቀዱልኝ ፡ እንድጠይቅዎ ፤
— ሰው ፡ ይዞ ፡ መብላትን ፡ ማን ፡ አስተማረዎ ።

ሠ ፡ ሰውን ፡ አስሮ ፡ አስገድዶ ፡ መብላት ፡ ማን ፡ አስለመደዎ ።

ወ ፡ ያለውን ፡ አብሮ ፡ መካፈልን ፡ ለብቻ ፡ አለመብላትን ፡ ከሰው ፡ ጋራ ፡ መመገብን ፡ ቸር ፡ መሆንን ፡ ማን ፡ አስተማረዎ ።

189 ራቡ ፡ በሆዴ ፡ በቅሎ ፡ ዘረዘረ ፤
—እናቴማ ፡ ብትኖር ፡ ታጭድልኝ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ መከሩን ፡ ታጭድልኝ ፡ አዝመራዬን ፡ ትሰበስብልኝ ፡ ነበር ።

ወ ፡ እናቴማ ፡ ብትኖር ፡ አይርበኝም ፡ ነበር ፤ ረኃቤን ፡ ታስታግሥልኝ ፡ ሆዴን ፡ ትሞላልኝ ፡ ነበር ።

190 ራብ ፡ ቢጠናብን ፡ እጅግ ፡ ቢጨንቀን ፡
—ጐመን ፡ በልተን ፡ አደርን ፡ ያነን ፡ ቀንጥሰን ።

ሠ ፡ ያንን ፡ ጐመን ፡ ቈርጠን ፡ ቀነጣጥሰን ፡ በልተን ፡ አደርን ።

ወ ፡ ያንን ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ አልፈን ፡ መጥፎውን ፡ ወራት ፡ ወጥተን ፡ የጭንቁ ፡ ጊዜ ፡ ተወገደልን ፤ እንዴት ፡ እናርፍ ፡ ይሆን ።

191 እራት ፡ በመታቀፍ ፡ አለቀ ፡ ሽማዬ ፤
—በቃ ፡ አድርገህ ፡ ስጠኝ ፡ እባክህ ፡ ጌታዬ ።

ሠ ፡ በገበታ ፡ በመሶብ ፡ በወስከንባይ ፡ አድርገህ ፡ ስጠኝ ፤ በዕቃ ፡ አቅርብልኝ ።

ወ ፡ እንደሚበቃ ፡ እንደማያንስ ፡ አድርገህ ፡ ሀብትን ፡ ስጠኝ ።

192 ርቀህም ፡ አትሂድ ፡ ጨርሰህ ፡ አትጥፋ ፤
—እስከ ፡ ጊዜው ፡ ድረስ ፡ ተቀመጥ ፡ ተከፋ ።

ሠ ፡ ከፋ ፡ ሄደህ ፡ ተቀመጥ ፤ እዚያ ፡ ኑር ።

ወ ፡ ቢከፋህም ፡ ብትበደልም ፡ እጊዜው ፡ ድረስ ፡ ታግሠህ ፡ አሳልፈህ ፡ ቻለው ።

193 ሰባት ፡ ዓመት ፡ ሥቃይ ፡ ከልቡ ፡ ባይደርስ ፡
—ተስሎ ፡ ተወጋ ፡ ቅዱስ ፡ ጊዮርጊስ ። (1)

ሠ ፡ ቅዱስ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ብፅዐት ፡ አድርጎ ፡ ስለቱን ፡ ለማድረስ ፡ በጦር ፡ ተወጋ ።

ወ ፡ የቅዱስ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ሥዕል ፡ በጦር ፡ ተወጋ ፤ በሾተል ፡ ተቀደደ ።

194 ሰኞ ፡ ለት ፡ ገሠገሥኩ ፡ ማክሰኞ ፡ ተጓዝሁ ፤
—ከቶ ፡ ብሄድ ፡ ብሄድ ፡ ረቡን ፡ አጣሁ ።

ሠ ፡ ረቡን ፡ አጣሁት ፤ ከቀኖቹ ፡ ሁሉ ፡ እሱ ፡ ጠፋብኝ ፤ ብፈልገው ፡ ባሰላስለው ፡ አልተገኘም ።

ወ ፡ ጥቅሙ ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አጣሁት ፤ ዋጋውን ፡ አላወቅሁትም ፤ ርባናው ፡ አልገባኝም ።

195 ሰዉ ፡ ለምንድነው ፡ የሚፈልግ ፡ ዋሻ ፡
—ከቤት ፡ ክሲያን ፡ ጓሮ ፡ እያለ ፡ መሸሻ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ መሸሸጊያ ፡ አለ ፤ መደበቂያ ፡ ይገኛል ፤ መከለያ ፡ ተርፏል ።

ወ ፡ «አቶ ፡ መሸሻ» ፡ እቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ጓሮ ፡ ተቀብሯል ።

196 ሰው ፡ ታሪክ ፡ ሲያነብ ፡ ዝምሮ ፡ በሀ ፡ ሁ ፡
—ቀን ፡ ማወቅ ፡ አቅቶኝ ፡ እኔ ፡ እኖራለሁ ።

---

(1) አረመኔ ፡ የቅዱስ ፡ ጊዮርጊስን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ አቃጥሎ ፡ በውስጡ ፡ ያገኘውን ፡ ሥዕል ፡ በጦር ፡ እየወጋ ፡ ሲጫወትበት ፡ ያየ ፡ ሰው ፡ ይህን ፡ ቅኔ ፡ ደረሰ ፡ ይባላል ።

ሡ ፡ ቀ ፡ የምትባለዋን ፡ ፊደል ፡ ዘር ፡ ማወቅ ፡ አቃተኝ ፤ መለየት ፡ ተሳነኝ ።

ወ ፡ የጊዜውን ፡ ሁናቴ ፡ ማወቅ ፡ መረዳት ፡ አልተቻለኝም ፤ ይህ ፡ ወራት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መገንዘብ ፡ አልሆነልኝም ።

197 ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሆዱ ፡ ጠጅ ፡ እያማረው ፡
—እግዚአብሔር ፡ ጠላና ፡ እንጀራ ፡ ነሣው ።

ሡ ፡ እንጀራ ፡ ጠላ ፡ ከለከለው ፤ እኽል ፡ ውሃ ፡ ነፈገው ፤ የሚጠጣው ፡ ሳይሰጠው ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ሀብት ፡ አሳጣው ፤ ድኻ ፡ አደረገው ፤ የሰው ፡ እጅ ፡ አሳየው ።

198 ሰው ፡ ሁሉ ፡ በማዘን ፡ ቤቱን ፡ ይሠራል ፤
—ምነው ፡ እናንተ ፡ ቤት ፡ አንድም ፡ ማዘን ፡ የለ ።

ሡ ፡ የዕንጨት ፡ ማእዘን ፡ የላችሁም ፤ ቋሚና ፡ አግዳሚ ፡ አላዘጋጃችሁም ።

ወ ፡ ሐዘንና ፡ ትካዜ ፡ በቤታችሁ ፡ የለም ፤ መጾም ፡ መጸለይ ፡ አታውቁም ።

199 ሰው ፡ ሁሉ ፡ በርስቱ ፡ ይጨርሳል ፡ ሀብቱን ፤
—የኋላ ፡ የኋላ ፡ ላያጣው ፡ መሬቱን ።

ሡ ፡ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ መሬቱን ፡ ያገኛል ፤ ውሎ ፡ አድሮ ፡ ርስቱን ፡ ይወርሳል ፤ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ምድሩን ፡ ይረከባል ።

ወ ፡ ያዳም ፡ ልጅ ፡ የመጨረሻ ፡ ርስቱ ፡ መቃብር ፡ ነው ፤ ኖሮ ፡ ኖሮ ፡ በሦስት ፡ ክንድ ፡ መሬት ፡ ይወሰናል ።

200 ሰው ፡ ሁሉ ፡ በከንቱ ፡ እንዴት ፡ ተታለለ ፡
—ያለእግዚአብሔር ፡ ላይሆን ፡ ያም ፡ አለ ፡ ያም ፡ አለ ።

ሡ ፡ ያም ፡ ቢል ፡ ያም ፡ ቢል ፡ ያለእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ አይሆንም ፤ ቢጥሩ ፡ ቢግሩ ፡ ቢደክሙ ፡ አድራጊው ፡ አንድ ፡ አምላክ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ወ ፡ ሁሉም ፡ ተማማሉ ፤ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ተገባቡ ።

201 ሰው ፡ ሁሉ ፡ አለጊዜው ፡ አረጀ ፡ አፈጀ ፤
—መኰንን ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ በውነቱ ፡ ያረጀ ።

ሡ ፡ በርግጥ ፡ በዕድሜው ፡ ያረጀ ፡ ሳይጕሳቈል ፡ ከእርጅና ፡ የደረሰ ፡ መኰንን ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ወ ፡ እውነትን ፡ ሳይለቅ ፡ ሐሰትን ፡ ሳይናገር ፡ የኖረ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ ብቻ ፡ ነው ።

202 ሰውም ፡ አላገኘሁ ፡ የሚያማልደኝ ፤
—ወንድሜ ፡ ታስሮብኝ ፡ እሄዳለሁኝ ።

ሡ ፡ ወንድሜ ፡ ታስሮ ፡ እወህኒ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ገባ ፡ ለመጠየቅ ፡ እሄዳለሁ ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ ሞቶ ፡ ስለ ፡ ተገነዘ ፡ ልቀብር ፡ እሄዳለሁ ።

203 ሰውነት ፡ ቢከሳ ፡ አካል ፡ ቢመነምን ፡
—እኔ ፡ ምን ፡ ቸገረኝ ፡ ራስ ፡ ደኅና ፡ ይሁን ፡፡ (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ብከሳ ፡ ብጠቍር ፡ ብቀጥን ፡ ብመነምን ፡ አእምሮዬ ፡ ትክክለኛ ፡ ከሆነ ፡ አላዝንም ፡፡

ወ ፡ የራስ ፡ እንጂ ፡ የአካል ፡ ግዝፈት ፡ ኀይል ፡ የለውም ፡፡

204 ሰው ፡ አይቸገርም ፡ ሌሊት ፡ ዝናብ ፡ ቢሆን ፤
— ጕዳት ፡ የሚበዛው ፡ ቀን ፡ የጣለ ፡ እንደሆን ፡፡

ሠ ፡ ዝናም ፡ ቀን ፡ የዘነመ ፡ እንደሆን ፡ ጕዳት ፡ ያመጣል ፤ ሰው ፡ ይቸገራል ፡፡

ወ ፡ ጊዜ ፡ የጣለ ፡ ዘመን ፡ ያዋረደ ፡ እንደሆን ፡ ለማንሰራራት ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ለመቋቋም ፡ አይቻልም ፡፡

205 ሰው ፡ ከሶኛል ፡ አሉ ፡ ቆሞ ፡ አደባባይ ፤
— እውነት ፡ ነውር ፡ ሆኖ ፡ ሊያስቀጣኝ ፡ ነወይ ፡፡ (ማ ፡ ወ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እውነት ፡ የሚያስከስስ ፡ የሚያስወቅሥ ፡ ጥፋት ፡ አግኝቶብኝ ፡ ሊያስቀጣኝ ፡ ይሆን ፡፡

ወ ፡ እውነት ፡ ተጠላ ፤ እንደ ፡ ነውር ፡ ተቈጠረ ፤ ከሰው ፡ አንደበት ፡ ጠፋ ፡፡

206 ሰፊ ፡ ቤት ፡ እያለው ፡ አዳራሽ ፡ ከልፍኝ ፡
— ምነው ፡ ባደባባይ ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ መታኝ ፡፡

ሠ ፡ ምነው ፡ ሕዝብ ፡ በተሰበሰበበት ፡ በሸንጎ ፡ ማኸል ፡ ባደባባይ ፡ እሰው ፡ ፊት ፡ ቀጣኝ ፤ አዋረደኝ ፡፡

ወ ፡ ምነው ፡ ፈጣሪዬ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ አሳየኝ ፤ ሀብት ፡ ነሣኝ ፤ የምበላው ፡ የምጠጣው ፡ አሳጣኝ ፡፡

207 ሲመሰገን ፡ ኖሮ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡
— ዛሬ፡ ብቻ ፡ ሠራ ፡ ሰው ፡ የሚያሳዝን ፡፡

የትኛው ፡ አንቀጽ ፡ ነው ፡ የተጠቀሰው ፤
—ያለውን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሞቱ ፡ ቀጣው ፡፡ (አ ፡ ደ) ፡

1 ሠ ፡ ገና ፡ ዛሬ ፡ ተሳሳተ ፤ ሰውን ፡ በደለ ፤ መጥፎ ፡ ሥራ ፡ ሠራ ፤ የማይገባ ፡ ነገር ፡ አደረገ ፡፡

ወ ፡ ሕዝቡን ፡ በሞቱ ፡ አሳዘነው ፤ አስለቀሰው ፤ እንባ ፡ በንባ ፡ አደረገው ፤ አንሰቀሰቀው ፡፡

2 ሠ ፡ ሁሉንም ፡ የሞት ፡ ፍርድ ፡ ፈረደበት ፤ አይቀጡ ፡ ቅጣት ፡ ቀጣው ፡፡

ወ ፡ በሞቱ ፡ ሕዝቡ ፡ ተጐዳ ፤ አገር ፡ ተበደለ ፤ (ስለ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ሞት) ፡፡

208 ሲበላ ፡ ሲጠጣ ፡ የማይወፍር ፡ ምነው ፤
—ጥንቱን ፡ ሲፈጠር ፡ የተጐዳ ፡ ሰው ፡ ነው ፡፡

ሠ ፡ ሲበላ ፡ የማይጠረቃ ፡ በተፈጥሮው ፡ ኰሳሳ ፡ የነሆ ፡ ሰው ፡ ነው ።

ወ ፡ በሥጋውም ፡ በነፍሱም ፡ መከራ ፡ የማይለየው ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ ነው ፤ በተፈጥሮው ፡ መጨነቅ ፡ መጠበብ ፤ መሥጋት ፡ አይለየውም ።

209 ሲናድ ፡ ሲናድ ፡ ያድራል ፡ እነማይ ፡ ሲሸበር ፤
—ወልታ ፡ መልከ ፡ ጥፉ ፡ ማስፈራሪያ ፡ ነበር ።

ሠ ፡ የወልታ ፡ መልክ ፡ ማስፈራሪያ ፡ ጐረጐማ ፡ አስቀያሚ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ኀይለኛው ፡ ወልታ ፡ ዘመዶቹን ፡ የሚያስከብር ፡ ጥቃት ፡ የማያስገባና ፡ የሚያኰራ ፡ ነበር ።

210 ሲንጫጫ ፡ ሰማሁት ፡ የጐዣም ፡ የዳሞት ፡ ያገው፡ ምድር፡ ወፉ፡
—የሚቀመጥበት ፡ ተሰብሮበት ፡ ዛፉ ።

ሠ ፡ መስፈሪያው ፡ ማደሪያው ፡ ዛፉ ፡ ተሰብሮበት ፡ ወፉ ፡ ሁሉ ፡ ይንጫጫል ፤ ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ ያንዣብባል ።

ወ ፡ አዛኝ ፡ ርኅሩኅ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሞቶበት ፡ ሕዝቡ ፡ ተጨንቋል ፤ ይዋልላል ፤ የሚሆነውን ፡ አጥቷል ።

211 ሳታድለኝ ፡ ቀረህ ፡ እጅ ፡ እጅህን ፡ ሳይ ፤
እኔስ ፡ ብሆን ፡ ያንተው ፡ አይደለሁም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ሳትሰጠኝ ፡ ሳታቀብለኝ ፡ ሳትቀዳልኝ ፡ ቀረህ ።

ወ ፡ እኔም ፡ ያንተው ፡ ፍጡር ፡ ነበርኩ ፤ የቀሩትን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ስታደርግ ፡ እኔን ፡ ተውከኝ ፤ ሀብት ፡ ነሣኸኝ ፤ ዕድለ ፡ ቢስ ፡ አደረግኸኝ ።

212 ስለ ፡ ሕይወቴ ፡ እኔ ፡ ምንም ፡ ምን ፡ አልፈራም ፤
—ባላባት ፡ ገድዬ ፡ የነካኝ ፡ ሰው ፡ የለም ። (1)

ሠ ፡ ያገር ፡ አዋይ ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡ ገድዬ ፡ ምንም ፡ አልሆንኩም ፤ የያዘኝ ፡ የለም ፤ አሳልፎ ፡ ሊሰጠኝ ፡ ማንም ፡ አልደፈረም ።

ወ ፡ እንደ ፡ አባት ፡ የሚያዝንልኝ ፡ ባሌ ፡ ሞተብኝ ፤ ዕድሌ ፡ አባት ፡ አከል፡ የሆነ ፡ ባሌን ፡ አሳጣኝ ።

213 ስለ ፡ ምን ፡ ማኅተሙ ፡ ሳይታተም ፡ ቀረ ፤
—ጃንሆይማ ፡ ያሉት ፡ አትሙት ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ ጃንሆይማ ፡ የሰጡት ፡ ትእዛዝ ፡ ማኅተም ፡ ይደረግበት ፡ የሚል ፡ ነበረ ፤ ለምን ፡ ሳይታተምበት ፡ ቀረ ።

ወ ፡ የጃንሆይ ፡ ጥረታቸው ፡ ልፋታቸው ፡ ሁሉ ፡ እንድትድን ፡ እንዳትሞት ፡ ነበር ።

---

(1) ጐሹ ፡ ኀይሉ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ባላባት ፡ መቼም ፡ ለባሕርዬ ፡ ተስማሚ ፡ የምትሆን ፡ ሴት ፡ ማግኘት ፡ አልችልም ፡ በማለት ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ሚስት ፡ ሳያገባ ፡ ከኖረ ፡ በኋላ ፡ ተመክሮ ፡ የሚያሳድጋት ፡ አንዲት ፡ ልጃገረድ ፡ ዐጨ ፤ እንደ ፡ ታሰበውም ፡ አግብቶ ፡ በሰላም ፡ ሲኖር ፡ ሞት ፡ አይቀርምና ፡ በድንገት ፡ ተቀድሞ ፡ ሞተ ፤ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ እንዳባት ፡ የምትቈጥረውን ፡ አሳዳጊ ፡ ባሏን ፡ በማጣቷ ፡ ሚስቲቱ ፡ የገጠመችው ።

214　ስልከኛው ፡ ሲያሳልፍ ፡ ቃል ፡ አሳስቶ ፡ ነው ፤
—መኰንን ፡ አይደለም ፡ የሞተው ፡ ድኻ ፡ ነው ።　　(አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ድኻ ፡ ይሆናል ፡ እንጂ ፡ መኰንን ፡ አልሞተም ።

ወ ፡ የተጐዳው ፡ ድኻው ፡ ነው ፤ የሚያስብለት ፡ የሚያስታውስለት ፡ አጣ፤ ችግሩን ፡ የሚነግርለት ፡ አላገኘም ፤ (ስለ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ ሞት) ።

215　ስበላ ፡ እየራበኝ ፡ ስጠጣ ፡ እየጠማኝ ፡ አንዠቴን ፡ ይዞት ፡
—ባሌ ፡ ደመኛዬ ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ።

ሠ ፡ ጠላቴ ፡ ባሌ ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ፤ ባለጋራዬ ፡ ባለቤቴ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ የባሌ ፡ ሐዘን ፡ ገዳዬ ፡ ሆነ ፤ ያጐሳቈለኝ ፡ አንዠቴን ፡ ያሳረረው ፡ ቈሽቴን ፡ ያደበነው ፡ የሱ ፡ ሞት ፡ ነው ።

216　ስትታመም ፡ ታማ ፡ ስትሞት ፡ ተቀበረች ፤
—አንተ ፡ ስትነሣ ፡ እናቴ ፡ የት ፡ ቀረች ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ስትድን ፡ ከሞት ፡ ስትነሣ ፡ እናቴ ፡ አልተነሣችም ፤ የት ፡ ተውሃት ፤ ለማን ፡ ጥለሃት ፡ መጣህ ።

ወ ፡ አንተ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ስትል ፡ ሀብት ፡ ስታገኝ ፡ እሷ ፡ ለምን ፡ ቀረች ፤ አብራችሁ ፡ ለፍታችሁ ፡ አንተ ፡ ቀን ፡ ሲወጣልህ ፡ እናቴ ፡ ቀረባት ።

217　ሥንቄን ፡ ሠንቁልኝ ፡ ርቄ ፡ እሄዳለሁ ፤
—እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ሳማ ፡ እኖራለሁ ።　(አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ የምኞቴን ፡ ባለማግኘቴ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ በሐሜትና ፡ በሐዘን ፡ ተቀምጬ ፡ እኖራለሁ ።

ወ ፡ ስንት ፡ ዘመን ፡ የሳማን ፡ ገዳም ፡ ተሾሜ ፡ እቀመጣለሁ ፤ ወደ ፡ ሌላ ፡ ወደ ፡ ከፍተኛው ፡ ደብር ፡ አልዛወርምን ።

218　ስንጨነቅ ፡ ነበር ፡ ለመቀሌው ፡ ዘማች ፤
ስንጨነቅ ፡ ነበር ፡ ለሸዋውም ፡ ዘማች ፤
—እሱም ፡ ደኅና ፡ ገባ ፡ እሷም ፡ ደኅና ፡ ገባች ።　　(ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ሁለቱም ፡ በሰላም ፡ ከዘመቻው ፡ ተመለሱ ፤ ጕዳት ፡ ሳያገኛቸው ፡ ሳይጐሳቈሉ ፡ እንኳን ፡ በደኅና ፡ እቤታቸው ፡ ገቡ ።

ወ ፡ ጋብቻቸው ፡ መልካም ፡ ነው ፤ አቻ ፡ ለአቻ ፡ እኩያ ፡ ነው ፤ እሱ ፡ ለእሷ ፡ እሷም ፡ ለርሱ ፡ የተስማሙ ፡ ናቸው ።

219　ሦስቱም ፡ ልጆችህ ፡ ለብሰው ፡ አዲስ ፡ ልብስ ፡
—ተኝተውልሃል ፡ እቤተ ፡ መቅደስ ፤
—እባክህ ፡ ጌታዬ ፡ ተነሣ ፡ ቀስቅስ ።

1　ሠ ፡ አባ ፡ ቀስቅስ ፤ ልጆችህ ፡ እቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተኝተው ፡ እንቅልፍ ፡ ወስዷቸዋል ፤ አስነሣቸው ፤ እንዲነቁ ፡ አድርጋቸው ።

ወ ፡ ልጆችህ ፡ ከቤተ ፡ መቅደሱ ፡ ውስጥ ፡ ተቀብረዋል ።

2 ሠ ፡ አንተም ፡ ንቃ ፥ እነሱንም ፡ ቀስቅሳቸው ፤ ከእንቅልፋቸው ፡ አስነሣቸው ።

ወ ፡ አባ ፡ ቀስቅስን ፡ ተነሣ ፡ በሉት ፤ አንቂት ።

220 ሸማኔው ፡ ሰውዬ ፡ ችግር ፡ ሳይገባው ፤
—አንድ ፡ ዐርብ ፡ ቢኖረው ፡ ለሥጋ ፡ ሸጠው ። (በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ ሸማ ፡ ሠሪው ፡ ዐርቡን ፡ የሸማኔ ፡ ዕቃውን ፡ ለሥጋ ፡ ሸጠው ።

ወ ፡ ሰው ፡ የጾምን ፡ ነገር ፡ ተወው ፤ ዐርብ ፡ ረቡን ፡ እንኳ ፡ ይበላ ፡ ወተት ፡ ይጠጣ ፡ ዠመር ፤ ሆድ ፡ አምላኩ ፡ ሆነ ።

221 ሸማ ፡ የምታጥቡ ፡ ቀጭን ፡ ሸማ ፡ ለምለም ፤
—እንደ ፡ ገፎ ፡ ውሃ ፡ የሚያጠራ ፡ የለም ።

ሠ ፡ ልብስ ፡ የሚያጠራ ፡ እንደ ፡ ገፎ ፡ ወንዝ ፡ ውሃ ፡ ያለ ፡ የለም ።

ወ ፡ የገፎ ፡ ወንዝ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ወሰደ ፤ ሕዝቡን ፡ ጠራረገው ፡ ጨረሰው ።

222 ሸማማ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እለብስ ፡ የለም ፡ ወይ ፤
—ብርቅ ፡ መስሎ ፡ ታየኝ ፡ ጥበብ ፡ ለብሰው ፡ ሳይ ።

ሠ ፡ የጥበብ ፡ ሸማ ፡ የለበሱ ፡ ሰዎች ፡ ያስቀኑኛል ፤ ያምሩኛል ፤ የጥበብ ፡ ኩታ ፡ ያስደስታል ።

ወ ፡ ተማሪዎች ፡ ሠልጥነው ፡ ጠቢባን ፡ ሁነው ፡ ማየት ፡ ያስደስተኛል ።

223 ሸንበቆን ፡ ግድግዳ ፡ ማገር ፡ ከመቍረጥ ፡
—ማዘን ፡ ቤት ፡ ይሠራል ፡ የማይናወጥ ።

ሠ ፡ ከመቃና ፡ ከሸንበቆ ፡ ይልቅ ፡ በማዘን ፡ ጠርብ ፡ የሚሠራው ፡ ቤት ፡ አይናወጥም ፤ ይጠነክራል ፤ ቶሎ ፡ አይዘምም ።

ወ ፡ ማዘን ፡ መተከዝ ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ መለመን ፥ ልብን ፡ ለፈጣሪ ፡ መስጠት ፤ ትዳር ፡ ያቀናል ፡ መልካም ፡ ትውልድን ፡ ይሰጣል ፤ ዘር ፡ ያወጣል ።

224 ሸንኝ ፡ ትለኛለች ፡ የሴት ፡ ዘበናይ ፤
—ያገርሽ ፡ ጐዳና ፡ ጐዣም ፡ ጠፋሽ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ያገርሽ ፡ የጐዣም ፡ መንገድ ፡ ጠፋሽ ፡ ወይ ፤ ተረሳሽ ፡ ወይ ።

ወ ፡ ጐዣም ፡ አገሬ ፡ ጠፋሽ ፤ ተዘረፍሽ ፤ ተበዘበዝሽ ፤ ጠላት ፡ ወረረሽ ።

225 ሸክላን ፡ በሩቅ ፡ ሲያዩት ፡ ብረት ፡ ይመስላል ፤
—ለመረመረው ፡ ሰው ፡ ገል ፡ ዐፈር ፡ ኖሯል ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ሸክላ ፡ የሚሠራው ፡ ከዐፈር ፡ ኖሯል ፤ ዐፈር ፡ ሸክላ ፡ መሆኑ ፡ ዛሬ ፡ ገና ፡ ገባኝ ።

ወ ፡ የሰው ፡ አካል ፡ በመቃብር ፡ ይፈርሳል ፤ ይበሰብሳል ፤ ወደ ፡ ዐፈርነቱ ፡ ይመለሳል ።

226 ሸክም ፡ ተሸክሜ ፡ አለቅጥ ፡ ቢደክመኝ ፡
—ከድካሜ ፡ በቀር ፡ የለም ፡ ያዋረደኝ ።

ሠ ፡ ደክሞኝ ፡ ያወረደልኝ ፡ የለም ፤ የተሸከምሁትን ፡ ሳወርድ ፡ የረዳኝ ፡
የለም ፤ የደገፈልኝ ፡ አልነበረም ።

ወ ፡ ዝቅተኛ ፡ ዐቅመ ፡ ቢስ ፡ በመሆኔ ፡ ተዋረድሁ ፤ ዐቅም ፡ ማጣት ፡ ዝቅ
ተኛ ፡ አደረገኝ ፤ የጐልበት ፡ ማነስ ፡ አዋረደኝ ።

227 ሸዋ ፡ የጨዋ ፡ ልጅ ፡ የተበደላችሁ ፡
ትግሬም ፡ የጨዋ ፡ ልጅ ፡ የተበደላችሁ ፡
—ንጉሡ ፡ ለመስቀል ፡ ጐንደር ፡ ግቡ ፡ አሏችሁ ።

ሠ ፡ ንጉሡ ፡ የተበደላችሁ ፡ እንድትነግሯቸው ፡ የተዋለባችሁን ፡ ግፍ ፡
እንድታስረዷቸው ፡ የመስቀል ፡ ለት ፡ ጐንደር ፡ ግቡ ፡ ብለዋች
ኋል ።

ወ ፡ ንጉሡ ፡ ጐንደር ፡ ድረስ ፡ የሚጠሯችሁ ፡ ሊሰቅሏችሁ ፡ ሊያንጠለጥ
ሏችሁ ፡ ነው ፤ ይህን ፡ እንድታውቁት ፡ ልብ ፡ እንድታደርጉት ።

228 ሺሕ ፡ ኀመር ፡ ሺሕ ፡ ጉራች ፡ የሸዋ ፡ ፈረስ ፤
—አንድ ፡ ጥርኝ ፡ ሆነ ፡ ቢዘልቅ ፡ ቴዎድሮስ ።

ሠ ፡ ኀመሩ ፡ ጉራቻው ፡ ፈረስ ፡ ብዙ ፤ ነው ፡ የቴዎድሮስ ፡ ፈረሱ ፡ ግን ፡
አንድ ፡ ጥርኝ ፡ የሚባል ፡ ነው ።

ወ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ዐፈር ፡ ቅጠል ፡ የነበረው ፡ ጦር ፡ እፍኝ ፡ የማይሞላ ፡ ጥ
ርኝ ፡ ሆነ ፤ ከግምት ፡ በታች ፡ ዋለ ፤ በቀላሉ ፡ ድል ፡ ሆነ ።

229 ሽማግሌ ፡ ሁሉ ፡ ታረቂ ፡ ቢላት ፡
—እንቢ ፡ ነገር ፡ ብላ ፡ ሄደች ፡ አሉ ፡ ጧት ።

ሠ ፡ ነገር ፡ ጠላች ፤ ከአምባጓሮ ፡ መራቅ ፡ ፈቀደች ፤ እሰው ፡ ነገር ፡ አለመ
ድረስን ፡ መረጠች ።

ወ ፡ ከነጋዴ ፡ ጋራ ፡ ውላ ፡ በእንቢ ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ተቀምጣ ፡ ሄደች ።

230 ሽንብራ ፡ ይሆናል ፡ ፎገራን ፡ ላረሰው ፤
—እጁን ፡ አያሲዝም ፡ ለጠረጠረ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ለመጠርጠር ፡ ለመፈልፈል ፡ ፍሬውን ፡ ከገለባው ፡ በጥርስ ፡ ለመለ
የት ፡ አያስቸግርም ፤ በቀላሉ ፡ ይፈለፈላል ።

ወ ፡ ሰው ፡ ከጠረጠረ ፡ አይያዝም ፤ ከተጠነቀቀ ፡ እጠላቱ ፡ እጅ ፡ አይወድ
ቅም ፤ ካደጋ ፡ ይድናል ፤ ያመልጣል ።

231 ሽንብራውን ፡ ዘርተን ፡ እሸቱን ፡ ስንበላ ፡
—አወይ ፡ የኛ ፡ ነገር ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ጥርጠራ ።

ሠ ፡ የኛ ፡ ነገር ፡ የተዘራውን ፡ ሽንብራ ፡ በእሸቱ ፡ እንጨርሰዋለን ፤ ፈል
ፍለን ፡ አውልበን ፡ ጥርጣሪው ፡ ብቻ ፡ ይቀራል ።

ወ ፡ ርስ ፡ በርሳችን ፡ አንተማመንም ፤ መጠራጠር ፡ በማኸላችን ፡ አለ ፤
ሆድ ፡ ለሆድ ፡ አንገናኝም ።

232 ቀለምና ፡ ቀለም ፡ ተጣልተው ፡ በቦታ ፡
ጊዜ ፡ ተሰጥቷቸው ፡ የቀጠሮ ፡ ተርታ ፤

ነገሩን ፡ ብንጠይቅ ፡ አግድሞ ፡ ካለፈ ፡
—ብለው ፡ ገለጹልን ፡ ወ ፡ ገን ፡ አሸነፈ ።

ሠ ፡ «ወ» የሚባለው ፡ የፊደል ፡ ዘር ፡ «ገ» የሚባለውን ፡ የፊደል ፡ ዘር ፡ አሸነፈ ፤ አየለበት ፤ በረታበት ።

ወ ፡ ወገን ፡ አጋር ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ አሸነፈ ።

233 ቀለብ ፡ እናታችን ፡ ሁሉን ፡ ያሳደገች ፡
በማቴዎስ ፡ ታማ ፡ በማርቆስ ፡ ሞተች ።

መታመሟንና ፡ መሞቷን ፡ ሰማነው ፤
—መቃብር ፡ ቈፍሮ ፡ የቀበራት ፡ ማነው ።

ሠ ፡ መቃብርን ፡ የቈፈረ ፡ አስከሬኗን ፡ የቀበረ ፡ ማነው ፤ በውነት ፡ ስትቀበር ፡ የነበረ ፡ ዐፈር ፡ የመለሰ ፡ ማነው ።

ወ ፡ ቀለባችንን ፡ ያስቀራት ፡ የቀነሳት ፡ ማነው ፤ የከለከለን ፡ እንዳንሰጥ ፡ ያደረገን ፡ ማነው ፡ ይሆን ።

234 ቀኑን ፡ ባሸንፈው ፡ ሌት ፡ መጥቶ ፡ ታገለኝ ፤
—በኀይሉ ፡ ሞት ፡ ናና ፡ እባክህ ፡ ገላግለኝ ።

ሠ ፡ ስለ ፡ ኀይሉ ፡ ብለህ ፡ እንድትመጣ ፤ በሱ ፡ ይዤሃለሁ ፡ እንዳትቀርብኝ ፤ ገላግለኝ ።

ወ ፡ ሞት ፡ ሆይ ፡ እባክህ ፡ ኀይሉን ፡ ገላግለኝ ፤ ከሚያስቸግረኝ ፡ በሥልጣንህ ፡ ከላዬ ፡ ላይ ፡ አስወግድልኝ ።

235 ቀድሞ ፡ ሥጋን ፡ ጠልተው ፡ በጌትነትዎ ፤
—ራስ ፡ የሰው ፡ አንገት ፡ ምነው ፡ መብላትዎ ።

ሠ ፡ እንዴት ፡ ርስዎን ፡ ያኽል ፡ ትልቅ ፡ ሰው ፡ ያንገት ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ፤ ቈሸት ፡ ይመገባል ።

ወ ፡ ሞትዎ ፡ ካንገት ፡ ያሳዝናል ፤ ያስለቅሳል ፤ ያንገበግባል ፤ ሆድን ፡ ይበላል ።

236 ቀድሞ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ከቤት ፡ የተቀመጥሁ ፤
—ዛሬማ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ አያለሁ ።

ሠ ፡ ከአደባባይ ፡ እውላለሁ ፤ ከብዙ ፡ ሰው ፡ እገናኛለሁ ፤ አያሌ ፡ ሰው ፡ ተዋውቂያለሁ ።

ወ ፡ ተቸግሬያለሁ ፤ የሰው ፡ እጅ ፡ አያለሁ ፤ ፊት ፡ ገርፎኛል ፤ ችግር ፡ በዝቶብኛል ።

237 ቀድሞውን ፡ ሲፈጠር ፡ ሥጋ ፡ ብለውት ፡
ሲጨነቅ ፡ ይኖራል ፡ የለጡም ፡ ዕረፍት ።

ሠ ፡ ተጠንቀቅ ፡ ስላሉት ፡ ይሠጋል ፤ ይንቀጠቀጣል ፤ የሚሆነውን ፡ አጥ
ቶት ፡ ይርበደበዳል ።

ወ ፡ ሰው ፡ ለሥጋት ፡ ለመከራ ፡ የተፈጠረ ፡ ነው ፤ ሠግተህ ፡ ኑር ፡ ብሎ
ታል ፤ መጨነቅ ፡ መጠበብ ፡ በባሕርዩ ፡ ያለ ፡ ነው ።

238 ቍናው ፡ ቍናዬ ፡ ነው ፡ ይሁን ፡ እንደ ፡ ዋዛ ፤
—ምነው ፡ በኔ ፡ ጊዜ ፡ በጣም ፡ ዙሩ ፡ በዛ ።　　(ራስ ፡ ጎ ፡ ተ ፡ ሃ) ፡

ሠ ፡ የስፌቱ ፡ ዙር ፡ በዛ ፤ ቅጥሉ ፡ መሥመሩ ፡ ከኔው ፡ ላቀ ፤ የቍናው ፡
መጠን ፡ ከኔው ፡ በለጠ ።

ወ ፡ እኔ ፡ ከሠራሁት ፡ በደል ፡ የደረሰብኝ ፡ ቅጣት ፡ የበለጠ ፡ ሆነ ፤ ይህን ፡
ያኽል ፡ ያጠፋሁ ፡ አይመስለኝም ፡ ነበር ።

239 ቍጠባ ፡ ሳናደርግ ፡ ተሻምተን ፡ በልተን ፡
—እነኛ ፡ ወጣጡ ፡ እኛ ፡ እንጀራ ፡ አጣን ።

ሠ ፡ እነሱ ፡ እንጀራ ፡ አግኝተው ፡ ወጥ ፡ ሳያገኙ ፡ ቀሩ ፤ እኛ ፡ ደግሞ ፡ እን
ጀራ ፡ አጣን ።

ወ ፡ እነሱ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ወጣ ፡ ወጣ ፡ እያሉ ፡ ወደ ፡ ላይ ፡ በሥልጣን ፡ አ
ደጉ ፤ እኛ ፡ ግን ፡ ሀብት ፡ አጣን ፤ ራሳችንን ፡ መቻል ፡ አቃተን ።

240 ቍጠሩ ፡ ቢኗቸው ፡ የሳምንቱን ፡ ቀናት ፡
—ስድስቱን ፡ ጠሩና ፡ ረቡን ፡ ገደፉት ።

ሠ ፡ ስድስቱን ፡ ቀኖች ፡ ጠሩና ፡ ረቡን ፡ ሳይቈጥሩት ፡ ቀሩ ፤ ተዉት ፤ ዘ
ለሉት ፤ ገደፉት ።

ወ ፡ ከሳምንት ፡ አምስቱን ፡ ቀን ፡ ቢበሉ ፡ አነሳቸውና ፡ ረቡን ፡ በመ
ኻል ፡ ቢያገኙት ፡ ገደፉት ፤ ሥጋ ፡ ይበሉበት ፡ ወተት ፡ ይጠጡበት ፡
ዠመር ።

241 ቂማችንን ፡ ሲያውቀው ፡ ከኔ ፡ ጋር ፡ ተጣልቶ ፡
—ጋኔን ፡ ይለምን ፡ ወይ ፡ እቤት ፡ ድረስ ፡ መጥቶ ።

ሠ ፡ የጠላ ፡ ጋን ፡ ይለምነኝ ፡ ወይ ፤ መጥመቂያ ፡ ስጠኝ ፡ ይበል ፡ ወይ ።

ወ ፡ እንደ ፡ ሰይጣን ፡ ሆኖ ፡ ሊያስተኝ ፡ እንዴት ፡ እቤቴ ፡ ድረስ ፡ ይ
ምጣ ፤ እመኖሪያዬ ፡ ድረስ ፡ መጥቶ ፡ እንዴት ፡ ይፈትነኝ ።

242 ቃሌን ፡ ሳያስወርድ ፡ ከዳኛው ፡ ሳይደርስ ፡
—ሄዶ ፡ ገዳም ፡ ገባ ፡ ደብረ ፡ ሊባኖስ ።

ሠ ፡ መንኖ ፡ ዓለምን ፡ ንቆ ፡ ከገዳም ፡ ገባ ፤ ባሕታዊ ፡ ሆነ ፤ ለእግዚአብ
ሔር ፡ አደረ ።

ወ ፡ ሞቶ ፡ ደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ ተቀበረ ።

243 ቄስን ፡ ናት ፡ ወይ ፡ ዲያቆን ፡ የኛ ፡ እመቤታችን ፤
—ባርካ ፡ ተናኘ ፡ ወርቅ ፡ ይኸው ፡ አሳየችን ።　　(ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ በስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባረከችው ።

ወ ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ባርካ ፡ (ጀልባ) ፡ በልዕልት ፡ ተናኘ ፡ ወርቅ ፡ ኃ ፡ ሥ
ጊዜ ፡ ወጣ ፡ ተገኘ ።

244 ቅመማትን ፡ ሁሉ ፡ አንድም ፡ ሳይቀር ፡ ገዝታ ፡
—ተመለሰች ፡ አሉ ፡ ጤናዳምን ፡ አጥታ ።

ሠ ፡ «ጤናዳም» ፡ የሚባለውን ፡ ቅመም ፡ አጣች ፤ ተቸገረች ፤ ሳታገኝ ፡ ቀረች ።

ወ ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ጤና ፡ ቢስ ፡ ሆነ ፤ መቅኖ ፡ አጣ ፤ በበሽታ ፡ ተጠቃ ።

245 ቅባኑን ፡ ወጥቶ ፡ ሲተርፈው ፡ ለይፋት ፤
—ሱፍ ፡ አላጣሁ ፡ እኔ ፡ ያሰናጂ ፡ ጥፋት ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ቅመም ፡ አልተቸገርሁም ፤ ሱፍ ፡ የዘይት ፡ ቅመም ፡ ተርፎኛል ፤ አላጣሁም ።

ወ ፡ «ሱፋላ» ፡ የሚባለውን ፡ ልብስ ፡ አጣሁ ፤ ሳልሸለም ፡ ሳይሰጡኝ ፡ ቀረ ።

246 ቅኔውንስ ፡ ባስብ ፡ ብቀኝስ ፡ ብመራ ፡
—ኵርፍ ፡ አይደለሁም ፡ ወይ ፡ እኔ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ መቼ ፡ ንግግር ፡ አለኝ ፤ ተኳርፈን ፡ የለምን ፤ መቼ ፡ እንነጋገራለን ፤ ተቀያይመን ፡ የለምን ።

ወ ፡ እኔ ፡ ያለሁት ፡ ካንተ ፡ ጋራ ፡ ኩርፋ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ አይደለምን ፤ አብረን ፡ የምንኖር ፡ ሰዎች ፡ አይደለንም ፡ ወይ ።

247 ቅዳሜና ፡ እሑድን ፡ ሌትና ፡ ቀን ፡ ጦሜ ፡
—ሮብ ፡ ጧት ፡ ገደፍኩኝ ፡ ሥጋን ፡ ተሸክሜ ።

ሠ ፡ ጾሜ ፡ ጾሜ ፡ ሥጋ ፡ በላሁ ፤ ሮብን ፡ ገደፍኩ ፤ ተሳሳትሁ ፤ ጾምን ፡ ሻርሁ ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ ለባሲ ፡ በመሆኔ ፡ እሳሳታለሁ ፤ እግዚአብሔርን ፡ እበድላለሁ ፤ ሰውን ፡ አስቀይማለሁ ።

248 ቅዳሴ ፡ ገብቼ ፡ ተንሥኡ ፡ ጠፋብኝ ፤
—ታላቁ ፡ መከራ ፡ በሰማይ ፡ ሳለብኝ ።

ሠ ፡ «በሰማይ» ፡ የሚባል ፡ የቅዳሴ ፡ ጓዝ ፡ ገና ፡ ቀርቶኛል ፤ እሱን ፡ ማዜም ፡ አለብኝ ፤ ማወቅ ፡ ማጥናት ፡ ይገባኛል ።

ወ ፡ ገና ፡ ኵነኔ ፡ በሰማይ ፡ በነፍስ ፡ ቅጣት ፡ አለብኝ ፤ ገሃነመ ፡ እሳት ፡ ይጠብቀኝ ፡ ይሆናል ።

249 ቅጠል ፡ ይመስለኛል ፡ ሞት ፡ ያቤል ፡ ወዳጅ ፤
—ስሙም ፡ አቄራራጭ ፡ እናትና ፡ ልጅ ።

ሠ ፡ ሞት ፡ "አቄራራጭ " የሚባለውን ፡ እዩት ፡ ልጅዋን ፡ ጡት ፡ የምታስጥልበትን ፡ ቅጠል ፡ ይመስላል ።

ወ ፡ ሞት ፡ እናትና ፡ ልጅን ፡ መለየት ፡ መነጣጠል ፡ ያውቃል ።

250 ቆመህ ፡ ስትሿገት ፡ ዳኛው ፡ እያደላ ፡
ባፋረዱህ ፡ እንጂ ፡ እትህ ፡ ምን ፡ ልበላ ። (1)

1 ሠ ፡ ዳኝነት ፡ ባዩልህ ፡ በመረመሩልህ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ፍርድ ፡ ካዛቡብህ ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ላደርግልህ ፡ ምን ፡ ልረዳህ ፡ እችላለሁ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይየው ፡ እንጂ ።

ወ ፡ በአፋ ፡ አረዱህ ፤ ከለሉህ ።

2 ወ ፡ በአፍ ፡ አረዱህ ፡ ሸነገሉህ ፤ (ደለሉህ) ፤ አታለሉህ ።

251 በለሳን ፡ ደግ ፡ አገር ፡ የሚለው ፡ ማን ፡ አለ ፤
—በለስ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ እኛን ፡ የበደለ ። (ኤ ፡ ወ ፡ ጸ) ፡

ሠ ፡ እንደ ፡ በለሳ ፡ ተውሳክ ፡ የበዛበት ፡ አገር ፡ አለን ፤ ዘመዶቻችንን ፡ የፈጀ ፡ ያለሰው ፡ ያስቀረን ፡ እሱ ፡ አይደለምን ።

ወ ፡ ሞትና ፡ ኵነኔን ፡ ያኸል ፡ ዕዳ ፡ ያመጣብን ፡ ከገነት ፡ ያስወጣን ፡ በለስ ፡ የሚባለውን ፡ ፍሬ ፡ አዳም ፡ ስለ ፡ በላ ፡ አይደለምን ።

252 በሉ ፡ እናንተም ፡ ሂዱ ፡ እኛም ፡ ወደዚያው ፡ ነው ፤
—እንትም ፡ መንገደኛ ፡ ፊትና ፡ ኋላ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ተከታትለ ፡ ያይዞ ፡ መሄድ ፡ የተለመደ ፡ ነው ፤ ፊትና ፡ ኋላ ፡ መጓዝ ፡ ወግ ፡ ነው ።

ወ ፡ በቅደም ፡ ተከትል ፡ መሞት ፡ ተከታትሎ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ መለየት ፡ በየተራ ፡ ማረፍ ፡ የማይቀር ፡ ነው ።

253 በላሁ ፡ ይበቃኛል ፡ ከእንጀራው ፡ ከወጡ ፡
—እግዚአብሔር ፡ ይስጥልኝ ፡ ከሞሰቡ ፡ አይጡ ። (አ ፡ ገ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ከመሶብዎ ፡ እንጀራ ፡ አይጥፋ ፤ የሚበላም ፡ አይታጣ ፤ ሌማትዎ ፡ አይጕደል ፡ ማእድዎ ፡ አይጣጣ ።

ወ ፡ ከመሶብዎ ፡ ውስጥ ፡ ዐይጥ ፡ አለች ፤ ከሌማትዎ ፡ ዐይጥ ፡ ገብታለች ።

254 በሌሊት ፡ ከመሄድ ፡ በየሾኹ ፡ ላይ ፡
—ቀን ፡ እያዩ ፡ መሄድ ፡ አይሻልም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ በብርሃን ፡ ፀሐይ ፡ ሳለ ፡ መሄድ ፡ በጨለማ ፡ አለመጓዝ ፡ ሳይመሽ ፡ ለዐይን ፡ ሳይገዝ ፡ በጊዜ ፡ መከተት ፡ አይገባም ፡ ወይ ።

ወ ፡ መጥፎ ፡ ዘመን ፡ ሳይመጣ ፡ ቀድሞ ፡ መጓዝ ፡ በመልካም ፡ ወራት ፡ መሸኘትና ፡ በሰላም ፡ መሞት ፡ የተሻለ ፡ አይሆንምን ።

255 በልቼ ፡ ጠጥቼ ፡ ገባሁኝ ፡ ከፍዳ ፤
—አላልቅልህ ፡ ብሎኝ ፡ ይኸ ፡ የሥጋ ፡ ዕዳ ።

(1) በ ምድር ፡ መካነ ፡ ኢየሱስ ፡ በሚባል ፡ ቦታ ፡ አንዲት ፡ እግረ ፡ አንካሳ ፡ ሴት ፡ በችግር ፡ ስትኖር ፡ ጐዣም ፡ የነበረው ፡ ወንድሟ ፡ ሰምቶ ፡ ወስዶ ፡ በደኅና ፡ አስቀምጧት ፡ ሳለ ፡ ተከሶ ፡ ባፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ችሎት ፡ የሞት ፡ ፍርድ ፡ ተፈርዶበት ፡ አፋ ፡ በሚባል ፡ ፡ ከተደበደበ ፡ በኋላ ፡ የተከሰሰበት ፡ ነገር ፡ ሐሰት ፡ ሆኖ ፡ መገኘቱን ፡ በሰማች ፡ ገዜ ፡ የገጠመችው ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ የበላሁበት ፡ ዕዳ ፡ አለብኝ ፤ ፍሪዳ ፡ ገዝቼ ፡ ያመጣሁበትን ፡ ገንዘብ ፡ አልከፈልኩም ።

ወ ፡ የሥጋ ፡ መከራ ፡ አላልቅልህ ፡ አለኝ ፤ ሥጋዊ ፡ ችግር ፡ በዛብኝ ፤ የ ሰው ፡ ፊት ፡ ማየት ፡ ታከተኝ ።

256 —በል ፡ ተመለስ ፡ በይው ፡ በይ ፡ ወዴት ፡ ይሄዳል ፤
—መሸጋገሪያችን ፡ ድልድዩ ፡ ተንዷል ።

1 ሠ ፡ እስቲኮ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ የሚሄደው ፤ መድረሻው ፡ ወዴት ፡ ነው ።

ወ ፡ ማእድ ፡ ቀራቢው ፡ ግብር ፤ በላተኛው ፡ ድርጎ ፡ ተቀባዩ ፡ ተጠዋሪው ፡ እንግዲህ ፡ ወዴት ፡ ይድረስ ፤ ወዴትስ ፡ ይሂድ ።

2 ሠ ፡ መሸጋገሪያው ፡ ፈርሷል ፤ ተበላሽቷል ፤ መልካው ፡ ተንዷል ።

ወ ፡ ሕዝብ ፡ አስታራቂው ፡ አገር ፡ አዋዩ ፡ ሞቷል ፤ ጨዋው ፡ ሰው ፡ አል ቋል ።

257 በል ፡ እደር ፡ ጕሮዬ ፡ ነገ ፡ እቈርጥሃለሁ ፤
—ባንተም ፤ ክፉ ፡ ነገር ፡ ሰምቼብሃለሁ ።

ሠ ፡ መጥፎ ፡ ነገር ፡ ሰምቼብሃለሁ ፤ እንዳማሽኝ ፡ ዐውቄዋለሁ ፤ ተንኰል ፡ እንደ ፡ ሠራህብኝ ፡ ተረድቼዋለሁ ።

ወ ፡ ጕሮዬ ፤ ወቀሣን ፡ ሐሰትን ፡ ክፉ ፡ ነገርን ፡ ሰምቼብሃለሁ ፤ የሆነ ፡ ያልሆነውን ፡ አዳምጨብሃለሁ ።

258 በመሶቡ ፡ ሙሉ ፡ ይቅረብ ፡ እንጀራው ፤
—አስተዳዳሪያችን ፡ ሆደ ፡ ሰፊ ፡ ነው ። (ኤ ፡ ወ ፡ ጸ) ፡

ሠ ፡ አለቃችን ፡ በላተኛ ፡ ነው ፤ ምግብ ፡ ይደፍራል ፤ እንጀራውን ፡ በመ ሶብ ፡ ሞልታችሁ ፡ አቅርቡለት ።

ወ ፡ መሪያችን ፡ ታጋሽ ፡ ሆደ ፡ ሰፊ ፡ ነው ፤ በሆነው ፡ ባልሆነው ፡ መቈ ጣት ፡ ሰውን ፡ ማስቀየም ፡ አይፈልግም ።

259 በሚመጣው ፡ ፍዳ ፡ በኋለኛው ፡ ደይን ፡
—እስከ ፡ መች ፡ ድረስ ፡ ነው ፡ የኔ ፡ አለማዘን ።

ሠ ፡ ለምን ፡ እኔ ፡ አላዝንም ፤ አልጸልይም ፤ አልተክዝም ፤ እግዚአብሔ ርን ፡ አላስብም ፤ ዕለተ ፡ ሞቴን ፡ አልዘክርም ።

ወ ፡ ፍጹም ፡ ደስታ ፡ አግኝቼ ፡ አላውቅም ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ ደስታዬ ፡ ሐ ዘን ፡ ነው ፤ የኔ ፡ ተድላ ፡ ዓለም ፡ ብስጭትና ፡ ጸጸት ፡ ነው ።

260 በሚያዝያ ፡ ተዘርተህ ፡ ያልበቀልህ ፡ እንደሆን ፡
—አገርህ ፡ በጌምድር ፡ እንዴት ፡ ይራብ ፡ ይሆን ።

ሠ ፡ አዝመራዬ ፡ በሚያዝያ ፡ ዘርቼህ ፡ ያልበቀልክልኝ ፡ እንደሆን ፡ እንደ ሚርበኝ ፡ ዕወቅ ፤ እንደምቸገር ፡ ተገንዘብ ፤ የሰው ፡ እጅ ፡ ማየቴን ፡ አትርሳ ።

ወ ፡ በሚያዝያ ፡ ስትሞት ፤ ባንተ ፡ የሚተካ ፡ ልጅ ፡ ያልኖረ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ አገርህ ፡ በጌምድር ፡ እንዴት ፡ ይቸገር ፡ ይሆን ።

261 በማሩ ፡ መንገድ ፡ ከሰሬበታለሁ ፤
—እስኪ ፡ በማዘኑ ፡ እፈትነዋለሁ ።

ሠ ፡ እስቲ ፡ ደግሞ ፡ የዕንጨት ፡ ማእዘን ፡ በመንገድ ፡ ዕድሌን ፡ ልሞክረው ፤ ሀብቴን ፡ ልፈትነው ፤ ግንባሬን ፡ ልየው ።

ወ ፡ ፈጣሪዬን ፡ በማዘንና ፡ በመተከዝ ፡ እለምነዋለሁ ፤ ሌት ፡ ተቀን ፡ በመጸጸት ፡ በጾም ፡ በጸሎት ፡ አስታውሰዋለሁ ።

262 በማዘን ፡ መንገድ ፡ የተለመደው ፡
በሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ ገና ፡ ቀድሞ ፡ ነው ።

ሠ ፡ በማእዘን ፡ ዕንጨት ፡ መንገድ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ አይደለም ፤ የቈየ ፡ የተለመደ ፡ ነው ።

ወ ፡ በማዘን ፡ በመተከዝ ፡ ዘር ፡ ማውጣት ፡ ማስገኘት ፡ መንግሥትን ፡ ማጽናት ፡ የነገሥታታችን ፡ ተግባር ፡ ነው ።

263 በምሥራቅ ፡ በሰሜን ፡ የመጣን ፡ ጠላት ፤
—ጃንሆይ ፡ ካሳን ፡ ልከው ፡ በተራረቁት ።  (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ክሰው ፡ ዕርቅ ፡ ባደረጉ ፡ ሰላምን ፡ በፈለጉ ፡ ጠቡን ፡ ባበረዱት ፡ በተዉት ፡ መልካም ፡ ነበር ።

ወ ፡ በሰሜን ፡ የመጣውን ፡ ጠላት ፡ ራስ ፡ ካሳን ፡ አዝማች ፡ አድርገው ፡ በየተራው ፡ በወጉት ፡ ድል ፡ ባደረጉት ።

264 በሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ የተዘራው ፡ ገብስ ፡
—ቅንቅን ፡ ይበላዋል ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ።

ሠ ፡ ገብሱን ፡ ነቀዝ ፡ ያበላሸዋል ፤ ተባይ ፡ ይጫወትበታል ።

ወ ፡ ደጋግ ፡ ሰው ፡ ይጠራል ፤ መልካም ፡ ሐሳብ ፡ ያለው ፡ ይደገፋል ።

265 በሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ የታቀደው ፡ እድሞ ፡
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ በማዘን ፡ ይሠራል ፡ ደጋግሞ ።

ሠ ፡ አጥሩ ፡ የሚሠራው ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በግምብና ፡ ዕንጨት ፡ ነው ፤

ወ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በማዘን ፡ በመጸለይ ፡ መንግሥቱ ፡ ጸንቶ ፡ ይኖራል ፤ ከጠላት ፡ ይጠበቃል ፤ ከወረራ ፡ ይድናል ፤ ከዘራፊ ፡ ይሰወራል ።

266 በሥረ ፡ ነገሩ ፡ ውርርድ ፡ ካነሣ ፡
—ጠቅል ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ይህ ፡ እንዳይረሳ ።  (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አንሣሁ ፡ ተረታሁ ፡ እንዲል ፡ ማድረግ ፡ ነው ፤ አጕራህ ፡ ጠናኝ ፡ ማሰኘት ፡ ነው ።

ወ ፡ ን ፡ ነ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ አንድ ፡ አርገህ ፡ ጠቅለህ ፡ ግዛ ።

267 በራብ ፡ መሞቴ ፡ ነው ፡ ችግር ፡ በዝቶብኝ ፤
—ቀለቤን ፡ መተማ ፡ አዛውረውብኝ ።  (ዘለ ፡ ቍ ፡ 87 ፡ 184) ፡

ሠ ፡ ቀለቤን ፡ ከመተማ ፡ እንድወስድ ፡ አደረጉብኝ ፡ ወደዚያ ፡ አዛወሩ
ብኝ ፡ እዚያ ፡ ደለደሉኝ ።

ወ ፡ «ቀለቤ» ፡ የሚባለውን ፡ ልጄን ፡ መተማ ፡ ገደሉት ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡
አስቀሩት ።

268 **በሬዬ ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ስፈልግ ፡ ስባጅ ፡**

**—እውነት ፡ ከጠፋማ ፡ አምላክ ፡ ይፍረድ ፡ እንጅ ።**

ሠ ፡ በሬዬ ፡ በርግጥ ፡ ከጠፋ ፡ ከታጣ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡እችላለሁ ፡ እን
ዴት ፡ እሆናለሁ ።

ወ ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ ከጠፋ ፡ አምላክ ፡ ይፍረድ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚበ
ጀውን ፡ ያድርግ ፡ የተሻለውን ፡ ያምጣ ።

269 **በርሻ ፡ ዕድሌን ፡ ላየው ፡ ሄጄ ፡ እናቴ ፡ አገር ፡**

**—ተመልሼ ፡ መጣሁ ፡ አጥቼ ፡ አንድም ፡ ዘር ።**

ሠ ፡ ለዘር ፡ የሚሆን ፡ እኽል ፡ አጣሁ ፡ የምዘራው ፡ የምበትነው ፡ ተቸግሬ ፡
መጣሁ ።

ወ ፡ ምንም ፡ ዘመድ ፡ አልቀረኝ ፡ ሁሉም ፡ አለቁ ፡ ወገኔ ፡ ተጫጠጠ ፡ ያለ
ዘር ፡ ቀረሁ ።

270 **በሰንሰለት ፡ ታስሮ ፡ ዓመት ፡ ታራት ፡ ወር ፡**

**—ምን ፡ ዋስ ፡ አገኘና ፡ ተፈታ ፡ ጐንደር ።** ( ዘለ. ቍ 277 ) ፡

ሠ ፡ ያለዋስ ፡ ከእስራት ፡ እንዴት ፡ ተፈታ ፡ ከወህኒ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ምን ፡
ተለቀቀ ።

ወ ፡ ጐንደር ፡ በጦርነት ፡ ጠፋ ፡ በረኃብ ፡ ተፈታ ፡ በጠላት ፡ እጅ ፡ ተበዘበዘ ።

271 **በሳን ፡ ውሃ ፡ ይገቼ ፡ ሳላስታጥብዎ ፡**

**—ፍትፍት ፡ እንደ ፡ ያዘ ፡ ታሰረ ፡ ጣትዎ ።**

ሠ ፡ ፍትፍት ፡ የያዙበት ፡ እጅዎን ፡ አልታጠቡም ፡ ከነወጡ ፡ ነዎት ።

ወ ፡ እየፈተፈተ ፡ የሚያጐርሥ ፡ ለጋስ ፡ እጅዎ ፡ ታሰረ ፡ ተገነዘ ።

272 **በሴት ፡ ስም ፡ ቢጠሩሽ ፡ ምን ፡ ያሳዝንሻል ፡**

**—ከወንዶች ፡ የላቀ ፡ አንቺም ፡ ሰው ፡ ገለሻል ።**

ሠ ፡ በሴት ፡ ስም፡ መጠራትሽ ፡ አይቈጭሽ ፡ አንቺም ፡ ከወንዶቹ ፡ የላቀ ፡ ስም ፡
ያለውን ፡ ታላቅ ፡ ሰው ፡ ገድለሻል ፡ ጀግንነትሽን ፡ አ ሳይተሻል ።

ወ ፡ ባንቺም ፡ ጦርነትም ፡ ( አንቺም ፡ አገር ) ። ብዙ ታላላቅ ፡ ሰዎች ፡ ሞተዋል ፡
ስመ ፡ ጥሩ ፡ የሆኑት ፡ መኳንንት ፡ አልቀዋል ።

273 **በስምንተኛው ፡ ሺሕ ፡ የለዎም ፡ ወዳጅ ፡**

**—ራስ ፡ ራስዎን ፡ ይጠብቁት ፡ እንጅ ።** ( ዘለ. ቍ 433 ) ፡

ሠ ፡ ለምን ፡ ሰውነትዎን ፡ አይጠብቁም ፡ ለሕይወትዎ ፡ አያስቡም ፡ ራስ
ዎን ፡ ይጥላሉ ።

(1) ራስ ጉግሣ ወሌ በንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ መንግሥት ጊዜ አምጠው በመጋቢት 22 / 1922 ዓ. ም ከሸዋ ጦር ጋራ ገጥመው አንቺም ላይ ሲዋጉ በጦርነቱ ውስጥ ስለ ሞቱ አዝማሪያቸው ከጀግናም ጀግና የሆነ ጌታዬ አንቺም ላይ ወደቀ በማለት ጌታውን ለማሞገስና ለማስታወስ የገጠመው ።

ወ ፡ የራስነት ፡ ሥልጣን ፡ ያለውን ፡ ሹመትዎን ፡ እንዳይከዱዎ ፡ ይጠብቁ ፤ አይዘንጉ ፤ ይጠንቀቁ ።

274 በስተልፍኙም ፡ በኩል ፡ ሲፈልግህ ፡ ዐይኔ ፤
—አዳራሽ ፡ ኖረሃል ፡ ለካስ ፡ መኰንኔ ። (ዘ ፡ ወ ፡ ጸ) ፡

ሠ ፡ እኔ ፡ ከእልፍኝ ፡ ስፈልግህ ፡ አንተ ፡ አዳራሽ ፡ ቆመህ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ከክፉ ፡ ቀን ፡ የምታወጣ ፡ ወደ ፡ ክብር ፡ ወደ ፡ ማዕርግ ፡ የምታደርስ ፤ ቸርነትህ ፡ ለሁሉ ፡ የሚደርስ ፡ ጌታ ፡ ሆነሃል ።

275 በስተሸዋ ፡ ዙሮ ፡ በስተትግሬ ፡ ዙሮ ፡
—አገኘ ፡ መሰለኝ ፡ ዐረፈ ፡ ዘንድሮ ።

ሠ ፡ አገር ፡ ላገር ፡ መዞሩን ፡ የተወው ፡ ዐርፎ ፡ የተቀመጠው ፡ አንድ ፡ ቦታ ፡ የረጋው ፡ የተመኘውን ፡ ቢያገኝ ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ ከመቸገር ፡ ዐረፈ ፤ ዕዳውን ፡ ጠቀለለ ፤ የማይቀረውን ፡ ሞት ፡ ሞተ ።

276 በስተወሎም ፡ በኩል ፡ በስተጉግሳም ፡ በኩል ፡ ሣሣብኝ ፡ ሌማቱ ፤
በስተዐመዴም ፡ በኩል ፡ ሣሣብኝ ፡ ሌማቱ ፤
—ጠፍታለች ፡ መሰለኝ ፡ እንጀራ ፡ ጣይቱ ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እንጀራ ፡ ዐዳይዋ ፡ መብል ፡ አቅራቢዋ ፡ አሳላፊዋ ፡ አልተገኘችም ፤ ጠፍታለች ፡ መሰለኝ ።

ወ ፡ እንጀራና ፡ ሀብት ፡ ሰጭዋ ፡ ትዳር ፡ አስፋፊዋ ፡ ንብረት ፡ አጕልማሿ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ዐረፈች ፤ ሞተች ።

277 በሸዋም ፡ በትግሬም ፡ በሌላውም ፡ ቦታ ፡
—እንደ ፡ ጐንደር ፡ አርጎ ፡ ማንም ፡ አልተፈታ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 270) ፡

ሠ ፡ እንደ ፡ ጐንደር ፡ የጕዞ ፡ ፍታት ፡ የተደረሰበት ፡ አይገኝም ።

ወ ፡ እንደ ፡ ጐንደር ፡ የጠፋ ፡ የተወረረ ፡ የተመዘበረ ፡ አገር ፡ የለም ።

278 በሸዋ ፡ በስሜን ፡ ብትወጣ ፡ ጣይቱ ፡
—ላንድ ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፡ ሞቀች ፡ ለፍጥረቱ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ጣይ ፡ ለሁሉም ፡ እኩል ፡ ትሞቃለች ፤ ድኻ ፡ ባለጸጋ ፡ ትልቅ ፡ ትንሽ ፡ አትለይም ።

ወ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ወገን ፡ ሳትለይ ፡ አገር ፡ ሳትከፍል ፡ ለመላ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መልካም ፡ ሥራ ፡ ሠራች ፤ ትንሽ ፡ ትልቁን ፡ በሀብት ፡ አነሣችው ፤ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገችው ።

279 በሹመት ፡ ቢበልጡኝ ፡ እንዴት ፡ በነደደኝ ፡ እንዴት ፡ በቈጨኝ ፤
—እነያም ፡ ጭቃ ፡ ናቸው ፡ እኔም ፡ ጭቃ ፡ ነኝ ።

ሠ ፡ በሹመት ፡ እኩል ፡ ሆነን ፡ በሥልጣን ፡ ሳንበላለጥ ፡ ቢንቁኝ ፡ አልቈጭም ፤ ሁላችንም ፡ ጭቃ ፡ ሹሞች ፡ ነን ፤ በክብር ፡ እንተናነስም ።

ወ ፡ ሁላችንም ፡ ሟቾች ፡ ነን ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ እንወርዳለን ፤ ጭቃ ፡ ዐፈር ፡ ትቢያ ፡ እንሆናለን ።

280 በቀንስ ፡ ይውላል ፡ ጣይ ፡ እየሞቀው ፤
—ባዳሩ ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ ሰው ፡ የተጐዳው ።

ሠ ፡ የአዳሩ ፡ ሁኔታ ፡ ያሳዝናል ፤ የሌሊት ፡ ልብስ ፡ የለውም ፤ ማታ ፡ ማታ ፡ ይቸገራል ።

ወ ፡ ሰዉ ፡ የተቸገረው ፡ በንብረቱ ፡ በትዳሩ ፡ ነው ፤ በኑሮው ፡ የተጐሳቈለ ፡ ነው ።

281 በቀን ፡ አያስቀምጥ ፡ ሌሊት ፡ አያስተኛ ፡ የዥማ ፡ ተባይ ፤
—በሉ ፡ አቃጥሉትና ፡ ሰው ፡ ይበል ፡ እፎይ ።

ሠ ፡ ለብልቡትና ፡ ሰዉ ፡ እፎይ ፡ ይበል ፤ አቃጥሉት ፡ እንድዱትና ፡ ሕዝቡ ፡ ዐርፎ ፡ ይተኛ ፤ ዕረፍት ፡ ያግኝ ።

ወ ፡ ወዲያ ፡ ግደሉትና ፡ ሰላም ፡ እናግኝ ፤ ከሥጋት ፡ ከሥቃይ ፡ እንረፍ ፤ ከመከራው ፡ እንዳን ።

282 በበጌምድር ፡ ጐዣም ፡ ተሻገር ፡ ያልከኝ ፡
—ስሜን ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ አኑረህልኝ ።

ሠ ፡ ስሜን ፡ የሚባለውን ፡ አገር ፡ ወደ ፡ ኋላ ፡ ትተህ ፡ ረስተህ ፡ ወዴት ፡ ትሄዳለህ ።

ወ ፡ መልካም ፡ የነበረውን ፡ ስሜን ፡ አጐደፍኸው ፤ አጠፋኸው ፤ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ስሜ ፡ እንዲበላሽ ፡ አደረግህ ።

283 በባላገር ፡ ነበር ፡ ኑሮስ ፡ የሚሻል ፤
—ከተማ ፡ ሰው ፡ ገብቶ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ ይሆናል ።

ሠ ፡ ሰው ፡ እከተማ ፡ ተገባ ፡ ይበላሻል ፤ ወስላታ ፡ ይሆናል ፤ ሁኔታው ፡ ሁሉ ፡ ይለወጣል ፤ አዲስ ፡ ዐመል ፡ ያወጣል ።

ወ ፡ መቃብር ፡ ከገቡ ፡ ወዲያ ፡ ሰው ፡ መባል ፡ አይቻልም ፤ ከሰው ፡ መልክ ፡ ይወጣል ፤ ወደ ፡ ዐፈርነት ፡ ይለወጣል ።

284 በባቡር ፡ ተጒዞ ፡ ምንድርነው ፡ ቅልውጡ ፤
—ግብጾች ፡ ለሐበሻ ፡ ደግሰው ፡ ላይሰጡ ። (1) (ማ ፡ ወ ፡ እ)፡

ሠ ፡ ወርደው ፡ ወጥተው ፡ አዘጋጅተው ፡ ለፍተው ፡ ደግሰው ፡ ግብጻውያን ፡ ለኢትዮጵያውያን ፡ አያበሉም ፤ አያጠጡም ፤ ጥሩ ፡ ጥሩውንም ፡ አያቀምሱም ።

ወ ፡ ግብረ ፡ ገብነት ፡ ያለው ፡ መልካም ፡ ጳጳስ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ግብጽ ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ላትልክ ፡ ልፋቱ ፡ ለምንድነው ።

285 በብዙ ፡ ለመግዛት ፡ ካሰብሁኝ ፡ በኋላ ፡
—መዝኜ ፡ መለስኩት ፡ ያን ፡ የሰው ፡ ገለባ ።

---

(1) የግብጽ ፡ ጳጳሳት ፡ ለሕዝቡ ፡ በማስተማር ፡ ረገድ ፡ ያደረጉልን ፡ ርዳታ ፡ ስለሌለ ፡ ከመምጣታቸው ፡ ይልቅ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ኢትዮጵያውያን ፡ ጳጳሳት ፡ እንዲኖሯት ፡ ይታሰብበት ፡ በማለት ፡ ቀደም ፡ ብሎ ፡ የተነገረ ።

ሠ ፡ ለክቼ ፡ መጠኑን ፡ ዐውቄ ፡ መለስሁት ፤ ክብደቱን ፡ መዝኜ ፡ ተረዳሁት ።

ወ ፡ ያንን ፡ ቀላል ፡ ሰው ፡ ገመትሁት ፤ ታዘብሁት ፤ ቅሌቱን ፡ ዐወቅሁበት ።

286 በተኰስ ፡ እንገባለን ፡ እያሉ ፡ ይላሉ ፤
—ስተው ፡ አያውቁም ፡ ወይ ፡ ሰዎችዎ ፡ ሁሉ ።

ሠ ፡ ሰዎችዎ ፡ ሁሉ ፡ እንገባለን ፡ እያሉ ፡ የሚፎክሩት ፡ እስከዚህ ፡ ተኳሾች ፡ ናቸውን ፤ መሳት ፡ አያውቁምን ።

ወ ፡ አሽከሮችዎ ፡ ሁሉ ፡ ጭፍሮችዎ ፡ ይሉኝታ ፡ የላቸውም ፤ ስፈራ ፡ ከነገር ፡ ስሸሽ ፡ ጠቡን ፡ አዎ‌ባጓሮውን ፡ ስተው ፡ አያውቁም ፤ አይረዱምን ።

287 በተድላ ፡ በጐሹ ፡ ያልነበረ ፡ ነገር ፡
—በከርሠ ፡ መቃብር ፡ ካቡን ፡ መነጋገር ። (1)

ሠ ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ከጳጳስ ፡ ጋራ ፡ መነጋገር ፡ ከአቡን ፡ ጋራ ፡ መጨዋወት ፡ ይቻላልን ።

ወ ፡ በሬሳ ፡ መቃብር ፡ ላይ ፡ ከተገነባው ፡ ካብ ፡ ጋራ ፡ መኖር ፡ ከግንብ ፡ በታች ፡ መዋል ።

288 በታላቅ ፡ ሽልቻ ፡ ተሸክሜ ፡ ዐፈር ፡
—ማረፊያው ፡ ጠፍቶብኝ ፡ አለሁኝ ፡ ስዞር ።

ሠ ፡ ማረፊያው ፡ ጠፍቶብኝ ፡ እዞራለሁ ፤ እንከራተታለሁ ፤ እለፋለሁ ።

ወ ፡ የምሞትበትን ፡ ጊዜ ፡ ባለማወቄ ፡ ሥጋን ፡ ለብሼ ፡ እጨነቃለሁ ፤ ለሚቀረው ፡ ዓለም ፡ እወጣለሁ ፤ እወርዳለሁ ።

289 በታንኳ ፡ በመርከብ ፡ ሲገቡ ፡ ብታይ ፡
—እረ ፡ አባይን ፡ በግር ፡ ትገባለህ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ የአባይን ፡ ባሕር ፡ በቁም ፡ በእግር ፡ ለመሻገር ፡ ትችላለህ ፡ ወይ ፤ በደረት ፡ ማቋረጥ ፡ ይሆንልሃል ፡ ወይ ።

ወ ፡ ረኃብ ፡ ሆይ ፡ ከሆድ ፡ በቀር ፡ በዐይንና ፡ በእግር ፡ ገብተህ ፡ በሰውነት ፡ ተሠራጭተህ ፡ ታደክማለህን ።

290 በትግሬ ፡ በጐንደር ፡ የተጣለው ፡ ጠጅ ፡
—እኔ ፡ ተጠጥቷል ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ መጠጡ ፡ ተጠጥቶ ፡ ያለቀ ፡ እንጂ ፡ ያለ ፡ አልመሰለኝም ፡ ነበር ፤ እንደ ፡ ተረፈ ፡ አላወቅሁም ።

ወ ፡ በነገሩ ፡ ያዘነ ፡ የተጸጸተ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፤ እንዳቃለለው ፡ እንደ ፡ ተወው ፡ አላወቅሁም ፡ ነበር ።

---

(1) ጳጳሱ ፡ አቡነ ፡ ሉቃስ ፡ አስቀድሞ ፡ በተቀበሩበት ፡ መቃብር ፡ አጠገብ ፡ አባታቸው ፡ ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ስለ ፡ ተቀበሩ ፡ ልጃቸው ፡ ራስ ፡ ኀይሉ ፡ ያለቀሱት ።

291 በችግር ፡ ላይ ፡ ሲኖር ፡ በዝቶ ፡ ድኽነቱ ፡
—መቼ ፡ ከበረና ፡ ዠማ ፡ ሆነ ፡ ቤቱ ።

ሠ ፡ ከመቼ ፡ ወዲህ ፡ ከበረና ፡ እንዲህ ፡ በለጸገ ፤ ቤቱ ፡ ንብረቱ ፡ መላ ፤ ሀብቱ ፡ ተትረፈረፈ ፤ እንደ ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ዠማ ፡ የሚባለው ፡ ወንዝ ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ ወሰደው ።

292 በንጉሡ ፡ በጨጌው ፡ ባቡኑ ፡ ቅስና ፡
—አይዞህ ፡ ጐዣም ፡ ሙተው ፡ ትፈታለህና ።

ሠ ፡ ብትሞትም ፡ ንጉሡ ፡ ባሉበት ፡ ዕጨጌውና ፡ አቡኑ ፡ ጸሎተ ፡ ፍትሐቱን ፡ ያደርሱልሃል ፤ በወግ ፡ በማዕርግ ፡ ትቀበራለህ ።

ወ ፡ አይዞህ ፡ ጐዣም ፡ በርታ ፡ ጠንክር ፤ ትሰንፍና ፡ ትፈታለህ ፤ ድል ፡ ትሆናለህ ።

293 በዕድሜ ፡ ይበልጥሻል ፡ የሚለኝ ፡ ሰው ፡ ማነው ፤
—ፊታውራሪ ፡ ቸኰል ፡ ባልንጀራዬ ፡ ነው ።

ሠ ፡ እኩያዬ ፡ ጓደኛዬ ፡ እቻዬ ፡ ነው ፤ አንበላለጥም ።

ወ ፡ ፊታውራሪ ፡ ቸኰል ፡ ባሌ ፡ ትዳሬ ፡ ንብረቴ ፡ ነው ፤ እንጀራዬ ፡ ሀብቴ ፡ እሱ ፡ ነው ።

294 በዚህ ፡ እጽፋለሁ ፡ አለኝ ፡ ብረት ፡ ብር ፤
—እንዳታመጡብኝ ፡ ያንን ፡ መቃ ፡ ብር ።

ሠ ፡ ከመቃ ፡ የተቀረጸ ፡ ብር ፡ አልፈልግም ፤ በሱ ፡ አልጽፍም ።

ወ ፡ ያለጊዜ ፡ መሞት ፡ ርደተ ፡ መቃብር ፡ እንዳይመጣብኝ ፡ እፈራለሁ ፤ ይህ ፡ እንዳይደርስብኝ ፡ እሠጋለሁ ።

295 በዛብህ ፡ አገሩ ፡ ስለ ፡ ናፈቀው ፤
—አፍቀራ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ ዳሞትን ፡ አየው ።

ሠ ፡ አፍቀራ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ አገሩን ፡ ዳሞትን ፡ አየው ፤ ተመለከተው ።

ወ ፡ በዛብህ ፡ አፍቀራ ፡ ላይ ፡ በግዞት ፡ ሆኖ ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ ዐረፈ ።

296 በደጅ ፡ ሰላሙ ፡ አትገቡም ፡ ምነው ፤
በመቃብር ፡ እኩል ፡ ይኸ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ለምን ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ በደጅ ፡ ሰላም ፡ በኩል ፡ ይሄዳል ፤ በመቃብር ፡ ቤቱ ፡ በኩል ፡ አይተላለፍም ።

ወ ፡ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ትልቅም ፡ ትንሽም ፡ ቢሆን ፡ በመቃብር ፡ እኩል፡ ነው ፤ ልዩነት ፡ የለውም ።

297 በዳሞት ፡ ተልኳል ፡ ጥናው ፡ ሊመጣ ፡ ነው ፤
በሜጫ ፡ ተልኳል ፡ ጥናው ፡ ሊመጣ ፡ ነው ፤
—ተድላ ፡ ጓሉ ፡ ሞቶ ፡ ጐዣም ፡ ሊፈታ ፡ ነው ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 397) ፡

ሠ ፡ ፍትሐቱ ፡ ሥርዐተ ፡ ቀብሩ ፡ በጐዣም ፡ ሊሆን ፡ ነው ።

ወ ፡ በተድላ ፡ ጓሉ ፡ ሞት ፡ ጐዣም ፡ ሊጐዳ ፡ ሊበደል ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሊያጣ ፡ ነው ።

298 በገና ፡ በጥምቀት ፡ አልልህም ፡ ጠጅ ፤
—ኋላ ፡ በትንሣኤ ፡ አትበድለኝ ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ የፋሲካ ፡ ለት ፡ ጠጅ ፡ እንዳትከለክለኝ ፤ እንዳትነፍገኝ ፤ እንዳትነሣኝ ።

ወ ፡ በዕለተ ፡ ምጽአት ፡ እንዳትበድለኝ ፤ በግራ ፡ እንዳታቆመኝ ፡ ከኀጢአተኞች ፡ ቍጥር ፡ እንዳታገባኝ ።

299 በገና ፡ አስመጣና ፡ በል ፡ ደርድርልኝ ፤
—እንዴት ፡ ስሜ ፡ ጠፋህ ፡ እኔ ፡ እያለሁኝ ።　　(ዘለ ፡ ቍ ፡ 826) ፡
(ራስ ፡ ዐ) ፡

ሠ ፡ ስሜን ፡ እንዴት ፡ ዛነጋሽው ፤ እንዴት ፡ ጠፋህ ፤ እንዴትስ ፡ ተረሳህ ።
ወ ፡ ገና ፡ በሕይወት ፡ ሳለሁ ፡ አገሬ ፡ ስሜን ፡ እንዴት ፡ ይዋረድ ።

300 በገና ፡ ገዝቶ ፡ ነው ፡ ለልጁ ፡ ያቈየው ፤
—እየደረደረ ፡ መኰንን ፡ የቃኘው ።

ሠ ፡ መኰንን ፡ ገና ፡ ለሚወልደው ፡ ልጅ ፡ በገና ፡ ገዝቶ ፡ አስቀመጠለት ።

ወ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ ገና ፡ በደኅንነታቸው ፡ ሳሉ ፡ የሠሩት ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ዘር ፡ አወጣላቸው ።

301 በገዛ ፡ አገራችን ፡ በገዛ ፡ ወንዛችን ፡
—በሉ ፡ እጠቡንና ፡ እንግባ ፡ እቤታችን ።

ሠ ፡ እጠቡን ፤ ለቃልቁን ፤ አጽዱንና ፡ እቤታችን ፡ እንግባ ።

ወ ፡ ዝረፉን ፤ በዝብዙን ፤ ንጠቁንና ፡ ባዶ ፡ እጃችንን ፡ እንሂድ ፤ መቼስ ፡ ምን ፡ ይደረግ ።

302 በጊዜ ፡ ውሰደኝ ፡ ሳትገባ ፡ ፀሓይ ፤
—የማይቀር ፡ ሰው ፡ ሊያመሽ ፡ ይገባዋል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ሀያጅ ፡ ሰው ፡ ሊያመሽ ፡ መቼ ፡ ይገባዋል ፤ በጊዜ ፡ መሄድ ፡ አለበት ።

ወ ፡ ቢሸኝ ፡ ከሞት ፡ የማይቀር ፡ ሰው ፡ በእርጅና ፡ በችግር ፡ ከሚሠቃይ ፡ በጊዜ ፡ በዕድሜው ፡ ቢሞት ፡ አይሻልምን ።

303 በግና ፡ ፍየሉ ፡ እያለ ፡ ቤትህ ፡
—ምነው ፡ በፋሲካ ፡ ዐዞ ፡ የበላህ ።

ሠ ፡ በፋሲካ ፡ ምድር ፡ ከዐዞ ፡ ከሳማ ፡ የተሠራ ፡ ወጥ ፡ ለምን ፡ በላህ ፤ ለምን ፡ በዚህ ፡ ጾምህን ፡ ፈታህ ።

ወ ፡ በትንሣኤ ፡ ምድር ፡ እንዴት ፡ ዐዞ ፡ ይብላህ ፤ ይውሰድህ ።

304 በጎ ፡ ምክር ፡ መከረው ፡ ክፉን ፡ የሚያስጥሉ ፡
ያርባ ፡ አራቱ ፡ ደብር ፡ ሊቃውንት ፡ እያሉ ፡
—ጐንደር ፡ ተበሳጭቶ ፡ በጣም ፡ ነዷል ፡ አሉ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 1098 ) ፡

ሠ ፡ የጐንደር ፡ ሕዝብ ፡ ተናዷል ፡ ተበሳጭቷል ፡ አሉ ።

ወ ፡ ጐንደር ፡ በእሳት ፡ ተቃጥሏል ፡ ጠፍቷል ፡ አሉ ።

305 በጎች ፡ በመጠበቅ ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ፡
—በሥጋት ፡ ሞተብኝ ፡ ኀይለ ፡ መለኮት ። (1)

ሠ ፡ በማሰብ ፡ በመሥጋት ፡ ሰውነቱ ፡ አለቀ ፤ ዐቅሙ ፡ ደከመብኝ ።

ወ ፡ የሥጋዬ ፡ ቍራጭ ፡ ያጥንቴ ፡ ፍላጭ ፡ የሆነው ፡ ወንድሜ ፡ ሞተብኝ ።

306 በጐዣም ፡ ያካፋል ፡ በሸዋ ፡ ፀሓይ ፤
—በጐንደር ፡ ደመና ፡ መቅረቱ ፡ ነወይ ።

ሠ ፡ በጐንደር ፡ ደመና ፡ ሆኖ ፡ ሳይዘንብ ፡ ቀረ ፤ ደመናው ፡ በሰማይ ፡ ተን ቀዋሎ ፡ ተመለሰ ።

ወ ፡ በጐንደር ፡ ንጹሕ ፡ ደም ፡ እንደ ፡ ፈሰሰ ፡ መቅረቱ ፡ ነው ፤ የሰው ፡ ደም ፡ የሚበቀል ፡ መታጣቱ ፡ ነውን ።

307 በጐዣም ፡ በትግሬ ፡ የነበረ ፡ ላም ፡
—ተሰባብሮ ፡ ቀረ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ቀንዳም ።

ሠ ፡ የቀንድ ፡ ከብቱ ፡ ሁሉ ፡ አለቀ ፤ በሬው ፡ ላሙ ፡ ገደል ፡ ገባ ።

ወ ፡ አገር ፡ አዋይ ፡ ያገር ፡ ቀንድ ፡ የነበረው ፡ ሽማግሌ ፡ ሁሉ ፡ አለቀ ፤ ባገሩ ፡ ውስጥ ፡ ጨዋ ፡ ሰው ፡ ጠፋ ።

308 በጣሙን ፡ አዝነዋል ፡ የሰሙቱ ፡ ሁሉ ፡
—በይ ፡ ደግሰው ፡ ጠፍቶ ፡ እንዲያው ፡ ቀረ ፡ ቢሉ ።

ሠ ፡ የተደገሰውን ፡ የሚበላ ፡ የሚጠጣ ፡ ጠፍቶ ፡ ግብዣው ፡ ስለ ፡ ተበ ላሸ ፡ አዝነዋል ።

ወ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ በዓለም ፡ ላይ ፡ አልተገኘም ፤ ቅን ፡ ሰው ፡ ጠፋ ።

309 በጣም ፡ ሰፋ ፡ ብሎ ፡ ይሠራ ፡ ቤታችን ፤
—ማዘኑ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሞልቷል ፡ ባገራችን ።

ሠ ፡ ማእዘን ፡ ዕንጨት ፡ በብዛት ፡ ይገኛል ፤ ባገራችን ፡ አይቸግርም ።

ወ ፡ ማዘን ፡ መራራት ፡ ባገራችን ፡ ተርፏል ፡ መተዛዘን ፡ አለ ፤ አንጨ ካከንም ።

310 በጣም ፡ ቈይቻለሁ ፡ ከወጣሁ ፡ ሰምቼ ፤
—ገና ፡ ዛሬ ፡ መጣሁ ፡ ጕዳዬን ፡ ከትቼ ።

---

(1) ንጉሥ ፡ ኀይለ ፡ መለኮት ፡ ባረፉ ፡ ጊዜ ፡ እህታቸው ፡ ወይዘሮ ፡ ትደነቂያለሽ ፡ ጥልቅና ፡ መሪር ፡ የሆነ ፡ ሐዘናቸውን ፡ የገለጹበት ።

ሠ ፡ ሥራዬን ፡ አጠናቅቄ ፡ ጕዳዬን ፡ ፈጽሜ ፡ መጣሁ ።
ወ ፡ አቶ ፡ «ጕዳዬን» ፡ ቀብሬ ፡ ግብአተ ፡ መሬት ፡ አድርጌ ፡ ተመለስሁ ፤ አስቀብሬ ፡ መጣሁ ።

311 በጣም ፡ ተደነቅሁኝ ፡ ስትሠራው ፡ ባይ ፤
—ለካ ፡ ይህ ፡ ገላችን ፡ ዐፈር ፡ ኖሯል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ገል ፡ (ሸክላ) ፡ ካፈር ፡ የሚሠራ ፡ ኖሯል ።
ወ ፡ ይህ ፡ ገላችን ፡ ሰውነታችን ፡ ዐፈር ፡ የሚሆን ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ኖሯል ።

312 በጣም ፡ አዝኛለሁ ፡ ጕዳት ፡ በዝቶብኝ ፤
—የዘራሁት ፡ ሁሉ ፡ ጠፋ ፡ ብለውኝ ።

ሠ ፡ አዝመራህ ፡ ጠፋ ፡ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ፡ ብለውኝ ፡ በጣም ፡ አዝኛለሁ ።
ወ ፡ የወለድሁት ፡ አልተባረከልኝም ፤ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ አልደረሰም ፤ በልጅነቱ ፡ ሞተ ።

313 በጣም ፡ ኮምጧለ ፡ ደርቋለ ፡ ጠጃችሁ ፤
—ተማሩ ፡ ጨምሩ ፡ ልጆች ፡ እባካችሁ ።

ሠ ፡ ጠጁ ፡ ኮምጧል ፡ ማር ፡ አልሱት ።
ወ ፡ በጣም ፡ ተማሩ ፤ አጥኑ ፤ በርቱ ፤ በዕውቀት ፡ ግፉ ፤ በአእምሮ ፡ ጠን ክሩ ።

314 በጦር ፡ ማን ፡ ያኸለዋል ፡ የሀገሬን ፡ ልጅ ፤
—ባንድ ፡ አልሆንም ፡ ብሎ ፡ ተበታተነ ፡ እንጅ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ ፡)

ሠ ፡ አንድ ፡ አልሆንም ፡ አልተባበርም ፡ ብሎ ፡ ተበታተነ ።
ወ ፡ ባንዳ ፡ የጠላት ፡ ጭፍራ ፡ አልሆንም ፡ አለ ፤ የጠላት ፡ ወታደር ፡ መሆንን ፡ ጠላ ፤ የፋሽስት ፡ አገልጋይ ፡ ለመሆን ፡ አልፈቀደም ።

315 በጨለማ ፡ መሄድ ፡ ያገባል ፡ ከፈፋ ፤
—አሉላ ፡ ደግ ፡ ሄደ ፡ ጣይቱ ፡ ሳትጠፋ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 362፡ 640)፡

ሠ ፡ ያገሬ ፡ ልጅ ፡ የአንድነት ፡ ኃይል ፡ ነው ፡ የሚለውን ፡ ምሳሌ ፡ ዘንግቶ ፡
ሠ ፡ ተበተነ ፡ እንጂ ፡ ጀግንነት ፡ መች ፡ አነሰው ፡ ነበር ።
ጠልቅ ፡ እቤቱ ፡ ገባ ።
ወ ፡ ራስ ፡ አሉላ ፡ ከእቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ቀድሞ ፡ ሞተ ፤ በወግ ፡ በማዕርግ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ባሉበት ፡ ዘመን ፡ ተቀበረ ፤ በመልካም ፡ ተሸኘ ።

316 በፈረሰኛውም ፡ ፈረሰኛ ፡ አለበት ፤
—በደርሰህ ፡ ውብሸት ፡ በላይ ፡ ደረሰበት ።

ሠ ፡ ፈረሰኛውን ፡ ፈረሰኛ ፡ ቀደመው ፤ ለሁሉም ፡ የበላይ ፡ አለው ።
ወ ፡ ደርሰህን ፡ በላይ ፡ ደረሰበት ፡ በኀይልም ፡ ሊደመስሰው ፡ ታጥቆ ፡ መጣበት ።

317 ቢላዋዬን ፡ ስዬ ፡ እጠብቅሃለሁ ፤
—ሥጋ ፡ አምላክ ፡ ብትሰጠኝ ፡ እበላበታለሁ ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ብትሰጠኝ ፡ ለመብላት ፡ ቢላዋዬን ፡ ስዬ ፡ እጠባበቃለሁ ።
ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ ሥጋህን ፡ ለመቀበል ፡ እንድታበቃኝ ፡ ተዘጋጅቼ ፡ እጠባበቃለሁ ።

318 ቢሸከም ፡ አይከብደው ፡ የለበት ፡ ድካም ፤
—እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ራስ ፡ እኔ ፡ አላየሁም ።

ሠ ፡ ብርቱና ፡ ጠንካራ ፡ የሆነ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ራስ ፡ አላየሁም ፤ ቢሸ ከም ፡ አይከብደውም ፤ አይዝለፈለፍም ።
ወ ፡ የማስተዳደር ፡ ችሎታ ፡ ያለው ፡ ደጎና ፡ ገገር ፡ እንደ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ተፈሪ ፡ ያለ ፡ አይገኝም ፤ ራስ ፡ አገዛዝ ፡ ያውቃሉ ።

319 ቢነግሩት ፡ አይሰማ ፡ የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፤
—እስቲ ፡ ማን ፡ ይመስላል ፡ ዘውዴ ፡ የለበሰው ።

ሠ ፡ ዘውዴ ፡ የለበሰው ፡ የማን ፡ ልብስ ፡ ይመስላል ፤ የሱን ፡ ዐይነት ፡ ልብስ ፡ የሚለብስ ፡ ማነው ።
ወ ፡ ዘውድ ፡ የጫነው ፡ ማነው ፡ ነጋሢው ፡ ማን ፡ ይባላል ።

320 ቢወጡም ፡ ቢወርዱም ፡ ቢዞሩም ፡ በዓለም ፡
—እንደ ፡ ባልንጀራ ፡ የሚስማማ ፡ የለም ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ጓደኛ ፡ እንደ ፡ ባልንጀራ ፡ የሚስማማ ፡ የለም ፤ በጓደኛና ፡ በ ባልንጀራ ፡ መካከል ፡ በቀላሉ ፡ መግባባት ፡ ይገኛል ።
ወ ፡ (2) ሀብት ፡ እንዳለው ፡ እንደ ፡ ጌታ ፡ ሁሉ ፡ የሚስማማው ፡ የለም ።
ወ ፡ (1) እንደባል ፡ ቤት ፡ የሚመች ፡ የለም ፤ ስጋትና ፡ መሰቀቅ ፡ የለበትም ።

321 ቢገዛን ፡ በጠላሁ ፡ የራስ ፡ ኀይሉ ፡ ልጅ ፤
—የኋላውን ፡ ካሳ ፡ ብፈራ ፡ ነው ፡ እንጂ ።

ሠ ፡ በኋላ ፡ ካሳ ፡ መክፈልን ፡ ብፈራ ፡ ነው ፤ መቀጮ ፡ መግባባትን ፡ ባል ፈቅድ ፡ ነው ።
ወ ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ የተገዛሁት ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ካሳ ፡ የሚባለው ፡ ይመጣና ፡ ያጠቃኛል ፡ ብዬ ፡ ብፈራ ፡ ነው ።

322 ቢጮኸው ፡ ቢያነባው ፡ ስላልጠቀመው ፡
—ድኾ ፡ በጉልበቱ ፡ ነው ፡ ያለቀሰው ።

ሠ ፡ እየተንፏቀቀ ፡ እየወደቀ ፡ እየተነሣ ፡ ነው ፡ ያለቀሰው ፤ ተንበርክኮ ፡ ነው ፡ ሲያነባው ፡ የዋለው ።
ወ ፡ ድኻ ፡ የሚያዝነው ፡ የሚያለቅሰው ፡ በከንቱ ፡ ስለሚያልቀው ፡ ያለ ዋጋ ፡ ስለሚቀረው ፡ ጉልበቱ ፡ ነው ።

323 ባሁኑ ፡ ጦርነት ፡ ማንም ፡ ማን ፡ አይኩራ ፤
—ኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ ነው ፡ ይኸንን ፡ የሠራ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ይህ ፡ የሆነው ፡ በሥላሴ ፡ ኀይል ፡ ነው ፤ የአጋዕዝተ ፡ ዓለም ፡ ሥራ ፡ ነው ።
ወ ፡ ነጻነት ፡ የተገኘው ፡ በግ ፡ ቀ ፡ ኃ ፡ ሥላሴ ፡ ብርታትና ፡ ትጋት ፡ ነው ።

324 ባላባት ፡ መሆኑን ፡ እናውቀውም ፡ እኛ ፤
—መቱማ ፡ ላይ ፡ ኗሪ ፡ ይኸን ፡ ወሰንተኛ ።

ሠ ፡ ወሰን ፡ ተፋላሚ ፡ ዳር ፡ ድንበር ፡ ተቈጣጣሪ ፡ ክልል ፡ ተመልካች ፡ ነው ።

ወ ፡ ከወሰን ፡ ላይ ፡ የሞተ ፡ ላገሩ ፡ ሲል ፡ ሕይወቱን ፡ የሠዋ ፡ ሰው ፡ ነው።

325 ባልሻሪው ፡ ቢሠራ ፡ በዶማ ፡ ባካፋ ፡
—የዘሩትም ፡ ቀረ ፡ አልበቀለም ፡ ጠፋ ።

ሠ ፡ የዘሩት ፡ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ፤ ሳይበቅል ፡ ዘር ፡ ሳይሰጥ ፡ ቀረ ፤ ጠፋ ።

ወ ፡ ጠላት ፡ ሕዝቡን ፡ በዶማና ፡ ባካፋ ፡ ቢፈጀውም ፡ እጅግ ፡ አልተጠቀመም ፤ ያሰበውም ፡ አልሆነም ።

326 ባልሽ ፡ ቢለምንሽ ፡ ይዞ ፡ ገላጋይ ፡
—ዓለም ፡ በቃኝ ፡ ብለሽ ፡ ትሄጃለሽ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ዓለምን ፡ ንቀሽ ፡ በምናኔ ፡ ትሄጃለሽን ፤ ተድላና ፡ ደስታ ፡ በቃሽን ።

ወ ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ መለየትሽ ፡ ነውን ።

327 ባልሽ ፡ ወዴት ፡ ሄደ ፡ ብለን ፡ ብንጠይቃት ፡ ስለ ፡ ጕዳያችን ፡
—ተሰብሮ ፡ አሁን ፡ መጥቶ ፡ ተኝቷል ፡ አለችን ።

ሠ ፡ ሰብሮ ፡ ከሚባል ፡ ቦታ ፡ መጥቶ ፡ ተኝቷል ፤ አሸልቦታል ፤ ደክሞታል ፡ አለችን ።

ወ ፡ ወድቆ ፡ ዐጥንቱ ፡ ደቆ ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ ይገኛል ፤ ተሰብሮ ፡ ተኝቷል አለችን ።

328 ባልቆም ፡ ይሻለኛል ፡ ብሄድ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፤
—ያ ፡ የተማመንኩት ፡ ከጠፋብኝ ፡ በቅሎ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ልጭነው ፡ ያሰብሁት ፡ በቅሎ ፡ ከጠፋብኝ ፡ በጊዜ ፡ ላዝግም ።

ወ ፡ ይጦረኛል ፡ ይቀብረኛል ፡ ብዬ ፡ የተማመንኩበትና ፡ የተመካሁበት ፡ ልጄ ፡ እንዲህ ፡ ሆኖ ፡ ከተሰናከለ ፡ ባልቆም ፡ ይሻለኛል ።

329 ባልጋ ፡ ተቀምጬ ፡ ምድሩ ፡ ይርቀኛል ፤
—መውረድ ፡ እያለብኝ ፡ ምን ፡ ያስጨንቀኛል ።

ሠ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በአልጋ ፡ ላይ ፡ አልኖርም ፤ እመሬት ፡ እወርዳለሁ ።

ወ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ሞቼ ፡ እመቃብር ፡ እገባለሁ ።

330 ባሏን ፡ ብንጠይቃት ፡ የት ፡ ሄደ ፡ ብለን ፡
— የሥጋ ፡ ዕዳ ፡ አብሮት ፡ ጠፍቷል ፡ አለችን ።

ሠ ፡ በዱቤ ፡ ሥጋ ፡ እየገዛ ፡ የበላበት ፡ ዕዳ ፡ ስለ ፡ በረከተበት ፡ ካገር ፡ ወጥቷል ፤ ዕዳ ፡ አብሮታል ፡ አለችን ።

ወ ፡ የማይቀር ፡ ሞት ፡ ይዞት ፡ ሄዷል ፤ እመቃብር ፡ ገብቷል ።

331 ባሰላው ፡ ባሰላው ፡ እንቢ ፡ አለኝ ፡ እንዝርቱ ፤
— ከታችም ፡ አይደለ ፡ ከላይ ፡ ነው ፡ ጥመቱ ።

ሠ ፡ የእንዝርቱ ፡ ጥመት ፡ ከአናቱ ፡ ከራሱ ፡ በኩል ፡ ነው ።

ወ ፡ የኔ ፡ መጉላላት ፡ መቸገር ፡ ከሰው ፡ በታች ፡ መሆን ፡ በሰው ፡ ተን ኰል ፡ አይደለም ፤ የአምላክ ፡ መልካም ፡ ፈቃድ ፡ ሳይጨመርበት ፡ ቢቀር ፡ ነው ።

332 ባባ ፡ ፈንዞ ፡ ጠምሩ ፡ በመንገሻ ፡ ጠምሩ ፡ ወትሮ ፡ የጐዳኝ ፡
—ተመልሶ ፡ መጣ ፡ መግቢያ ፡ ሊያሳጣኝ ።

ሠ ፡ ሊያስጨንቀኝ ፡ ሊያስጠብበኝ ፡ ሊያስቸግረኝ ፡ ዳግም ፡ መጣብኝ ።

ወ ፡ ያለፈው ፡ አንሶ ፡ አሁን ፡ ደግሞ ፡ መጠጊያ ፡ መሸሸጊያ ፡ ዘመድ ፡ ሊያሳጣኝ ፡ ነው ።

333 ባገር ፡ ቤት ፡ ገበያ ፡ ከመንከራተት ፡
—ከተማ ፡ ይሻላል ፡ ልብስ ፡ ለመግዛት ።

ሠ ፡ አሮጌ ፡ እላቂ ፡ ልብስ ፡ ለመግዛት ፡ ከተማ ፡ ይሻላል ፤ እዚያ ፡ ይረከ ሳል ።

ወ ፡ እከተማ ፡ በመኖር ፡ ልባም ፡ ብልኀ ፡ ይኮናል ፤ አስተዋይ ፡ ሰውነት ፡ ይገኛል ፤ ማመዛዘን ፡ ይፈጠራል ።

334 ባፈር ፡ ላይ ፡ ተዘርቶ ፡ እየታየ ፡ ባይን ፡
—አይለቀምም ፡ ወይ ፡ የወደቀ ፡ ዕጣን ።

ሠ ፡ የፈሰሰ ፡ ዕጣን ፡ አይለቀምም ፡ ወይ ፤ ለምን ፡ ዝም ፡ ይባላል ፤ አይነ ማምን ።

ወ ፡ ሕፃንም ፡ ሽማግሌም ፡ ከሞት ፡ አይመለስም ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ካረፈ ፡ ተስፋ ፡ የለውም ፡ ወይ ።

335 ቤቱ ፡ ክሲያን ፡ አትግባ ፡ ዘውዴ ፡ አለብዩን ፡
—ሚስትህ ፡ ከወለደች ፡ አንተማ ፡ ራስ ፡ ሁን ። (1)

ሠ ፡ እንደሚስትህ ፡ እመቤት ፡ ሁን ፤ በአራስነት ፡ ተቀመጥ ፤ አዲስ ፡ የወ ለደችውን ፡ ሴትህን ፡ ምሰል ።

ወ ፡ አንተም ፡ የራስነት ፡ ማዕርግ ፡ ይኑርህ ፤ የራስነትን ፡ክብር ፡ አግኝ ።

336 ቤቱን ፡ በሸንበቆ ፡ የሚሠራ ፡ ማነው ፤
—ላወቀውማ ፡ ሰው ፡ ያገዳም ፡ መልካም ፡ ነው ።

ሠ ፡ የአገዳ ፡ ቤት ፡ ደኅና ፡ ነው ፤ ምንም ፡ አይል ፡ አይከፋም ።

ወ ፡ የገዳም ፡ ኑሮ ፡ ጥሩ ፡ ነው ፤ ንዝንዝ ፡ ጭቅጭቅ ፡ የለበትም ፤ ለነፍስ ፡ ይበጃል ።

(1) ደጃች ፡ ዘውዴ ፡ ከራስ ፡ ኀይሉ ፡ ልጅ ፡ ከወይዘሮ ፡ ድንቅነሽ ፡ ደጃች ፡ ጐሹን ፡ በወ ለዱ ፡ ጊዜ ፡ የተገጠመ ።

337 ቤታችን ፡ ቢሰወር ፡ ከንግዳ ፡ ይተርፋል ፤
—ቢመሽ ፡ ከኛ ፡ አደረ ፡ ነገም ፡ በናንት ፡ ያልፋል ።

ሠ ፡ እንግዳው ፡ ዛሬ ፡ ከኛ ፡ ቤት ፡ አደረ ፤ ቢመሽ ፡ እዚሁ ፡ ሰፈረ ፤ ነገ ፡ በናንተ ፡ በኩል ፡ ይሄዳል ፤ በዚያ ፡ አድርጎ ፡ ያልፋል ።

ወ ፡ በኛ ፡ ያለ ፡ ችግር ፡ በናንተም ፡ ይደርሳል ፤ ይመጣል ፤ ሀብትና ፡ ጌትነት ፡ ያልፋል ፤ ተለዋዋጭ ፡ ነው ።

338 ቤት ፡ እሠራ ፡ ብዬ ፡ ተሣነኝ ፡ ጕልበቴ ፤
—አለማገር ፡ ቀረች ፡ ዋ ፡ ቤቴ ፡ ዋ ፡ ቤቴ ።

ሠ ፡ ቤቷ ፡ ሳትማገር ፡ ግድግዳዋ ፡ ሳይያያዝ ፡ ሳይጠብቅ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚታይባት ፡ ያች ፡ ለም ፡ ፍሬያማ ፡ አገር ፡ ቀረች ፤ አልተገኘችም ።

339 ብለምነው ፡ ጐንደር ፡ ውሃ ፡ እንዲያጠጣኝ ፡
—እኔም ፡ ውሃ ፡ ጠምቶኝ ፡ ተቃጠልኩ ፡ አለኝ ።

ሠ ፡ ውሃ ፡ ጠምቶኝ ፡ ምላሴ ፡ ደረቀ ፡ አንደበቴ ፡ ተሳሰረ ፡ አለኝ ።

ወ ፡ ጐንደር ፡ ነደደ ፤ ተቃጠለ ፤ ጠፋ ፤ ተበዘበዘ ።

340 ብላጨው ፡ አመመኝ ፤ ብሠራው ፡ ከፋኝ ፤
—አንድ ፡ ራሴ ፡ እኮ ፡ ነው ፡ የሚያስቸግረኝ ።

ሠ ፡ ራሴ ፡ አስቸገረኝ ፤ ጕተና ፡ ሳደርገው ፡ ያስከፋል ፤ ስላጨው ፡ ያመኛል ፤ ይበርደኛል ።

ወ ፡ አንድ ፡ ራሴን ፡ መቻል ፡ አቃተኝ ፤ የምጥረው ፡ የምግረው ፡ ላንድ ፡ ራሴ ፡ ነው ፤ ድካሜ ፡ ለግሌ ፡ ነው ።

341 ብልኅ ፡ ነው ፡ ስትሉኝ ፡ እዩት ፡ ሞኝነቴን ፤
—ራሴ ፡ ላይ ፡ ሆኖ ፡ አላውቀውም ፡ ሞቴን ።　　(ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እቆማለሁ ፡ እንጂ ፡ እሞታለሁ ፡ አልልም ።

ወ ፡ ሞት ፡ ቢዘገይ ፡ የቀረ ፡ ይመስላል ።

342 ብረቱ ፡ ይቀመጥ ፡ አሽከሮች ፡ አይልፉ ፤
—አምላክ ፡ የሰጠዎ ፡ በቂዎ ፡ ነው ፡ ሰይፉ ።　　(ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ብረቱ ፡ ይቅር ፤ ሰይፉ ፡ ይበቃዎታል ፤ ጠመንዣ ፡ አይያዙ ፤ ሾተሉ ፡ በቂዎ ፡ ነው ።

ወ ፡ ልጅዎ ፡ ሰይፉ ፡ ደጋፊዎ ፡ ረዳትዎ ፡ ነው ፤ ለብዙ ፡ ይተርፋል ።

343 ብረት ፡ ብር ፡ ሳለ ፡ በወርቅ ፡ የተጌጠ ፡
—ሰው ፡ ሁሉ ፡ በሙሉ ፡ መቃ ፡ ብር ፡ መረጠ ።

ሠ ፡ ትልቅ ፡ ትንሹ ፡ የሸንበቆ ፡ ብር ፡ ወደደ ፤ በሱ ፡ መጻፍን ፡ መረጠ ።

ወ ፡ ሰዉ ፡ ሁሉ ፡ ባጕል ፡ ከመቆም ፡ ሞቶ ፡ መቀበርን ፡ ፈቀደ ።

344 ብርሃኔ ፡ ታስራለች ፡ ይላል ፡ ሰራዊቱ ፡
—ለቅሶ ፡ ትርፍም ፡ የለው ፡ እንግዲህ ፡ አስፈቱ ።

ሠ ፡ ከእስራት ፡ አስፈቷት ፤ ከወህኒ ፡ ቤት ፡ አውጧት ።
ወ ፡ ጸሎተ ፡ ፍትሐቱን ፡ አስደርሱ ፤ አስፈቱና ፡ አስቀብሩ ።

345 ብቻችንን ፡ ገጥመን ፡ ከመተናነቅ ፡
—ባንድ ፡ ላይ ፡ ተስሚምተን ፡ እርዱን ፡ እንነቅ ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እንረዳዳና ፡ አጥብቀን ፡ እንመክት ፤ ተጋግዘን ፡ እንመልሰው ፤ ተባብ ረን ፡ እናስወግደው ።
ወ ፡ ቲረዳድተን ፡ የጠላትን ፡ ምሽጉን ፡ እንያዝ ፤ ሰፈሩን ፡ እናስለቅቅ ።

346 ብዙ ፡ ሰው ፡ አለቀ ፡ ዐድዋ ፡ ላይ ፡ ቦሰይፍ ፤
—ለምሳሌ ፡ እንዲሆን ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ይትረፍ ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ከሞት ፡ ይዳን ፤ ከመማረክ ፡ ከመገደል ፡ ያም ልጥ ።
ወ ፡ «አባ ፡ ይትረፍ» ፡ ራስ ፡ አባተ ፡ እንኳ ፡ ይዳን ፤ ከሞት ፡ ይቅር ።

347 ብንጠይቃቸው ፡ ዘመዶቹን ፡ ሁሉ ፡
—ትላንትና ፡ ማታ ፡ ይፈጭ ፡ ነበር ፡ አሉ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 358) ፡

ሠ ፡ እኽል ፡ ይከረትፍ ፡ ይፈጭ ፡ ይሰልቅ ፡ ነበር ፡ አሉ ።
ወ ፡ ይፈጭ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ነበር ፤ ከዚያ ፡ አይተነዋል ፡ አሉን ።

348 ብቻዬን ፡ ተኝቼ ፡ ቢበርደኝ ፡ ሌሊት ፡
—ሽማዬን ፡ ላጥፍ ፡ ነው ፡ የተመኘሁት ።

ሠ ፡ ሽማዬን ፡ አጣጥፌ ፡ ለመልበስ ፡ ነው ፡ የፈቀድሁት ፤ ጋቢዬን ፡ ደ ርቤ ፡ ለመተኛት ፡ ነው ፡ የተመኘሁት ።
ወ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ ርቄ ፡ መንኜ ፡ ዐጽፍ ፡ ለብሼ ፡ ለመኖር ፡ ነው ፡ የምመኘው ።

349 ብዙ ፡ ሸቀጥ ፡ ይዘን ፡ ገበያ ፡ ወጥተን ፡
—ምንም ፡ ምን ፡ ሳይቀረን ፡ አጣርተን ፡ መጣን ።

ሠ ፡ ቀንቶን ፡ በሙሉ ፡ ሸጠን ፡ መጣን ፤ የቀረ ፡ ሸቀጥ ፡ የለም ፤ የያዝነው ፡ ዕቃ ፡ በሙሉ ፡ ተነሣልን ።
ወ ፡ ዘመዶቻችን ፡ በሙሉ ፡ አለቁብን ፤ ለወሬ ፡ ነጋሪ ፡ የቀረ ፡ የለም ፤ ዘራችን ፡ ተሟጠጠ ፤ ፈጽሞ ፡ ጠፋ ።

350 ብዙ ፡ ቤት ፡ እያለ ፡ የሚያምር ፡ ደጃፉ ፡
—ምነው ፡ መኳንንቱ ፡ በሰቀላ ፡ ዐረፉ ።

---

(1) ጣሊያን ፡ ኢትዮጵያን ፡ ለመውረር ፡ ባ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በተነሣ ፡ ጊዜ ፡ ከዓለም ፡ ማኅበር ፡ ርዳታና ፡ ኀይልን ፡ አገራችን ፡ በየጊዜው ፡ አቤት ፡ አቤት ፡ በማለት ፡ ትጠ ይቅ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፡ የሚያመለክት ።

ሠ ፡ ብዙ ፡ ቤት ፡ እያለ ፡ መኳንንቱ ፡ ለምን ፡ እዛኒጋባ ፡ ዳስ ፡ ውስጥ ፡ ተቀ
መጡ ፤ ከሰቀላ ፡ አጠገብ ፡ ዐረፉ ።

ወ ፡ ምነው ፡ መኳንንቱና ፡ ባላባቱ ፡ በስቅላት ፡ ሞት ፡ አለቁ ፤ ግፍ ፡ ተዋ
ለባቸው ።

351 ብፈራ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እናትና ፡ አባቴን ፡
—መች ፡ ይመታው ፡ ነበር ፡ ግማሽ ፡ አካላቴን ።

ሠ ፡ መች ፡ ይመታው ፡ ነበር ፡ ዘመዶቼን ፡ ብፈራ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ጫፉ
ንም ፡ አይነካው ፡ ነበር ።

ወ ፡ ግማሽ ፡ የሚባለው ፡ አሽከር ፡ ወዳጄን ፡ ሊመታው ፡ መች ፡ ይደፍር ፡
ነበር ።

352 ቦግ ፡ አርገሽ ፡ ክፈችው ፡ አንች ፡ ገረድ ፡ በሩን ፡
—በይ ፡ እያየው ፡ ይሂድ ፡ አለመኖሩን ።

ሠ ፡ አላፊ ፡ አግዳሚው ፡ አለመኖሩን ፡ እያየ ፡ ይሂድ ፤ እየተረዳው ፡ ይለፍ ።

ወ ፡ በጄ ፡ የበላ ፡ የጠጣ ፡ ለጋሱ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ አለመኖሩን ፡ ይወ
ቀው ፤ እርሙን ፡ እያወጣ ፡ ይመለስ ።

353 ተመለስ ፡ ወንድሜ ፡ ግባ ፡ ወዳገርህ ፡
—እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ አለት ፡ ትኖራለህ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 423 ፡ 901) ፡

ሠ ፡ በኸረት ፡ ድንጋይ ፡ በአለት ፡ ላይ ፡ እንዴት ፡ ትኖራለህ ።

ወ ፡ ያለእኅት ፡ እንዴት ፡ ትኖራለህ ፤ እንዴትስ ፡ ትዘልቀዋለህ ።

354 ተምረህ ፡ ተምረህ ፡ ዐዋቂ ፡ ስንልህ ፡
—ምነው ፡ በገል ፡ ዐፈር ፡ አድገህ ፡ ትሰፍራለህ ።

ሠ ፡ ካደግህ ፡ በኋላ ፡ እንዴት ፡ በገል ፡ ዐፈር ፡ ትሰፍራለህ ፡ ሕፃን ፡ ይመ
ስል ፤ ለምን ፡ ባፈር ፡ ትጫወታለህ ።

ወ ፡ ሊቁ ፡ «አድገህ» ፡ ሞተህ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለየህን ፤ ወደ ፡ ዐፈርነት ፡
ተለወጥህን ።

355 ተምሮ ፡ ተመርጦ ፡ ለመሆን ፡ መምህር ፡
—እንደ ፡ ታናሽ ፡ እቱ ፡ ይሰፍራል ፡ ዐፈር ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ታናሽ ፡ እኅቱ ፡ ዐፈር ፡ እየሰፈረ ፡ ይጫወታል ።

ወ ፡ ታናሽ ፡ እኅቱን ፡ ተከትሎ ፡ ሞተ ፤ ዐፈር ፡ ሆነ ።

356 ተሰማ ፡ ሳይቀጣው ፡ በልጅነት ፡ ቀርቶ ፡
—ጠና ፡ ራስ ፡ ይመታል ፡ እንኳን ፡ ባት ፡ አግኝቶ ።

ሠ ፡ እንኳን ፡ እቅርቡ ፡ የሆነውን ፡ እግሩን ፡ ተንጠራርቶ ፡ ራስ ፡ ለመም
ታት ፡ ይችላል ።

ወ ፡ አባ ፡ ጠና ፡ እንኳን ፡ ከተራ ፡ ሰው ፡ ከራስ ፡ ጋራ ፡ ጦርነት ፡ ገጥሞ ፡
ድል ፡ ይመታል ።

357 ተሳፋሪው ፡ በዝቶ ፡ እጠባበቃለሁ ፤
እመንገድ ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ ቆሜ ፡ አሳልፋለሁ ።

ሠ ፡ መንገደኛው ፡ ስለ ፡ በዛ ፡ መሳፈሪያ ፡ ቦታ ፡ ስለ ፡ ጠፋ ፡ ወጪ ፡ ወራ
ጁን ፡ ቆሜ ፡ አሳልፋለሁ ፤ ተራዬን ፡ እጠባበቃለሁ ።

ወ ፡ የኔ ፡ ዕለተ ፡ ሞት ፡ እስኪ.መጣ ፡ ድረስ ፡ እየቀደሙኝ ፡ የሚሄዱትን ፡
ሙታን ፡ ወንድሞቼን ፡ እሸኛለሁ ፤ አስከሬናቸውን ፡ እቀብራለሁ ።

358 ተቃጥረን ፡ ነበረ ፡ ልንወጣ ፡ ከተማ ፡
—ምን ፡ እናደርጋለን ፡ ይፈጭ ፡ ከሄደማ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 347) ፡

ሠ ፡ እኽል ፡ ሊፈጭ ፡ ከሄደ ፡ የምናደርገው ፡ ነገር ፡ የለም ።

ወ ፡ ይፈጭ ፡ ከሚባል ፡ ቦታ ፡ ከሄደ ፡ አይገኝም ፤ በከንቱ ፡ አንልፋ ፤ አን
ድከም ።

359 ተቃጥሮ ፡ ሲከዳኝ ፡ የገዛ ፡ ሥጋዬ ፡
—እንግዲህ ፡ ሰው ፡ በቃኝ ፡ አለቀ ፡ ተስፋዬ ።

ሠ ፡ ሁለተኛ ፡ በሰው ፡ አልኰራም ፤ የገዛ ፡ ዘመዶ ፡ ሲከዳኝ ፡ ባዕድ ፡ ወ
ዳጅ ፡ ተስፋ ፡ አላደርግም ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ ተስፋዬ ፡ ሞተ ፤ ዐፈር ፡ ሆነ ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለየ ።

360 ተቸግሪያለሁኝ ፡ ማኅበር ፡ ደርሶብኝ ፤
—እባክህ ፡ አምላኬ ፡ አሳልፍልኝ ።

ሠ ፡ እባክህ ፡ አስተናግድልኝ ፤ አስተናብርልኝ ፤ ዐድልልኝ ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሀብት ፡ ስጠኝ ፤ ዕድሌን ፡ አቃናልኝ ፤ አሳልፍልኝ ።

361 ተነሡ ፡ ሳትለን ፡ ሳንፈጠም ፡ እኛ ፡
—ብቻ ፡ እንዴት ፡ ይሄዳል ፡ ጭብጥ ፡ የያዘ ፡ ዳኛ ። (ቀኛ ፡ ኀ ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ ፍሬ ፡ ነገሩን ፡ የተረዳው ፡ ሥር ፡ መሠረቱን ፡ ያወቀው ፤ እኛን ፡ ሳ
ይዝ ፡ ብቻውን ፡ እንዴት ፡ ይሄዳል ።

ወ ፡ እኛ ፡ ሳንሞት ፡ ሳናልቅ ፡ አስተዳዳሪያችን ፡ ንጉሣችን ፡ ምኒልክ ፡
እንዴት ፡ ትሞትብናለህ ።

362 ተነሡ ፡ እኅቶቼ ፡ ረፍዷል ፡ ሰዓቱ ፤
—በጣም ፡ ከፍ ፡ ብላለች ፡ ትሙቀን ፡ ጣይቱ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 315 ፡ 640) ፡

ሠ ፡ የጧት ፡ ፀሓይ ፡ ትሙቀን ፤ ጣይቱ ፡ ትምታን ።

ወ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ታድርገን ፤ ተድላ ፡ ደስታን ፡ ታድለን ።

363 ተነሣ ፡ ወንድሜ ፡ መንገድ ፡ እንቀጥል ፤
—እኔም ፡ ቅሌን ፡ ይገፍ ፡ አንተም ፡ አገልግል ።

ሠ ፡ አገልግልና ፡ ቅል ፡ ይዘን ፡ እንነሣ ፤ እንሂድ ።

ወ ፡ ሥራህን ፡ በሚገባ ፡ ሥራ ፡ እንደኔ ፡ በቅንነት ፡ አገልግል ።

364 ተነጋግረን ፡ ነበር ፡ ውል ፡ ያለው ፡ ነገር ፤
—ተወው ፡ ታንቀላፋህ ፡ ተተኛህ ፡ ይቅር ።

ሠ ፡ እንቅልፍ ፡ ከወሰደህ ፡ መስማት ፡ ካልቻልክ ፡ የማታዳምጣኝ ፡ ከሆ ንክ ፡ ንግግሬን ፡ ላቁም ፤ ወሬው ፡ ይብቃኝ ።

ወ ፡ አንተ ፡ ከሞትክብኝ ፡ የተነጋገርነው ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ መቅረቱ ፡ ነው ።

365 ተናገር ፡ አንተ ፡ ቤት ፡ እነማ ፡ አደሩብህ ፤
—ሞተህ ፡ ባትቀበር ፡ መዘጋት ፡ አለብህ ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ጌታህ ፡ መሞት ፡ መቀበር ፡ ባይኖርብህ ፡ ተዘግተህ ፡ መቀመጥ ፡ አለብህ ፤ ማንማ ፡ ሰው ፡ ሊኖርብህ ፡ አይገባም ።

ወ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የታየብህ ፡ ቤት ፡ ዛሬ ፡ እነማ ፡ ይኖሩብሃል ፡ የማን ፡ መቀመጫ ፡ ሆነሃል ።

366 ተከተልከኝ ፡ ብዬ ፡ ዞሬ ፡ ዞሬ ፡ ሳይ ፡
—ወይ ፡ ጥጋብ ፡ ወይ ፡ ኩራት ፡ ጐንደር ፡ ቀረህ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ እኔን ፡ ለመከተል ፡ ኰርተህ ፡ እጐንደር ፡ መቅሬትህ ፡ ነውን ።

ወ ፡ መንቀባረር ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ መሆን ፡ እጐንደር ፡ ላይ ፡ ቀረ ።

367 ተከፍሎ ፡ ታለቀ ፡ የጐቻሙ ፡ ግብር ፡
—ደሞ ፡ እናስብለት ፡ ለዳሞቱ ፡ ምድር ።

ሠ ፡ የጐቻሙን ፡ የመሬት ፡ ግብር ፡ ተከፈልን ፡ እጓግዱህ ፡ ደሞ ፡ ለዳሞቱ፡ ርስታችን ፡ የሚከፈል ፡ ገንዘብ ፡ በጊዜ ፡ እናሰናዳ ፤ አዘጋጅተን ፡ እና ስቀምጥ ።

ወ ፡ ለሥጋችን ፡ እንደምንጥር ፡ ሁሉ ፡ ለነፍሳችንም ፡ እናስብ ፤ ዕለተ ፡ ሞታችንን ፡ እንዘከር ፤ ያችን ፡ የመጨረሻ ፡ ቀን ፡ እናስታውስ ።

368 ተውከው ፡ ወይ ፡ ተውከው ፡ ወይ ፡ እጅጌ ፡ መሥራቱን ፤
—ቀሚስ ፡ ያለክናድ ፡ አይተውም ፡ መስፋቱን ።

ሠ ፡ ቀሚስ ፡ እጅጌ ፡ ከሌለው ፡ አያምርም ፤ ይዝረከረካል ።
ወ ፡ ያለሞያ ፡ ያለክንድ ፡ ቀሚስ ፡ ቢለብሱት ፡ ዋጋ ፡ አይሰጥም ፡ አያስከብርም ።

369 ተዋበች ፡ ጉተናሽ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አማረ ፤
—እኔም ፡ ባልሠራ ፡ ይሻለኝ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ ቄንዳላ ፡ ባልሆን ፡ ሽሩባ ፡ ባልሠራ ፡ ጠጉሬን ፡ ባልፍረው ፡ ደግ ፡ ኖሯል ፡ ጉተና ፡ ሳያምርብኝ ፡ አይቀርም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ሞት ፡ እንዲህ ፡ ለማናቸውም ፡ የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ እኔም ፡ ባልፈጠር ፡ ይሻለኝ ፡ ነበር ፤ ደም ፡ ሆኜ ፡ በቀረሁ ፡ ደግ ፡ ነበር ።

370 ተዋት ፡ ትሂድና ፡ የልቧን ፡ ታድርሰው ፤
—ቢይዟት ፡ ቢይዟት ፡ አትገላገል ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ቢለምኗት ፡ ቢነሡ ፡ ቢወድቁ ፡ የማትመለስ ፡ ከሆነች ፡ ትሂድና ፡ የፈ
ቀደችውን ፡ ታድርግ ፤ አሳቧን ፡ ትፈጽም ፤ የልቧን ፡ ታድርስ ።

ወ ፡ እጅ ፡ እግሯን ፡ ቢይዙ ፡ ለማዋለድ ፡ ቢታገሉ ፡ የማይሆንላቸው ፡
ሆነ ፤ ምጥ ፡ ጸናባት ፤ በወሊድ ፡ ሞተች ።

371 ተዋት ፡ አትገላግሏት ፡ ሩቅ ፡ ነው ፡ መንገዷ ፤
—የከበደ ፡ ነገር ፡ ይዛለች ፡ በሆዷ ።

ሠ ፡ ትልቅ ፡ ምስጢር ፡ በልቧ ፡ አለ ፤ ከባድ ፡ የሆነ ፡ ነገር ፡ በሆዷ ፡ ይዛ
ለች ፤ ሂዳ ፡ ትናገርና ፡ ይውጣላት ፤ አትጋብዟት ።

ወ ፡ ፅንስ ፡ በሆዷ ፡ እያለ ፤ በማሕፀኗ ፡ ሽል ፡ ይዛ ፡ ሳትገላገል ፡ ሞተች ፤
ወደማይቀረው ፡ ዓለም ፡ ሄደች ።

372 ተድላ ፡ የውሽ ፡ ሄዶ ፡ ለምን ፡ ተቀበረ ፡ (1)
—አብማማ ፡ ቢሆን ፡ ይነሣ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ «አብማማ» ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ተቀብሮ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ይነሣ ፡
ነበረ ፤ ቦታው ፡ ዐፈሩ ፡ ቃል ፡ ኪዳን ፡ ነበረው ።

ወ ፡ እግዚአብሔር ፡ አብማ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ እንደ ፡ ኢየሱስ ፡ ይነሣ ፡ ነበር ፤
እሱን ፡ ስላልሆነ ፡ ሞቶ ፡ ቀረ ፡ እንጂ ።

373 ተጓዥ ፡ ዘነበ ፡ ወርቅ ፡ ዳዊትሽን ፡ እዘይ ፤
—ተደገመችልሽ ፡ አምሳለ ፡ ጎሩይ ።

ሠ ፡ አምሳለ ፡ ጎሩይ ፡ የምትደግመው ፡ ከሆነ ፤ ዘነበ ፡ ወርቅ ፡ ዳዊትሽን ፡
ይዘሽላት ፡ ሂጂ ፤ እንዳትረሺው ።

ወ ፡ ዘነበ ፡ ወርቅ ፤ አምሳለ ፡ ጎሩይ ፡ ተከትላሽ ፡ ሞተች ፤ ያንችን ፡ የመ
ሰለ ፡ አሳዛኝ ፡ ሞት ፡ ደረሰባት ።

374 ተጠርቶ ፡ ሄደ ፡ አሉ ፡ ድንገት ፡ በሌሊት ፤
—አባቱ ፡ ተመርተው ፡ ላቈዩት ፡ ርስት ።

ሠ ፡ አባቱ ፡ በተተከለው ፡ ሲገብርበት ፡ በቈየው ፡ ርስት ፡ ላይ ፡ ባለጋራ ፡
ተነሥቶበት ፡ ለሙግት ፡ ተጠርቶ ፡ ሄደ ።

ወ ፡ ሞት ፡ የማይቀር ፡ ርስት ፡ በመሆኑ ፡ ፋንታውን ፡ ተወጣ ፤ አባቱ ፡
አያቱ ፡ የሞቱትን ፡ ሞት ፡ ሞተ ።

375 ተፈሪ ፡ መኰንን ፡ ምን ፡ ታገኛለህ ፡
—ችኮ ፡ አርገሽኝ ፡ ቀረህ ፡ ውበቴን ፡ ወስደህ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ቀልቤን ፡ አሳጣሽኝ ፤ ውቃቢ ፡ አስራቅሽኝ ፤ ግርማ ፡ ሞገስ ፡ የሌ
ለው ፡ ሰው ፡ ሆንኩ ፤ ውበቴን ፡ ገፈፍከኝ ።

ወ ፡ እኔን ፡ ትተህ ፡ ውበቴ ፡ የሚባለውን ፡ ተጫዋች ፡ በመውሰድህ ፡ በሕ
ዝብ ፡ ዘንድ ፡ ሞገስንና ፡ መወደድን ፡ አሳጣኸኝ ፤ ተናቅሁ ።

---

(1) ደጃች ፡ ተድላ ፡ ባ፲፰፻፳፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ሲሞቱ ፡ በሽሽግ ፡ ከደብረ ፡ ማርቆስ ፡ ወስደው ፡
የውሽ ፡ ቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሲቀብሯቸው ፡ የተገጠመ ።

ሠ ፡ ሥራዬን ፡ አጠናቅቄ ፡ ጕዳዬን ፡ ፈጽሜ ፡ መጣሁ ።

ወ ፡ አቶ ፡ «ጕዳዬን» ፡ ቀብሬ ፡ ግብአተ ፡ መሬት ፡ አድርሼ ፡ ተመለስሁ ፤ አስቀብሬ ፡ መጣሁ ።

311 በጣም ፡ ተደነቅሁኝ ፡ ስትሠራው ፡ ባይ ፤
—ለካ ፡ ይህ ፡ ገላችን ፡ ዐፈር ፡ ኖሯል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ገል ፡ (ሸክላ) ፡ ካፈር ፡ የሚሠራ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ይህ ፡ ገላችን ፡ ሰውነታችን ፡ ዐፈር ፡ የሚሆን ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ኖሯል ።

312 በጣም ፡ አዝኛለሁ ፡ ጕዳት ፡ በዝቶብኝ ፤
—የዘራሁት ፡ ሁሉ ፡ ጠፋ ፡ ብለውኝ ።

ሠ ፡ አዝመራህ ፡ ጠፋ ፡ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ፡ ብለውኝ ፡ በጣም ፡ አዝኛለሁ ።

ወ ፡ የወለድሁት ፡ አልተባረከልኝም ፤ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ አልደረሰም ፤ በልጅነቱ ፡ ሞተ ።

313 በጣም ፡ ኮምጧለ ፡ ደርቋለ ፡ ጠጃችሁ ፤
—ተማሩ ፡ ጨምሩ ፡ ልጆች ፡ እባካችሁ ።

ሠ ፡ ማር ፡ አክሉ ፤ ጨምሩ ፤ አይበቃም ፡ ያንሳል ።

ወ ፡ በጣም ፡ ተማሩ ፤ አጥኑ ፤ በርቱ ፤ በዕውቀት ፡ ግፉ ፤ በአእምሮ ፡ ጠንክሩ ።

314 በጦር ፡ ማን ፡ ያኸለዋል ፡ የሀገሬን ፡ ልጅ ፤
—ባንድ ፡ አልሆንም ፡ ብሎ ፡ ተበታተነ ፡ እንጅ ። (ነ ፡ ተ) ፡

ሠ ፡ አንድ ፡ አልሆንም ፡ አልተባበርም ፡ ብሎ ፡ ተበታተነ ።

ወ ፡ ባንዳ ፡ የጠላት ፡ ጭፍራ ፡ አልሆንም ፡ አለ ፤ የጠላት ፡ ወታደር ፡ መሆንን ፡ ጠላ ፤ የፋሽስት ፡ አገልጋይ ፡ ለመሆን ፡ አልፈቀደም ።

315 በጨለማ ፡ መሄድ ፡ ያገባል ፡ ከፈፋ ፤
—አሉላ ፡ ደግ ፡ ሄደ ፡ ጣይቱ ፡ ሳትጠፋ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 362፡ 640)፡

ሠ ፡ አሉላ ፡ ሳይመሽ ፡ በጊዜ ፡ ሄደ ፤ ጣይ ፡ ሳለች ፡ ተጓዘ ፤ ዠንበር ፡ ሳትጠልቅ ፡ እቤቱ ፡ ገባ ።

ወ ፡ ራስ ፡ አሉላ ፡ ከእቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ቀድሞ ፡ ሞተ ፤ በወግ ፡ በማዕርግ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ባሉበት ፡ ተቀበረ ፤ በመልካም ፡ ተሸኘ ።

316 በፈረሰኛውም ፡ ፈረሰኛ ፡ አለበት ፤
—በደርሰህ ፡ ውብሸት ፡ በላይ ፡ ደረሰበት ።

ሠ ፡ ፈረሰኛውን ፡ ፈረሰኛ ፡ ቀደመው ፤ ለሁሉም ፡ የበላይ ፡ አለው ።

ወ ፡ ደርሰህን ፡ በላይ ፡ ደረሰበት ፡ በኀይልም ፡ ሊደመስሰው ፡ ታጥቆ ፡ መጣበት ።

317 ቢላዋዬን ፡ ስዬ ፡ እጠብቅሃለሁ ፤
—ሥጋ ፡ አምላክ ፡ ብትሰጠኝ ፡ እበላበታለሁ ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ብትሰጠኝ ፡ ለመብላት ፡ ቢላዋዬን ፡ ስዬ ፡ እጠባበቃለሁ ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ ሥጋህን ፡ ለመቀበል ፡ እንድታበቃኝ ፡ ተዘጋጅቼ ፡ እጠባበቃለሁ ።

318 ቢሸከም ፡ አይከብደው ፡ የለበት ፡ ድካም ፤
—እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ራስ ፡ እኔ ፡ አላየሁም ።

ሠ ፡ ብርቱና ፡ ጠንካራ ፡ የሆነ ፡ እንደዚህ ፡ ያለ ፡ ራስ ፡ አላየሁም ፤ ቢሸከም ፡ አይከብደውም ፤ አይዝለፈለፍም ።

ወ ፡ የማስተዳደር ፡ ችሎታ ፡ ያለው ፡ ደኅና ፡ ገዢ ፡ እንደ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ተፈሪ ፡ ያለ ፡ አይገኝም ፤ ራስ ፡ አገዛዝ ፡ ያውቃሉ ።

319 ቢነግሩት ፡ አይሰማ ፡ የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፤
—እስቲ ፡ ማን ፡ ይመስላል ፡ ዘውዴ ፡ የለበሰው ።

ሠ ፡ ዘውዴ ፡ የለበሰው ፡ የማን ፡ ልብስ ፡ ይመስላል ፤ የሱን ፡ ዐይነት ፡ ልብስ ፡ የሚለብስ ፡ ማነው ።

ወ ፡ ዘውድ ፡ የጫነው ፡ ማነው ፡ ንጉሢው ፡ ማን ፡ ይባላል ።

320 ቢወጡም ፡ ቢወርዱም ፡ ቢዞሩም ፡ በዓለም ፡
—እንደ ፡ ባልንጀራ ፡ የሚስማማ ፡ የለም ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ጓደኛ ፡ እንደ ፡ ባልንጀራ ፡ የሚስማማ ፡ የለም ፤ በጓደኛና ፡ በባልንጀራ ፡ መካከል ፡ በቀላሉ ፡ መግባባት ፡ ያገኛል ።

ወ ፡ (2) ሀብት ፡ እንዳለው ፡ እንደ ፡ ጌታ ፡ ሁሉ ፡ የሚስማማው ፡ የለም ።

ወ ፡ (1) እንደባል ፡ ቤት ፡ የሚመች ፡ የለም ፤ ስጋትና ፡ መሰቀቅ ፡ የለበትም ።

321 ቢገዛን ፡ በጠላሁ ፡ የራስ ፡ ኀይሉ ፡ ልጅ ፤
—የኋላውን ፡ ካሳ ፡ ብፈራ ፡ ነው ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ በኋላ ፡ ካሳ ፡ መክፈልን ፡ ብፈራ ፡ ነው ፤ መቀጮ ፡ መግባባትን ፡ ባልፈቅድ ፡ ነው ።

ወ ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ የተገዛሁት ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ካሳ ፡ የሚባለው ፡ ይመጣና ፡ ያጠቃኛል ፡ ብዬ ፡ ብፈራ ፡ ነው ።

322 ቢጮኸው ፡ ቢያነባው ፡ ስላልጠቀመው ፡
—ድኾ ፡ በጕልበቱ ፡ ነው ፡ ያለቀሰው ።

ሠ ፡ እየተንፏቀቀ ፡ እየወደቀ ፡ እየተነሣ ፡ ነው ፡ ያለቀሰው ፤ ተንበርክኮ ፡ ነው ፡ ሲያነባው ፡ የዋለው ።

ወ ፡ ድኻ ፡ የሚያዝነው ፡ የሚያለቅሰው ፡ በከንቱ ፡ ስለሚያልቀው ፡ ያለ ዋጋ ፡ ስለሚቀረው ፡ ጕልበቱ ፡ ነው ።

323 ባሁኑ ፡ ጦርነት ፡ ማንም ፡ ማን ፡ አይኰራ ፤
—ኀይለ ፡ ሥላሴ ፡ ነው ፡ ይኸንን ፡ የሠራ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ይህ ፡ የሆነው ፡ በሥላሴ ፡ ኀይል ፡ ነው ፤ የአጋዕዝተ ፡ ዓለም ፡ ሥራ ፡ ነው ።

ወ ፡ ነጻነት ፡ የተገኘው ፡ በግ ፡ ቀ ፡ ኃ ፡ ሥላሴ ፡ ብርታትና ፡ ትጋት ፡ ነው ።

ሠ ፡ መረባርብ ፡ መሸጋገሪያ ፡ ድልድይ ፡ ሠርተህ ፡ ተሻግረህ ፡ ጠብቀን ።

ወ ፡ እመረብ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ጠላት ፡ ወግተህ ፡ እርዱን ፡ አስለቅቀህ ፡ ወዲያ ፡ ማዶ ፡ ተሻግረህ ፡ ቈየን ።

389 ታጠቅን ፡ ባል ፡ ብሎ ፡ ማን ፡ አምኖ ፡ ይቈርባል ፤
—ሴሰኛውን ፡ ጐበዝ ፡ ያራቱን ፡ ማዘን ፡ ባል ።

ሠ ፡ ዘማዊውን ፡ በያለበት ፡ ቈባት ፡ ያለውን ፡ ታጠቅን ፡ ካንዲት ፡ ሴት ፡ ይረጋል ፡ ብሎ ፡ ማን ፡ ይቈርባል ።

ወ ፡ ምኞቱ ፡ ታላቅ ፡ የሆነው ፡ መንግሥቱን ፡ ለማስፋፋት ፡ የተነሣው ፡ ጀግናው ፡ ቴዎድሮስ ፡ መቼ ፡ ባንድ ፡ ክፍለ ፡ ሀገር ፡ የሚወሰን ፡ ነው ።

390 ታጥቦ ፡ ተገንዞ ፡ መጣሁ ፡ ሳይቀበር ፤
—ትናንትና ፡ ሰንበት ፡ ባለእግዚአብሔር ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ሰንበትና ፡ ባለወልድ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ አልተቀበረም ።

ወ ፡ ሾቹ ፡ ባሌ ፡ ከመሬት ፡ አንሥቶ ፡ ሰው ፡ ያደረገኝ ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ ለመውለድ ፡ ለመክበድ ፡ ያበቃኝ ፡ እንደ ፡ እግዚአብሔር ፡ የማከብረው ፡ ነበር ።

391 ታፈረ ፡ ሺበሺ ፡ አዬ ፡ ትልቅ ፡ ጌታ ፡
—ሳይታመም ፡ ሳይሞት ፡ በጤናው ፡ ተፈታ ።

ሠ ፡ የቁም ፡ ፍታት ፡ ተደረገለት ፤ በሕይወቱ ፡ ጸሎተ ፡ ፍትሐት ፡ ተደረሰለት ።

ወ ፡ ጤናው ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ ታፈረ ፡ ሺበሺን ፡ ድል ፡ አደረገው ፤ አሸነፈው ።

392 ትልቅ ፡ ሴት ፡ ወይዘሮ ፡ በጌምድር ፡ ሞተች ፤
—መቃብሯ ፡ ጐንደር ፡ ጐዣም ፡ ተፈታች ።

ሠ ፡ በጌምድር ፡ ሞታ ፡ ጐዣም ፡ ተፈታ ፡ ጐንደር ፡ ተቀበረች ።

ወ ፡ በጌምድር ፡ ድል ፡ ሆነ ፤ ጐዣም ፡ ተያዘ ፤ ጐንደር ፡ ተቃጠለ ፤ ጠፋ ።

393 ትልቅ ፡ ዕቃስ ፡ ቢሆን ፡ ትንሽስ ፡ ማሰሮ ፡
—ሠሪ ፡ ለማሳማት ፡ እንዴት ፡ ያለዦሮ ።

ሠ ፡ ትልቅ ፡ ዕቃ ፡ ሆነ ፡ ትንሽ ፡ ማሰሮ ፡ ያለመያዣ ፡ ያለዦሮ ፡ እንዴት ፡ ይሠራል ፤ ይህማ ፡ ሠሪውን ፡ የሚያስነቅፍና ፡ የሚያሳማ ፡ አይደለምን ።

ወ ፡ ያልሰሙትን ፡ ያላረጋገጡትን ፡ ነገር ፡ ወስዶ ፡ ለበላይ ፡ መንገር ፡ ክፉ ፡ መሥራት ፡ እንዴት ፡ ያሳዝናል ፤ አውሪውንም ፡ ተቀባዩንም ፡ የሚያስነቅፍ ፡ ነው ።

394 ትመታኝን ፡ ብዬ ፡ ሴቷ ፡ ልጅ ፡ ወንዱን ፡
—በመቃጣቷ ፡ ነው ፡ ሆዴ ፡ የሚያዝን ። (1)

(1) አቶ ፡ ዓለምነህ ፡ ክንፌ ፡ የሚባል ፡ የጐዣም ፡ ሰው ፡ ይህ ፡ ቀረሽ ፡ የማይዷት ፡ ቈንገ ፡ እናት ፡ ስለ ፡ ሞተችበት ፡ ያለቀሰው ።

ሠ ፡ ለመምታት ፡ መቃጣቷን ፡ መከጀሏን ፡ ሳስበው ፡ ያሳዝነኛል ።

ወ ፡ መቃ ፡ የመሰለው ፡ ጣቷ ፡ ዐፈር ፡ መሆኑን ፡ ሳስበው ፡ ያንገበግበ ኛል ፤ ሆዴን ፡ ይበላዋል ።

395 ትቀበለኝ ፡ እንደሁ ፡ ያመጣሁትን ፡
—ይኸው ፡ ማር ፡ ጌታዬ ፡ በደለኛውን ።

ሠ ፡ ማር ፡ አምጥቻለሁና ፡ ጌታዬ ፡ ተቀበለኝ ።

ወ ፡ ጌታዬ ፡ በደለኛውን ፡ ይቅር ፡ በል ፤ ምሕረት ፡ አድርግለት ፤ ስሕተ ቱን ፡ አትቍጠረው ።

396 ትናንት ፡ በገናውን ፡ እየደረደረ ፡
—ረምሐ ፡ ክንፉ ፡ ነው ፡ በዥማት ፡ ያደረ ። (1)

ሠ ፡ በገና ፡ እየደረደረ ፡ ሲጫወት ፡ ያደረ ፡ ረምሐ ፡ ክንፉ ፡ ነው ።

ወ ፡ ረምሐ ፡ ክንፉ ፡ የሚባለውን ፡ ሰው ፡ አውሬ ፡ ተጣላው ፤ በጫጭቆ ፡ በላው ።

397 ትናንትና ፡ በቀን ፡ ከትናንትም ፡ በፊት ፡ ገበያ ፡ ነበሩ ፤
—ዛሬስ ፡ ደጃች ፡ ተድላ ፡ የት ፡ ጠፉ ፡ ካገሩ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 297) ፡

ሠ ፡ ትናንትናና ፡ ከዚያም ፡ በፊት ፡ እገበያ ፡ ታይተው ፡ ነበር ።

ወ ፡ እንደ ፡ ገበያ ፤ ሕዝብ ፡ ሰብሳቢ ፡ ጕዳይ ፡ ፈጻሚ ፡ የነበሩት ፡ ደጃች ፡ ተድላ ፡ ወዴት ፡ ጠፉ ፤ ጨካኙ ፡ ሞት ፡ ወሰዳቸውን ።

398 ትንሽ ፡ እኽል ፡ ነበር ፡ የታዘዘላቸው ፤
—አለቃ ፡ መጡ ፡ አሉ ፡ በምን ፡ ትሰጧቸው ።

ሠ ፡ ያለመያዣ ፡ ያለስልቻ ፡ መጡ ፤ እኽሉን ፡ በምን ፡ ይወስዱታል ።

ወ ፡ የደብሩ ፡ አለቃ ፡ መጡ ፤ መምህሩ ፡ ከደጅ ፡ ቆመዋል ።

399 ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ግፊው ፡ አንቺ ፡ ልጅ ፡ ወተቱን ፡
—ቅቤው ፡ ቶሎ ፡ ወጥቶ ፡ ይቀባ ፡ ራሳችን ። (2)

ሠ ፡ ወተቱን ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ናጭውና ፡ ቅቤው ፡ ወጥቶ ፡ ራሳችንን ፡ እን ቀባው ።

ወ ፡ ራስነት ፡ ያለው ፡ ጌታችን ፡ ቅብዐ ፡ መንግሥት ፡ ተቀብቶ ፡ ይንገሥ ።

400 ቸሩ ፡ ወልደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሽማኔ ፡ ነህ ፡ አሉ ፤
ያንተ ፡ ሽማኔነት ፡ ምኑ ፡ ይደነቃል ፤
—ካንድ ፡ ወገን ፡ ስትሠራ ፡ ካንዱ ፡ ወገን ፡ ያልቃል ።

---

(1) ደጃች ፡ ብሩና ፡ ራስ ፡ ዐሊ ፡ «ሶማ» ፡ በሚባል ፡ አምባ ፡ ላይ ፡ ጦርነት ፡ አድርገው ፡ ሳለ ፤ ጀግና ፡ የነበረ ፡ ረምሐ ፡ ክንፉ ፡ የሚባል ፡ የደጃች ፡ ብሩ ፡ ጋሻ ፡ ዣግሬ ፡ ሞቶ ፡ ሌሊት ፡ ዥብ ፡ ስለ ፡ በላው ፡ ጌታው ፡ ደጃች ፡ ብሩ ፡ ያለቀሱለት ።

(2) ግርማዊ ፡ ቀዳማዊ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ በራስነት ፡ ማዕርግ ፡ አልጋ ፡ ወራሽ ፡ በነበሩ ፡ ጊዜ ፡ አንዳንድ ፡ ደራሲዎች ፡ ሥርዐተ ፡ ንግሥ ፡ እንዲፈጸምላቸው ፡ በፈሊጥ ፡ ሕዝ ቡን ፡ ያሳሰቡት ።

ሠ ፡ አንዱን ፡ ፈርጅ ፡ ስትሠራ ፡ ባንዱ ፡ በኩል ፡ ያለው ፡ ፈርጅ ፡ ያል ቃል ፤ ባንድ ፡ በኩል ፡ ስትቋጥር ፡ ከሌላው ፡ ወገን ፡ ትቈርጣለህ ።

ወ ፡ አንዱን ፡ በልደት ፡ ወደዚህ ፡ ዓለም ፡ ስትልከው ፡ ሌላውን ፡ በሞት ፡ ትጠራዋለህ ።

401　ቸሩ ፡ አባታችን ፡ ከሁሉም ፡ ሲያበላ ፡
—ይገርማል ፡ አንዳንዱ ፡ አይሰጥም ፡ ከጠላ ።

ሠ ፡ ከጠላ ፡ መጠጥ ፡ አይሰጥም ፤ ጠላውን ፡ ለሰው ፡ አያቀምስም ።

ወ ፡ እግዚአብሔር ፡ አባታችን ፡ ከጠላ ፡ ሀብትን ፡ አይሰጥም ፤ ተድላ ፡ ደስታን ፡ አያድልም ።

402　ቸኵል ፡ ገበያውን ፡ ሰጥተውሃል ፡ አሉ ፤
—ተዋጋ ፡ አትበለጥ ፡ እንደ ፡ ወትሮህ ፡ ሁሉ ።

ሠ ፡ በገበያ ፡ ዋጋ ፡ እንዳትታለል ፤ ተከራክረህ ፡ ውጣ ፡ ውረድ ፡ ብለህ ፡ ግዛ ።

ወ ፡ ጠላትህን ፡ ተዋግተህ ፡ ድል ፡ አድርገው ፤ እንዳትሰንፍ ።

403　ችግርም ፡ የለብን ፡ እስከ ፡ ወዲያኛው ፤
—በኛ ፡ ቤት ፡ የሞላው ፡ ማዘን ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ሠ ፡ የቤት ፡ ማእዘን ፡ ከኛ ፡ ዘንድ ፡ አይቸግርም ፤ እንደ ፡ ልብ ፡ ይገኛል ።

ወ ፡ በኛ ፡ ቤት ፡ ሐዘን ፡ ትካዜ ፡ ሞልቷል ፤ እግዚአብሔርን ፡ መፍራት ፡ አለ ።

404　ኀይሉ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ ስነግራችሁ ፡
—ትታገሉትና ፡ ትሰበራላችሁ ።

ሠ ፡ ከኀይለኛው ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ አትታገሉ ፡ ትወድቃላችሁ ፤ ያለዐቅማችሁ ፡ አትፍጨርጨሩ ።

ወ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያልጣለውን ፡ ረድኤት ፡ ያልተለየውን ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴን ፡ አትታገሉት ፤ የማይሆንላችሁን ፡ አትልፉ ፤ በከንቱ ፡ አትድከሙ ።

405　ነገርህን ፡ መርምረህ ፡ ብትነግረኝ ፡ ምነው ፤
—ባታውቀው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አለማፈር ፡ ነው ።

ሠ ፡ አርመህ ፡ ተናገር ፤ እንዲህ ፡ ያለው ፡ ንግግር ፡ እፍረተ ፡ ቢስ ፡ ያሰኛል ።

ወ ፡ በዓለም ፡ ያለው ፡ ሁሉ ፡ ከዐፈር ፡ የወጣ ፡ ነው ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ ደግሞ ፡ ዐፈር ፡ ይሆናል ።

406　ነግጄም ፡ ዘምቼም ፡ አርሼም ፡ አየሁት ፤ አልረዳኝም ፡ ሀብቴ ፤
—አልቅሼ ፡ እበላለሁ ፡ እንደ ፡ ልጅነቴ ።　(1)

---

(1) የንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ አሽከር ፡ የነበረ ፡ ቦጋለ ፡ ዐይኔ ፡ አበባ ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ ከርሳቸው ፡ ዕረፍት ፡ በኋላ ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ ስለ ፡ ታየው ፡ ዕድሜ ፡ ልኩን ፡ ሲያለቅስ ፡ ነበር ፡ ይባላል ፤ የወታደርነት ፡ ሥራውን ፡ ትቶ ፡ አልቃሽ ፡ መሆን ፡ ሲዝምር ፡ የገጠመው ።

ሠ ፡ በሕፃንነቴ ፡ ሳለቅስ ፡ የምበላው ፡ ይሰጠኝ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፤ ዛሬም ፡ እያዘንኩ ፡ እያለቀስኩ ፡ አብሉኝ ፡ አጠጡኝ ፡ በማለት ፡ እኖራለሁ ።

ወ ፡ እንግዲህ ፡ ሁሉም ፡ ካልሆነልኝ ፡ አልቃሽ ፡ ሆኜ ፡ ሙሾ ፡ እያወረድኩ ፡ እኖራለሁ ።

407 ነፍሱ ፡ ነፈሰ ፡ የለኝ ፡ መጋረጃ ፤
—ልብስ ፡ አልገዛሁም ፡ ምክንያቱን ፡ እንጃ ።

ሠ ፡ ለምን ፡ ይሆን ፡ አሮጌ ፡ ልብስ ፡ ያልገዛሁት ፤ ውራጅ ፡ ያላመጣሁት ።

ወ ፡ አስተዋይ ፡ ያልሆንኩት ፡ ልብ ፡ ያልገዛሁት ፡ ምን ፡ ነክቶኝ ፡ ይሆን ፤ ምክንያቱን ፡ አልተረዳሁትም ።

408 ነፍስ ፡ ብትታመም ፡ ፍሪዳ ፡ አረዱላት ፤
—በከንቱ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሥጋ ፡ ላያድናት ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ይጠግናት ፡ መብል ፡ ያድናት ፡ ይመስል ፡ ነፍስ ፡ ብትታመም ፡ ፍሪዳ ፡ አረዱላት ።

ወ ፡ ለሥጋዊ ፡ ኑሮ ፡ የሚደረገው ፡ ልፋትና ፡ ጥረት ፡ ለነፍስ ፡ አይበጅም ፤ የሚጠቅማት ፡ አይደለም ፤ ሥጋና ፡ ነፍስ ፡ በሥራቸው ፡ አይጣጣሙም ።

409 ና ፡ ብላ ፡ ና ፡ ጠጣ ፡ ደርቋልና ፡ ጠጁ ፤
—አንድ ፡ ቀን ፡ ጥለውት ፡ አባትና ፡ ልጁ ።

ሠ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ ተረዳድተው ፡ የጠመቁት ፡ በመተባበር ፡ የጣሉት ፡ ጠጅ ፡ ደርቋል ፤ በጣም ፡ ተዋጥቷል ፤ መጥተህ ፡ ጠጣ ።

ወ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ ጥለውዎት ፡ በሞት ፡ ተለዩ ፤ ብቻዎን ፡ ቀሩ ።

410 ንጉሥ ፡ በሬ ፡ ይግዙ ፡ እኔ ፡ መሬት ፡ ልሁን ፤
—እንዲያ ፡ እንደ ፡ ወትሯችን ፡ ባለኩል ፡ እንሁን ። (1) (ወ፡ላቀች)፡
(ዘለ ፡ ቍ ፡ 461) ፡

ሠ ፡ እንደ ፡ ቀድሞው ፡ የምናገኘውን ፡ እኩል ፡ እንካፈል ፤ ትዳራችን ፡ ሀብትህ ፡ በሀብቴ ፡ ይሁን ።

ወ ፡ በሞት ፡ አልለይዎት ፤ አብሬዎት ፡ ልቀበር ።

411 ንጉሥ ፡ ተሰማርተው ፡ መኳንንቱ ፡ ሲያርሱ ፡
—ራስ ፡ መኰንንም ፡ ዘር ፡ ይዘው ፡ ደረሱ ።

ሠ ፡ የዘር ፡ እኽል ፡ ይዘው ፡ ወደ ፡ እርሻ ፡ መጡ ።

ወ ፡ የበቃ ፡ የነቃ ፡ ለታላቅ ፡ ማዕርግ ፡ የተገባ ፡ ልጅ ፡ ወለዱ ፤ ዘር ፡ ወጣላቸው ።

412 ንጉሥ ፡ አይቈጡ ፡ የቀረች ፡ መስሎዎ ፡
—ዕዳዬን ፡ ከፍዬ ፡ እስትከተልዎ ። (2)

---

(1 ፡ 2) ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ባረፉ ፡ ጊዜ ፡ ባለቤታቸው ፡ ወይዘሮ ፡ ላቀች ፡ እጅግ ፡ መሪር ፡ የነበረ ፡ ሐዘናቸውን ፡ የገለጹበት ።

ሠ ፡ የተበደርሁትን ፡ ከፍዬ ፡ እከተልዎታለሁ ፤ ዕዳዬን ፡ ጨርሼ ፡ እለጥ
ቅዎታለሁ ፤ የቀረሁ ፡ መስሎዎ ፡ አይቀየሙ ።

ወ ፡ ጽዋ ፡ ተራዬ ፡ ሲደርስ ፡ በሞት ፡ እመስልዎታለሁ ፤ እኔም ፡ አንድ ፡
ቀን ፡ እንደ ፡ ርስዎ ፡ እሆናለሁ ።

413 ንጉሥ ፡ ይመለሱ ፡ ይህ ፡ ነገር ፡ ይከፋል ፤
—ከብት ፡ ይጠፋል ፡ እንጂ ፡ እረኛን ፡ ይጠፋል ።

ሠ ፡ ከብት ፡ ቢጠፋስ ፡ ቅሉ ፡ ጠባቂው ፡ አብሮ ፡ መጥፋት ፡ ይገባዋልን ፤
ጅባት ፡ ብሎ ፡ መመለስ ፡ የለበትምን ።

ወ ፡ የሕዝብ ፡ አስተዳዳሪ ፡ እንዴት ፡ ይሙት ፤ ሻውል ፡ ሲሞት ፡ ሺሕ ፡ ይ
ሙት ፡ እንደሚባለው ።

414 ንጉሥ ፡ ይባረኩ ፡ አቡን ፡ አስመጥተው ፤
—ካረመኔ ፡ ጋራ ፡ ተናክተው ፡ ተናክተው ። (1)

ሠ ፡ ከአረመኔ ፡ ጋራ ፡ ኖረው ፡ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ክርስቲያንነት ፡ ተገኘ ፤
ይልቁንስ ፡ አሁን ፡ አቡኑን ፡ አስመጥተው ፡ ይባረኩ ፤ መጽሐፈ ፡
ቄደር ፡ ይጠመቁ ።

ወ ፡ አረመኔውን ፡ ጠላት ፡ ተምች ፡ መትተው ፤ እንክትክት ፡ ስብርብር ፡
አድርገው ፡ ድል ፡ ነሡት ።

415 አሁንም ፡ ሙትልኝ ፡ ታጠቅ ፡ እንደ ፡ ገና ፤
—መቼም ፡ መች ፡ አይገድህ ፡ ሞት ፡ በጅህ ፡ ነውና ። (አ ፡ እ)፡

ሠ ፡ እንደገና ፡ ታጠቅ ፤ መሣሪያህን ፡ አንሳ ፡ ኃይልህን ፡ ደግመህ ፡ አሳየኝ ፡

ወ ፡ ሞት ፡ ያለው ፡ በጅህ ፡ ነውና ፡ የጠላኸውን ፡ መግደል ፤ የወደድኸ
ውን ፡ ማዳን ፡ ትችላለህ ።

416 አሁን ፡ ምን ፡ ያደርጋል ፡ ሡሥኛ ፡ መሆን ፤
—ብዙ ፡ ቤት ፡ ፈረሰ ፡ ትናንት ፡ በዚያ ፡ ቡን ። (ዮ ፡ ን)፡

ሠ ፡ ለሡሥ ፡ ላምሮት ፡ ተብሎ ፡ በተፈላው ፡ ቡና ፡ ላይ ፡ ጠብ ፡ ተነሥቶ፡
አምባጓሮ ፡ ሆነ ፤ የብዙ ፡ ሰው ፡ ትዳርም ፡ ፈረሰ ።

ወ ፡ በዚያ ፡ አቡን ፡ በጳጳስ ፡ ምክንያት ፡ የብዙ ፡ ሰው ፡ ቤት ፡ ጠፋ ።

417 አሁን ፡ ምን ፡ ያጣላል ፡ ለመሬት ፡ ጉዳይ ፡
—እንዲህ ፡ ዘር ፡ ሲጠፋ ፡ ይቀር ፡ የለም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ የሚዘሩት ፡ ሲጠፋ ፡ የዘር ፡ እኽል ፡ ሲታጣ ፡ ለሚያድር ፡ መሬት ፡
ምን ፡ ያጓጓል ፤ ምን ፡ ያጨቃጭቃል ።

ወ ፡ ዘመድ ፡ አዝማድ ፡ አልቆ ፡ የሰው ፡ ዘር ፡ እንዲህ ፡ ሲታጣ ፡ ብቻዋን ፡
ለምትቀር ፡ ምድር ፡ ያዳም ፡ ልጅ ፡ ምን ፡ ያጣላዋል ።

---

(1) በንጉሡ ፡ በዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ መሪነት ፡ በራስ ፡ አዳል ፡ አበጋዝነት ፡ የጋላው ፡ አገር ፡
ሲቀና ፡ ሠላሳ ፡ አንድ ፡ ቆሮዎች ፡ ድል ፡ በመሆናቸው ፡ የተነገረ ።

418 አሁን ፡ የት ፡ ይገኛል ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሕፃን ፡
—ሥጋውን ፡ አብልቶ ፡ እናቱን ፡ የሚያድን ።

ሠ ፡ የራሱን ፡ ፈንታና ፡ ድርሻ ፡ ሥጋ ፡ መግቦ ፡ እናቱን ፡ ከረኃብ ፡ የሚያድን ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ አሳቢና ፡ አስተዋይ ፡ የሆነ ፡ ልጅ ፡ የት ፡ ይገኛል ።

ወ ፡ ከችግር ፡ የተነሣ ፡ እናት ፡ የልጅዋን ፡ ሥጋ ፡ በልታ ፡ በረኃብ ፡ ከመሞት ፡ ዳነች ፤ ክፉውን ፡ ቀን ፡ ወጣች ።

419 አለ ፡ ትለኛለች ፡ ሞኝ ፡ መስያት ፡ እኔ ፤
—ቅቤው ፡ በፊት ፡ አልቆ ፡ እያየሁት ፡ ባይኔ ። (አ ፡ ገ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ገና ፡ ዱሮ ፡ ማለቁን ፡ ልቤ ፡ ሲያውቀው ፡ ሞኝ ፡ አርጋኝ ፡ የሌለውን ፡ ቅቤ ፡ አለ ፡ ትለኛለች ።

ወ ፡ ቅቤው ፡ የፊት ፡ ማባበሻ ፡ የራስ ፡ ቅባት ፡ ሆኖ ፡ ማለቁን ፡ እያየሁት ፡ አለ ፡ ትለኛለች ።

420 አለ ፡ እያልኩኝ ፡ ልኑር ፡ እያስታወስኩኝ ፤
—እውነት ፡ ሞቶ ፡ እንደሆን ፡ እንዳታረዱኝ ።

ሠ ፡ በርግጥ ፡ ከሞተ ፡ እንዳታረዱኝ ፡ ቢሞትም ፡ ባይሞትም ፡ በተስፋ ፡ ልኑር ፤ ቍርጡን ፡ አትንገሩኝ ።

ወ ፡ «እውነት» ፡ እንደሌለ ፡ እንጂ ፡ ሞተ ፡ ከተቈጠረ ፡ በከንቱ ፡ ለምን ፡ ይደከማል ።

421 አሉባልታ ፡ ሰምተው ፡ እውነት ፡ ነው ፡ እያሉ ፡
ያሳባቂን ፡ ወሬ ፡ እየተቀበሉ ፡

መግባባት ፡ ቀረና ፡ ከረረ ፡ ነገሩ ፤
—አባትና ፡ ልጁ ፡ ተቈራርጠው ፡ ቀሩ ።

ሠ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ ሆድ ፡ ለሆድ ፡ ተጨካከኑ ፤ ባሉባልታና ፡ በሰብቅ ፡ ተለያይተው ፡ ቀሩ ።

ወ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ በሰይፍ ፡ ተጋደሉ ፤ በጨቤ ፡ በሾተል ፡ ተቀራደዱ ፡ ተጨፋጨፉ ።

422 አላለቅስልህም ፡ ዐይኔ ፡ ይሻለኛል ፤
—አንተም ፡ የገና ፡ ለት ፡ ጠም ፡ አውለኸኛል ።

ሠ ፡ የገና ፡ ለት ፡ አላበላኸኝም ፤ ነፍገህ ፡ ባዶ ፡ ሆዴን ፡ አውለኸኛል ።

ወ ፡ በገና ፡ ምድር ፡ ሞትክብኝ ፤ በዓሉ ፡ በዓል ፡ ሳይመስለኝ ፡ዋለ ።

423 አላስመሰክርም ፡ እኔስ ፡ ይህነን ፤
—ሰው ፡ ሁሉ ፡ ያውቀዋል ፡ አለት ፡ መቅረቱን ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 353 ፡ 901) ፡

ሥ ፡ ሞቶ ፡ በአለት ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ መ ቅረ ቱን፡ ሁሉም ፡ አይቶ ፡ በዚህ ፡ ነቃሽ ፡ አያስፈልገም ፤ እማኝ ፡ አያሻም ።

ወ ፡ አለእኅት ፡ ብቻውን ፡ መቅረቱን ፡ አገር ፡ ያውቀዋል ፤ ምስከር ፡ መቍጠር ፡ አያሻም ።

424 አላውቅህም ፡ አለው ፡ እነማይ ፡ በረንታ ፤
—ዳንግላ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ የታደገ ፡ ወልታ ።

ሥ ፡ ወልታ ፡ ያደገው ፡ በዳንግላ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፤ አላውቅህም ፡ የተባለው ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ ነው ።

ወ ፡ ወልታ ፡ ዳንግላ ፡ ለሚባለው ፡ አገር ፡ ወገን ፡ ደጋፊ ፡ አልነበረምን ።

425 አላውቅህም ፡ ያልከኝ ፡ እንደ ፡ ዘበናይ ፡
—እንጀራ ፡ አባቴ ፡ ቤት ፡ አልነበርክም ፡ ወይ ።

ሥ ፡ በእናቴ ፡ ባል ፡ ቤት ፡ አልነበርክም ፡ ወይ ።

ወ ፡ ሀብት ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ አባቴ ፡ ቤት ፡ አልነበርክምን ፤ ምነው ፡ እኔስ ፡ አጣሁህ ።

426 አላውቅሽም ፡ አልከኝ ፡ እንደ ፡ ዘበናይ ፡
—ወይ ፡ ጥጋብ ፡ ወይ ፡ ጥጋብ ፡ መልኬ ፡ ጠፋህ ፡ ወይ ።

ሥ ፡ ይገርማል ፡ እኮ ፤ ያስደንቃል ፤ ወይ ፡ ዘመናይ ፡ መሆን ፤ አሁን ፡ የኔ ፡ መልክ ፡ ጠፋህ ፡ ተሳሳተህ ።

ወ ፡ «መልኬ» ፡ በውነት ፡ በሞት ፡ ተለየሽኝ ፤ ዕረፍትህ ፡ ርግጥ ፡ መሆኑ ፡ ነውን ።

427 አላየሁም ፡ ይላል ፡ እንዲያው ፡ ሲያሞኘን ፡
—መርጦ ፡ የጁ ፡ አድርጎ ፡ ጉግሳ ፡ ዘውዲቱን ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 28 ፡ 576 ) ፡ (አ ፡ በ) ፡

ሥ ፡ ዘውዱን ፡ ወስዶ ፡ እጁ ፡ አድርጎ ፡ ሳለ ፡ እንደማያውቅ ፡ ሰው ፡ አላየሁም ፡ አልወሰድኩም ፡ እያለ ፡ ሲያሞኘን ፡ ይሞክራል ።

ወ ፡ ራስ ፡ ጉግሳ ፡ ወሌ ፡ የተመረጠችውን ፡ ዘውዲቱን ፡ (ንግሥተ ፡ ነገሥታት ፡ ዘውዲቱን) ፡ አግብቶ ፡ በየጁ ፡ ከተማ ፡ በመርጦ ፡ ተቀምጧል ።

428 አላየሁም ፡ ጐበዝ ፡ ኀይለኛ ፡ እንደ ፡ እኽል ፤
—ከመሸ ፡ ተነሥቶ ፡ ሰው ፡ የሚገድል ።

ሥ ፡ ሳይታሰብ ፡ ድንገት ፡ ተነሥቶ ፡ በዕለተ ፡ ጠብ ፡ ነፍስ ፡ የሚያሳልፍ ፡ ጐበዝ ፡ አላየሁም ።

ወ ፡ ጊዜ ፡ ሳይሰጥ ፡ በረኀብ ፡ የሚፈጅ ፡ ኀይለኛ ፡ መቅሠፍት ፡ እንደ ፡ እኽል ፡ ማጣት ፡ ያለ ፡ የለም ።

429 አሌፍ ፡ ብሂል ፡ ብዬ ፡ እታው ፡ ድረስ ፡ ሳውቀው ፡
—ቤት ፡ በማኽል ፡ ገብቶ ፡ ልቤን ፡ አስጨነቀው ።

ሠ ፡ ከአሌፋት ፡ ውስጥ ፡ ቤት ፡ የሚባለው ፡ ጸሎት ፡ ከበደኝ ፤ አልገባም ፡ ብሎ ፡ አስቸገረኝ ።

ወ ፡ የቤት ፡ የትዳር ፡ ነገር ፡ በሐሳቤ ፡ ሁሉ ፡ ጣልቃ ፡ እየገባ ፡ ሥራ ፡ አላ ሠራም ፡ አለኝ ፤ ዕንቅፋት ፡ እየሆነ ፡ አወከኝ ።

430 አልሞተም ፡ ይሉናል ፡ ደጃዝማች ፡ ተድላን ፡
—አሁን ፡ እሑድ ፡ ሲቀር ፡ የምናውቀውን ። (1)

ሠ ፡ እሑድ ፡ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሲቀር ፡ እንረዳለን ።

ወ ፡ የእሑድ ፡ ግብር ፡ ሲቀር ፡ መሞቱን ፡ እናውቀዋለን ፤ እንረዳዋለን ፤ ሕይወቱ ፡ ካለ ፡ ግብዣው ፡ እንደማይታጐል ፡ ርግጠኛ ፡ ነው ።

431 አልሰሙም ፡ ወይ ፡ ጌታ ፡ እንደ ፡ ተከሰሱ ፤
ከችሎት ፡ ሳይደርሱ ፡ ለምን ፡ ተመለሱ ፤
—ከሰማንያዎ ፡ እንኳ ፡ ምነው ፡ በደረሱ ።

ሠ ፡ ከቀጠሮዎ ፡ ባልቀሩ ፡ ደግ ፡ ነበር ፤ ከችሎት ፡ መቅረትዎ ፡ ደግ ፡ አልሆነም ፤ የሚያስወቅሥዎ ፡ ነው ።

ወ ፡ ምነው ፡ በዕድሜዎ ፡ ፹ ፡ ዓመት ፡ በደረሱ ፡ ነበር ፤ ከዚያ ፡ በፊት ፡ መሞትዎ ፡ አሳዝኖናል ።

432 አልሰሙኝም ፡ እንጂ ፡ ቀድሞም ፡ ብነግርዎ ፤
—ይሰሩ ፡ ራስዎን ፡ ፀሐይ ፡ አይምታዎ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 273) ፡

ሠ ፡ ራስዎን ፡ በሻሽ ፡ ይሰሩ ፤ የፀሐዩ ፡ ሐሩር ፡ ይጐዳዎታልና ፡ ይጠን ቀቁ ።

ወ ፡ ያስቸገረዎትን ፡ ባለማዕርግ ፡ ራስ ፡ በእስር ፡ ያቈዩት ፤ በግዞት ፡ ያስቀምጡት ።

433 አልሰማ ፡ ካለማ ፡ የነገርነውን ፡
—ተዉት ፡ አትገላግሉት ፡ ይጣ ፡ ይባዝን ።

ሠ ፡ ይንከራተት ፤ ይዋት ፤ የሚሠራውንና ፡ የሚያደርገውን ፡ ይጣው ፤ የሚነገረውን ፡ የሚሰማ ፡ ካልሆነ ፡ ተዉት ፡ ይንከራተት ፤ ይንቀዋለል ።

ወ ፡ የሚሰጠውን ፡ አመስግኖ ፡ የማይቀበል ፡ ከሆነ ፡ ይጣንም ፡ ይባዝንም፡ ሁለቱንም ፡ ድብሮች ፡ አጥቶ ፡ ከላይ ፡ እታች ፡ እያለ ፡ በደጅ ፡ ጥናት ፡ ይንከራተት ።

434 አልታገልህም ፡ እባክህን ፡ ተወኝ ፤
—ኋላ ፡ ማፈር ፡ አለ ፡ እሰው ፡ ፊት ፡ ጥለኸኝ ።

ሠ ፡ በሕዝብ ፡ ፊት ፡ የጣልኸኝ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እንዳላፍር ፡ አልታገልህም ።

ወ ፡ ኖሮ ፡ ኖሮ ፡ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ በመቃብር ፡ ዐፈር ፡ መሆን ፡ አለ ።

---

(1) የደጃች ፡ ተድላ ፡ ጓሉ ፡ ሞት ፡ ተደብቆ ፡ በመዘግየቱ ፡ ሐዘን ፡ የተሰማቸው ፡ ሰዎች ፤ እሑድን ፡ ያዘክሩ ፡ ነበርና ፡ ያ ፡ ሲታጐል ፡ እንረዳዋለን ፡ ለማለት ፤ ይህን ፡ ተናገሩ ፡ ይባላል ።

435 አልነገርኩህም ፡ ወይ ፡ ተው ፡ አይሆንም ፡ ብዬ ፡
—ልብህን ፡ አሞራ ፡ የበላው ፡ ሰውዬ ።

ሠ ፡ የማስታወስ ፡ ችሎታ ፡ የሌለህ ፡ ልበ ፡ ቢስ ፡ ነህ ።
ወ ፡ ሰውዬ ፤ ሞተህ ፡ ቀባሪ ፡ አጥተህ ፡ ልብህን ፡ አሞራ ፡ በላውን ።

436 አልነገርሽኝም ፡ ወይ ፡ ባላባት ፡ ነኝ ፡ ብለህ ፤
—እንግዲያ ፡ ምነዋ ፡ እዚህ ፡ አገር ፡ የለህ ።

ሠ ፡ ምነው ፡ በዚህ ፡ አገር ፡ ርስት ፡ የለህ ፤ ጌታ ፡ ነኝ ፡ ብዙ ፡ ጕልትና ፡ ሀብት ፡ አለኝ ፡ ትል ፡ አልነበረምን ።
ወ ፡ እንደ ፡ አባት ፡ የነበርከው ፡ ባሌ ፡ በሞት ፡ ጥለሽኝ ፡ ሄድክን ፤ ንግግርህ ፡ ሁሉ ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ።

437 አልጋ ፡ ቢደላደል ፡ መንግሥት ፡ ቢረጋ ፡
—በማገር ፡ ይበላል ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ሥጋ ። (1) (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ በማን ፡ አገር ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ያማረ ፤ ጮማ ፡ የሆነ ፡ ሥጋ ፡ ይበላል ።
ወ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ያማረ ፡ ሥጋ ፡ ቢላዎ ፡ ታጥቶ ፡ ለማገር ፡ በተሰናዳ ፡ በተሰነበጠ ፡ መቃ ፡ እየተቈረጠ ፡ ይበላል ።

438 ሐሚና ፡ ሳይበዛ ፡ ሳይገባብን ፡ ባገር ፡
—ወየው ፡ ዓለም ፡ በኛ ፡ እንዴት ፡ ያምር ፡ ነበር ። (እ ፡ ጣ) ፡

ሠ ፡ ላሊበላ ፡ ሳይበዛ ፡ በያለበት ፡ ሳይበተን ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ሳይረክስ ፡ ወየው ፡ ዓለም ፡ የሚባለው ፡ ዜማ ፡ እንዴት ፡ ያምርብን ፡ ነበር ።
ወ ፡ እንደ ፡ ዛሬው ፡ ሳናጣው ፡ መስጠት ፡ መንሣቱ ፡ መሾም ፡ መሻሩ ፡ ማብላት ፡ ማጠጣቱ ፡ በጃችን ፡ ሳለ ፡ እንዴት ፡ ያምር ፡ ነበር ፤ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ ዓለም ፡ እኮ ፡ ዋሾ ፡ ነው ።

439 አማቶችህ ፡ መጡ ፡ ተሸሸግ ፡ የለህም ፤
—እንዲያውም ፡ ማፈሩ ፡ አያዛልቅህም ።

ሠ ፡ አማቶችህ ፡ መጡልህ ፤ ማየቱ ፡ ያሳፍርሃልና ፡ ተደበቅ ።
ወ ፡ ተቀብረህ ፡ በዐፈሩ ፡ ውስጥ ፡ አትኖርም ፤ ትቢያ ፡ ትሆናለህ ።

440 አምላክ ፡ በጨለማ ፡ እንዳይሄድ ፡ ዐውቃለሁ ፤
—ቀን ፡ ያልፋል ፡ ብለውኝ ፡ እጠባበቃለሁ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 726)

ሠ ፡ አምላክ ፡ ፀሐይ ፡ ሳለ ፡ በጊዜ ፡ ይሄዳል ፡ ብለውኝ ፡ እጠብቃለሁ ።
ወ ፡ የመከራና ፡ የችግር ፡ ጊዜ ፡ ኀላፊ ፡ መሆኑን ፡ ስለምረዳ ፡ በትዕግሥት ፡ መጪውን ፡ መልካሙን ፡ ጊዜ ፡ እጠባበቃለሁ ።

---

(1) ዐፄ ፡ ምኒልክ ፡ ያዲስ ፡ ዓለምን ፡ አዳራሽ ፡ ጣራ ፡ ማገር ፡ ሲያስማግሩ ፡ ለግብር ፡ የቀረበው ፡ ሥጋ ፡ የሚበላባት ፡ ቢላዎ ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ ሳይመጣ ፡ ስለ ፡ ዘገየና ፡ በመቃ ፡ ስለ ፡ ተቈረጠ ፡ እዚያ ፡ የነበሩ ፡ አለቃ ፡ በዛብህ ፡ የገጠሙት ።

441 አምላክ ፡ ግብር ፡ ሠርቶ ፡ ያበላል ፡ ይላሉ ፤
—አንድም ፡ ቀሪ ፡ የለ ፡ ሁሉም ፡ ይጠራሉ ።

ሠ ፡ አምላክ ፡ ግብዣ ፡ ስለሚያደርግ ፡ ማንኛውም ፡ ሰው ፡ ይጠራል ፤ የሚቀር ፡ አይኖርም ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ የለበሰ ፡ ሁሉም ፡ ሟች ፡ ነው ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሚቀር ፡ የለም ።

442 አምሳ ፡ ባለዳለች ፡ አምሳ ፡ ባላምባላይ ፡
—ይኸ ፡ ሁሉ ፡ ፈረስ ፡ በቅሎ ፡ ጠፋ ፡ እነማይ ።

ሠ ፡ እነማይ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ፈረስ ፡ እንጂ ፡ በቅሎ ፡ የለም ።

ወ ፡ የነማይ ፡ ተወላጆች ፡ ሁሉ ፡ ታይቶ ፡ ጠፊዎች ፡ ሆኑ ፤ ሞት ፡ አጠቃቸው ።

443 አምናና ፡ ካች ፡ አምና ፡ ደኅና ፡ ሰው ፡ ነበረች ፤
—በሽታዋ ፡ መጣ፡ ትተኵስ ፡ ዠመረች ። (ን ፡ ሣ ፡ ሥ) ፡

ሠ ፡ ዘንድሮ ፡ ሕመም ፡ አደረባት ፡ መሰለኝ ፤ ሰውነቷ ፡ ያተኵስ ፡ ዠመር ።

ወ ፡ የሠራችውን ፡ ሸክላ ፡ በእሳት ፡ መተኰስ ፡ ዠመረች ፤ ሥራዋን ፡ ቀጠለች ፤ የዘሯን ፡ ሞያ ፡ አረሳችም ።

444 አሞራ ፡ እንኳ ፡ አዝኖ ፡ በወንድሜ ፡ ሞት ፡
—ዋ ፡ ብሎ ፡ በረረ ፡ አንዠቱን ፡ በልቶት ።

ሠ ፡ አሞራ ፡ እንኳ ፡ በወንድሜ ፡ ሞት ፡ አዝኖ ፡ ተክዞ ፡ ዋ ፡ ብሎ ፡ ጮኸ፤ አልቅሶ ፡ ሄደ ።

ወ ፡ የወንድሜን ፡ አንዠት ፡ አሞራ ፡ በላው ፤ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ወድቆ ፡ ጆፌው ፡ ጕሚው ፡ ተበጫጨቀው ።

445 አሞራው ፡ ንገረኝ ፡ ላልቅስለት ፡ እቱ ፡
—ባለሻሉ ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ የበላይ ፡ ከፊቱ ።

ሠ ፡ ከፊቱ ፡ ቀርበህ ፡ ትበላ ፡ የነበርከው ፡ ባለሻሉ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤ አንተ ፡ የማታውቀው ፡ ነገር ፡ የለምና ፤ ወንድሜ ፡ የሆነውን ፡ ንገረኝና ፡ ላልቅስለት ።

ወ ፡ የወንድሜን ፡ ፊት ፡ የዘነተርህ ፡ በጥፍርህም ፡ እየቧጠጥህ ፡ የበላኸው ፡ አሞራው ፡ አንተ ፡ ነህ ።

446 አሳብም ፡ የለብኝ ፡ እኔስ ፡ ዐርፌያለሁ ፤
—በቈላም ፡ በደጋም ፡ ዘሬን ፡ ጨርሻለሁ ።

ሠ ፡ በቈላም ፡ በደጋም ፡ ያለውን ፡ መሬቴን ፡ ዘርቼ ፡ ጨርሻለሁ ፤ አዝመራዬን ፡ አጠናቅቂያለሁ ።

ወ ፡ በያለበት ፡ ያሉት ፡ ዘመዶቼ ፡ በሞት ፡ አለቁ ፤ ዘሮቼ ፡ ወገኖቼ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተሻጠጡ ።

447 አሥራ ፡ አንድ ፡ አትግደል ፡ ደጃዝማች ፡ ማጠንቱ ፤
—ለዥብዱም ፡ እንደሆን ፡ ይበቃል ፡ ስምንቱ ።

ሠ ፡ ለግዳይ ፡ እንደሆን ፡ ስምንቱ ፡ ሰዎች ፡ ይበቁሃል ፡ ከዚህ ፡ በላይ ፡ አትግደል ፤ ዐሥራ ፡ አንድ ፡ መግደሉ ፡ ይቅርብህ ።

ወ ፡ ስምንቱ ፡ የሚባለውን ፡ ጕበዝ ፡ ደጃዝማች ፡ ማጠንቱ ፡ ገደለው ፤ ሕይወቱን ፡ አሳጣው ።

448 አረቄ ፡ አጠጥቶ ፡ ውስኪ ፡ መድገም ፡ ምነው ፡
—እኔስ ፡ ደስ ፡ የሚለኝ ፡ ግብዣ ፡ በፋንታ ፡ ነው ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ግብዣ ፡ የሚያምረው ፡ ሁሉም ፡ በበኩሉ ፡ ሲጋበዝ ፡ ነው ።

ወ ፡ በአረቄ ፡ በውስኪ ፡ በታላላቅ ፡ መጠጦች ፡ ከሚደረገው ፡ ግብዣ ፡ ፋንታ ፡ በሚባለው ፡ በቀዝቃዛ ፡ መጠጥ ፡ የሚሆነውን ፡ እመርጣለሁ።

449 አረጉም ፡ እንቢ ፡ አለ ፡ እየተበጠሰ ፤
ገመዱም ፡ እንቢ ፡ አለ ፡ እየተበጠሰ ፤
—ያለማገር ፡ ቀረ ፡ አንኮበር ፡ ፈረሰ ።

ሠ ፡ በአንኮበር ፡ የቆመው ፡ የቤት ፡ ግድግዳ ፡ ሳይማገር ፡ ቀረ ፤ በውጥን ፡ ሳያልቅ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ መልካሙ ፡ አገር ፡ አንኮበር ፡ የብዙ ፡ ሕዝብ ፡ መኖሪያ ፡ የነበረው ፡ ጠፋ ፤ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ማያ ፡ የነበረው ፡ ቦታ ፡ ተመዘበረ ።

450 አራሲቱ ፡ ወተት ፡ ጠጪ ፡ ይሻልሻል ፤
—አልቦ ፡ ይዞ ፡ ባልሽ ፡ ያስፈርድብሻል ።

ሠ ፡ ወተት ፡ አልቦ ፡ አምጥቶልሻል ፡ ጠጪ ፡ ይደግፍሻል ፤ እንደ ፡ ሴት ፡ አዘጋጅቶ ፡ ባልሽ ፡ ያመጣልሽን ፡ እንቢ ፡ ማለት ፡ ጡር ፡ ይሆንብሻል ።

ወ ፡ ባልሽ ፡ የግር ፡ አልቦሽን ፡ ይዞ ፡ ዘመድ ፡ አዝማድሽን ፡ ያስለቅሳል ።

451 አርባ ፡ ስድስት ፡ ዓመት ፡ የገዛኸው ፡ ንጉሥ ፡
—እንዳለህም ፡ ስጠኝ ፡ እንደሌለህ ፡ ላልቅስ ።

ሠ ፡ ገንዘብ ፡ እንዳለህ ፡ ስጠኝ ፤ ካጣህም ፡ ይቅር ፡ ተወው ፤ በዕድሌ ፡ ልዘን ፤ ላልቅስ ።

ወ ፡ መኖር ፡ አለመኖርህን ፡ ልወቀው ፤ ሞተህ ፡ እንደሆን ፡ እርሜን ፡ ላውጣ ፡ ላልቅስ ።

452 አርባ ፡ ቁም ፡ ከናውራው ፡ ሰጥተው ፡ ቢድሩት ፡
—እሸቴ ፡ ቀጸላ ፡ ይበላል ፡ አንዥት ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 89) ፡

ሠ ፡ ለርቢ ፡ የሚሆኑ ፡ ብዙ ፡ የቀንድ ፡ ከብቶች ፡ እያሉት ፡ አማርጦ ፡ አርዶ ፡ መብላት ፡ ሲችል ፡ ካላጣው ፡ ሥጋ ፡ አንዥት ፡ ይበላል ።

ወ ፡ የእሸቴ ፡ ቀጸላ ፡ ሞት ፡ አንዥት ፡ ይበላል ፤ ያቃጥላል ፤ ያንገበግባል ።

453 አርደህ ፡ ብላው ፡ አሉኝ ፡ ለምን ፡ አርደዋለሁ ፤
—ሲመጣ ፡ ከፊቱ ፡ ያን ፡ በግ ፡ አየዋለሁ ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ያ ፡ በግ ፡ ሲመጣ ፡ ቦቃ ፡ ይሁን ፡ በለጭማ ፡ አየዋለሁ ፤ እንዲታረድ ፡ ግን ፡ አልፈቅድም ።

ወ ፡ ክረምቱ ፡ ሲጠባ ፡ የበጋው ፡ ወራት ፡ ደግሞ ፡ እንዴት ፡ እንደሚሆን ፡ እረዳዋለሁ ።

454 አሰምራቸውና ፡ ከብቶቻችን ፡ ይብሉ ፤
አሰምራቸውና ፡ በጎቻችን ፡ ይብሉ ፤
አሰምራቸውና ፡ ፍየሎቹ ፡ ይብሉ ፤
—ያ ፡ ሣር ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ የምናየው ፡ ሁሉ ።

ሠ ፡ የምናየው ፡ የምንመለከተው ፡ ሁሉ ፡ ምን ፡ መሰለው ፤ ሣር ፡ እኮ ፡ ነው ፤ ከብቶቹን ፡ ወደዚያ ፡ ንዳቸውና ፡ ይጋጡ ።

ወ ፡ ማናቸውም ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የምናየው ፡ ሁሉ ፡ ትግል ፡ ጭንቅ ፡ ፈተና ፡ አሳር ፡ ያለበት ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ምን ፡ ያለፋል ።

455 አሳላፊው ፡ ሁሉ ፡ ባይሆነን ፡ ወዳጅ ፡
—ሳያድለን ፡ ቀረ ፡ እኛን ፡ ጠላ ፡ ጠጅ ።

ሠ ፡ አሳላፊው ፡ ጠላና ፡ ጠጅ ፡ ሳይሰጠን ፡ ቀረ ፤ ዘለለን ።

ወ ፡ ሀብት ፡ ሰጭ ፡ የሆኑ ፡ ጌቶች ፡ ሁሉ ፡ ሳንታደል ፡ በመቅረታችን ፡ ግዛት ፡ ሳያሰጡን ፡ ቀሩ ፤ ከችግር ፡ አላወጡንም ።

456 አሳላፊውማ ፡ ሰጠው ፡ ለወዳጅ ፡
—እንሥተው ፡ ሲጠጡት ፡ ይጣፍጣል ፡ እንጅ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ አሳላፊ ፡ ከሚሰጠው ፡ በጅ ፡ አንሥተው ፡ የሚጠጡት ፡ ጠጅ ፡ ይጥማል ፤ ከአንገሮት ፡ ይደርሳል ።

ወ ፡ ጌታ ፡ አንሥተህ ፡ ጠጣ ፡ ሲል ፡ ክብርና ፡ ደስታ ፡ ይሰማል ፤ ተወዳጅነትንና ፡ ባለሟልነትን ፡ ይገልጸል ።

457 አስፈልገን ፡ ነበር ፡ በያገሩ ፡ ሁሉ ፡
—እንሳሮ ፡ ወረዳ ፡ ቀን ፡ ታይታለች ፡ አሉ ።

ሠ ፡ በብርሃን ፡ ሳይመሽ ፡ እንሳሮ ፡ ወረዳ ፡ ታይታለች ፡ ይላሉ ።

ወ ፡ እንሳሮ ፡ ላይ ፡ ዓለም ፡ ታይቷል ፤ ፍሥሐና ፡ ደስታ ፡ ብቻ ፡ ሆኖ ፡ ከርሟል ።

458 አስፋ ፡ ወሰን ፡ ኀይሌ ፡ ብርንዶ ፡ አቅርቧል ፤
—እያጐረሠ ፡ ሰው ፡ አላምጡ ፡ ይላል ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ኀይሌ ፡ ባፍ ፡ ባፋቸው ፡ እያጐረሠ ፡ አላምጣችሁ ፡ ዋጡ ፡ ይላል ።

ወ ፡ ገበታው ፡ ሰፊ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ በግብሩ ፡ ላይ ፡ አለቀን ፡ አይወድም ፤ አለ ፡ ጨምሩ ፡ አምጡ ፡ ስጡ ፡ ይላል ።

459 አስፋ ፡ ወሰን ፡ ልብሱ ፡ አይሁን ፡ ተላላፊ ፤
አላወቀበትም ፡ ይኸ ፡ ልብስ ፡ ሰፊ ፤
—እሱን ፡ ያስወደደው ፡ ቢሆን ፡ እጁ ፡ ሰፊ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ልብስ ፡ ሰፊው ፡ የልብሱን ፡ አሰፋፍ ፡ አላወቀበትም ፤ ልቡ ፡ የሚፈቅደውን ፡ ዐይነት ፡ አልሰፋም ።

ወ ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ኀይሌ ፡ ፈቃዱ ፡ በሰፊው ፡ መስጠት ፡ በችሮታው ፡ ማስደሰት ፡ ነው ።

460 አሻቅቤ ፡ አይቼ ፡ አቈልቍዬ ፡ አያለሁ ፤
—አገሬን ፡ ካለሰው ፡ ምን ፡ አረገዋለሁ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ከሞተ ፡ የሚኖርበት ፡ ከሌለ ፡ አገር ፡ ባዶውን ፡ ምን ፡ ያደርጋል ።

ወ ፡ ሰው ፡ አገሬ ፡ ልግባ ፡ ብሎ ፡ ቈርጦ ፡ ከተነሣ ፡ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይቻላል ።

461 አሽከሬ ፡ ጠፍቶኛል ፤ በቅሎዬም ፡ ጠፍቶኛል ፤
—አፋልገኝ ፡ ጕዝሜ ፡ በባል ፡ ቀን ፡ ይገኛል ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 410)

ሠ ፡ ብዙ ፡ ሆነን ፡ በበዓል ፡ ቀን ፡ (ባዘቦት) ፡ ብንፈልግ ፡ ይገኛል ።

ወ ፡ ከባል ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ መኖር ፡ ከቁም ፡ ነገር ፡ ያደርሳል ፤ መውለድ ፡ መክበድ ፡ ይገኛል ።

462 አበቅቴ ፡ ሲቈጠር ፡ ብሰማ ፡ እንደ ፡ ዋዛ ፡
—ምን ፡ ያለ ፡ ዘመን ፡ ነው ፡ ተውሳኩ ፡ የበዛ ።

ሠ ፡ ዘመኑ ፡ ሲቈጠር ፡ ግድፈት ፡ የበዛበት ፡ መሆኑን ፡ ተረዳሁ ፤ ምን ፡ ያለ ፡ ያልተካከለ ፡ የቀን ፡ መቍጠሪያ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ዘመኑ ፡ በሽታ ፡ ረኃብ ፡ ችግር ፡ የበዛበት ፡ የማያስተማምን ፡ ሆነ ።

463 አቡኑም ፡ ተቈጡ ፤ ዕጨጌም ፡ ተቈጡ ፤
—ቅባቱ ፡ ቀረና ፡ ቃሪያ ፡ ቢሆን ፡ ወጡ ።

ሠ ፡ ወጡ ፡ ቅቤ ፡ የሌለው ፡ በቃሪያ ፡ የተሠራ ፡ በመሆኑ ፡ ተቈጡ ።

ወ ፡ የቅባት ፡ ሃይማኖት ፡ የተነቀፈ ፡ ነው ፡ በማለት ፡ ጳጳሱም ፡ ዕጨጌውም ፡ ተቈጡ ።

464 አባ ፡ ማሬ ፡ ውቤ ፡ ደመና ፡ መሳይ ፡
—አንተን ፡ ማን ፡ ከለለህ ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ አገር ፡ ጣይ ።

ሠ ፡ አገሩ ፡ ሁሉ ፡ ፀሓይ ፡ ሲሆን ፡ አንተን ፡ ማን ፡ ጋረደህ ፤ ማን ፡ እንዳትሞቅ ፡ ከለከለህ ።

ወ ፡ ማንኛውም ፡ ፍጡር ፡ ይህንን ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ ጥሎ ፡ የሚሄድ ፡ ነው ።

465 አባተ ፡ አባ ፡ ይትረፍ ፡ አሳባቂ ፡ ነው ፤
—ይህን ፡ መድፍ ፡ ከዚያ ፡ መድፍ ፡ አቈራረጠው ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አሳብቆ ፡ ነገር ፡ ከወዲያ ፡ ወዲህ ፡ ብሎ ፡ አጣላው ፤ አቈራረጠው ፤ አለያየው ።

ወ ፡ አባ ፡ ይትረፍ ፡ (ራስ ፡ አባተ) ፡ መድፉን ፡ በመድፍ ፡ ተኵሶ ፡ መቶ ፡ ሰባበረው ፤ ጠላትን ፡ አሳፈረው ።

466 አባትና ፡ ልጁ ፡ ተጣልተው ፡ በመንገድ ፡
—ልጁ ፡ ልቅደም ፡ አለ ፡ ወይ ፡ እንዳሻው ፡ መልመድ ።

ሠ ፡ አባትና ፡ ልጁ ፡ መንገድ ፡ ሲሄዱ ፡ ልጁ ፡ ካባቱ ፡ ፊት ፡ ቀድሜ ፡ ልሂድ ፡ አለ ።

ወ ፡ ልጁ ፡ ካባቱ ፡ በፊት ፡ ሞተ ፤ ወላጁ ፡ እያለ ፡ ልጁ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለየ ።

467 አባት ፡ የለውም ፡ ወይ ፡ የመጣው ፡ ንጉሥ ፤
—እኽል ፡ ይሙት ፡ ይላል ፡ ተክለ ፡ ጊዮርጊስ ። (1)

ሠ ፡ ተክለ ፡ ጊዮርጊስ ፡ «እኽል ፡ ይሙት» ፡ እያለ ፡ ይምላል ፤ የሚጠራበት ፡ የሚምልበት ፡ ወላጅ ፡ አባት ፡ የለውምን ።

ወ ፡ ተክለ ፡ ጊዮርጊስ፡ ጡር፡ አይፈራም፤ እኽል፡ ይጥፋ፡ እያለ፡ ያውጃል ።

468 አባት ፡ ያቈየንን ፡ አድርጎ ፡ እጅ ፡ ከፍንጅ ፡
—ዋቢ ፡ አናሳልፍም ፡ እኛው ፡ እንፍጅ ፡ እንጅ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ራሳችን ፡ እንሟገት ፤ ጠበቃ ፡ እንግዛ ፤ ነገረ ፡ ፈጅ ፡ እንፈልግ ።

ወ ፡ ጠላትን ፡ ዋቢ ፡ ሸበሌ ፡ ከሚባለው ፡ ወንዝ ፡ አናሳልፈው ፤ እዚያው ፡ እንፍጀው ።

469 አባ ፡ ጠቅል ፡ ኃይሌ ፡ በቈላው ፡ በደጋው ፡ ፍየል፡ አስመልምል፤
—እንዳታሳድገው ፡ አረባለሁ ፡ ሲል ።

ሠ ፡ በደጋም ፡ በቈላም ፡ ተክልና ፡ ሰብል ፡ እንዳያጠፉ ፡ ፍየል፡ ማርባትን፡ ከልክል ።

ወ ፡ ዐረብ ፡ ባገራችን ፡ እንዳይገባና ፡ እንዳይበዛ ፡ እንዳይበረክትም ፡ ብልኀት ፡ ይፈጠርለት ፤ ጥንቃቄ ፡ ይደረግለት ።

470 አባ ፡ ጠቅል ፡ ኃይሌ ፡ እየጠረጠረኝ ፡
—ሽማግሌውን ፡ ሰው ፡ አስገዝቶ ፡ አኖረኝ ።

ሠ ፡ መጠርጠር ፡ የማይገባኝን ፡ ሽማግሌውን ፡ ሰው ፡ አስምሎ ፡ አስገዝቶ ፡ አስቀመጠኝ ።

ወ ፡ ሾሞ ፡ ሸልሞ ፡ ግዛት ፡ ሰጥቶ ፡ አኖረኝ ።

---

(1) ራስ ፡ ደስታ ፡ ልጃቸውን ፡ ካገቡ ፡ በኋላ ፡ ስለ ፡ ከዱቸው ፡ ዐፄ ፡ ተክለ ፡ ጊዮርጊስ ፡ ወደ ፡ ጐጃም ፡ ሄደው ፡ አገሩን ፡ ስለ ፡ ዘረፉትና ፡ እኽሉን ፡ ስለ ፡ አቃጠሉት ፡ አንዲት ፡ የተራበች ፡ አልቃሽ ፡ ያለፍርሀት ፡ የተናገረችው ።

471 አባ ፡ ጠቅል ፡ ኃይሌ ፡ ዳኘነት ፡ ያውቃል ፤
—እያወራረደ ፡ ያፈጣጥማል ። (ነ ፡ ተ ፡ አ) ፡

ሠ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ ዳኝነት ፡ ይችላል ፤ በሚገባ ፡ እየመረመረ ፡ ይጨርሳል ፤ የሚጣራም ፡ ቢኖር ፡ በቀጠሮ ፡ እንዲቀርብ ፡ ያደርጋል ።

ወ ፡ በጀግንነት ፡ ያዋጋል ፤ ጠላትን ፡ አንገት ፡ አንገቱን ፡ እያስቈረጠ ፡ ድል ፡ ያደርጋል ።

472 አባ ፡ ጠቅል ፡ ኃይሌ ፡ ጦርክን ፡ ተመርኰዘው ፤
—ጋሻህ ፡ ኀይለኛ ፡ ነው ፡ ዘንግ ፡ አትበል ፡ አንተ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ ዘንግ ፡ አያሻህም ፤ ጋሻህን ፡ መክተው ፤ ጦርክን ፡ ተመርኰዘው ።

ወ ፡ አትዘንጋ ፤ ሁሉን ፡ አትመን ፤ ጠላትህንና ፡ ወዳጅህን ፡ ለይተህ ፡ ዕወቅ ።

473 አብርሃም ፡ ቢጣላ ፡ ከሳራ ፡ ከሚስቱ ፡
ባሪያውን ፡ አጋርን ፡ አስወጣት ፡ ከቤቱ ፤ (1)

ዳኛውም ፡ ፈረደ ፡ በሁለቱ ፡ ላይ ፡
አንተም ፡ ሠርተህ ፡ ብላ ፡ አንቺም ፡ ሠርተሽ ፡ ብይ ፤
—አላጋር ፡ እንጀራ ፡ አይበላም ፡ ወይ ። (ወ ፡ ጸ ፡ ጋ) ፡

ሠ ፡ አጋርን ፡ የሳራን ፡ ገረድ ፡ አብርሃም ፡ ከቤቱ ፡ አስወጣት ።

ወ ፡ ያለአጋር ፡ ያለረዳት ፡ እንጀራ ፡ ማግኘት ፡ አይቻልምን ፤ ሰው ፡ በዕውቀቱ ፡ በጕልበቱ ፡ መተዳደር ፡ አይሆንለትም ፡ ወይ ።

474 አብቹና ፡ ገላን ፡ ሰብቅ ፡ ይነሰንሳል ፤
—አሁን ፡ የኔ ፡ ጌታ ፡ በማሴት ፡ ይደርሳል ። (2) (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ ከማን ፡ ሚስት ፡ ይሄዳል ፤ ምንስ ፡ ቁባት ፡ አለው ።

ወ ፡ ማሴት ፡ በሚባለው ፡ አገር ፡ ጦር ፡ አስከትቶ ፡ ይመጣል ፤ አሁን ፡ እሳት ፡ ለብሶ ፡ እሳት ፡ ጐርሦ ፡ ይደርሳል ።

475 —አብዬ ፡ ሥጋህን ፡ ተቀብዬ ፡ አላውቅም ፡
—ታውቀዋለህና ፡ ሐሰት ፡ እንዳይጠቅም ።

ሠ ፡ ሥጋህን ፡ በሐሰት ፡ ያለጽኑ ፡ እምነት ፡ ተቀብዬ ፡ አላውቅም ፡

ወ ፡ «አ» ፡ ብዬ ፡ አፌን ፡ ከፍቼ ፡ ሥጋህን ፡ ተቀብዬ ፡ አላውቅም ።

---

(1) በመጽሐፍ ፡ ቅዱስ ፡ እንደ ፡ ተጻፈው ፡ አብርሃም ፡ አጋር ፡ የምትባለውን ፡ ገረዱን ፡ ከቤቱ ፡ አስወጥቶ ፡ እንዳባረራት ፡ የሚገልጥ ፡ ነው ።

(2) አብቹና ፡ ገላን ፡ ንጉሕ ፡ ተገዥነቱን ፡ አንድሎ ፡ ለመክዳት ፡ ማሰቡ ፡ በተሰማ ፡ ጊዜ ፡ ንጉሥ ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ «ማሴት» ፡ በሚባለው ፡ ቀበሌ ፡ አድርገው ፡ ለመውረርና ፡ ለመውጋት ፡ ማሰባቸውን ፡ አለቃ ፡ ወልደ ፡ ጊዮርጊስ ፡ የገለጹበት ።

476 አታክልት ፡ ጠባቂ ፡ ለካ ፡ ጃንሆይ ፡ ናቸው ፤
—ወይኔ ፡ ተቈረጠች ፡ ሲሉ ፡ ሰማኋቸው ።

ሠ ፡ የተከልኳት ፡ ወይኔ ፡ ተቈረጠች ፡ ተቀጥፋ ፡ ወደቀች ፡ ሲሉ ፡ ሰማ ኋቸው ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ ልጄ ፡ ተለየችኝ ፤ በወጣትነቷ ፡ ሞተችብኝ ፡ እያሉ ፡ ሲያለቅሱ ፡ ተሰሙ ።

477 አትሠሪ ፡ እንኳ ፡ ሥራ ፡ ለስልሶ ፡ እንደሆን ፡
—እስኪ ፡ እጅሽን ፡ ልየው ፡ ወይዘሮ ፡ ስኂን ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ወይዘሮ ፡ ስኂን ፡ የእጅሽን ፡ መለስለስ ፡ እስቲ ፡ ልይልሽ ።

ወ ፡ እስቲ ፡ ዳረጎት ፡ አድርጊልኝ ፤ በስጦታሽ ፡ ደጕሚኝ ።

478 አትሮጥም ፡ ይሉኛል ፡ አይደለሁ ፡ ደንዳና ፤
—ልከው ፡ ያስጠይቁኝ ፡ እበረለሁና ።

ሠ ፡ እሮጣለሁ ፤ ከተፎ ፡ ነኝ ።

ወ ፡ ከበር ፡ ቆሚያለሁና ፡ አጋፋሪውን ፡ ልከው ፡ ያስጠሩኝ ።

479 አትሥጋ ፡ ይሉኛል ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አልሠጋ ፤
—ከዱር ፡ እያደርኩኝ ፡ ተሸክሜ ፡ ሥጋ ።

ሠ ፡ ሥጋ ፡ ይዤ ፡ በዱር ፡ በጫካ ፡ ውስጥ ፡ ሳድር ፡ እንደ ፡ ምን ፡ መሥ ጋት ፡ መፍራት ፡ ይቅርብኝ ፤ ሥጋ ፡ የሸተተው ፡ አውሬ ፡ ቢበላኝስ ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሆኜ ፡ ተፈጥሬ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ መሥጋት ፡ መጨነቄ ፡ ይቅር ፤ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ አይደለሁምን ።

480 አትከለክልም ፡ ወይ ፡ ይዘህ ፡ ዐለንጋህን ፡
—አሞራ ፡ ሲበላው ፡ የገዛ ፡ ሥጋህን ።

ሠ ፡ ለመመገብ ፡ የምታስወስደውን ፡ ሥጋ ፡ አሞራ ፡ እየተናጠቀ ፡ ሲበ ላው ፡ ለምን ፡ ዝም ፡ ትላለህ ፤ ዐለንጋህን ፡ ይዘህ ፡ አትከላከልምን ።

ወ ፡ የወንድምህን ፡ ሥጋ ፡ አሞራ ፡ እየተበጫጨቀ ፡ በላው ፤ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ወድቆ ፡ ያሞራ ፡ ሲሳይ ፡ ሆነልህ ።

481 አትወራረዱ ፡ እናንተ ፡ በመልኩ ፤
—እጅግ ፡ ያማረ ፡ ነው ፡ ይኸ ፡ ልጅ ፡ ታሪኩ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ በመልኩ ፡ አትወራረዱ ፤ የፈጸመውም ፡ ታሪክ ፡ የሚያኰራ ፡ እኮ ፡ ነው ።

ወ ፡ የታሪኩ ፡ ቂመናና ፡ ተፈጥሮ ፡ እጅግ ፡ ያምራል ፤ ውብ ፡ ነው ።

482 አትወረድ ፡ አላልኩም ፡ ከፍርታ ፡ በታች ፡
—ደንቢያ ፡ ከብት ፡ ያለምዳል ፡ እንኳን ፡ የሰው ፡ ልጅ ።

ሠ ፡ ደንቢያ ፡ መልካም ፡ አገር ፡ ነው ፤ ሁሉን ፡ ያለምዳል ፤ እንኳን ፡ ለ ሰው ፡ ለከብት ፡ መኖሪያ ፡ ይስማማል ።

ወ ፡ ደንቢያ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ከሄድኩ ፡ አትመለስም ፤ በታው ፡ ሰው ፡ ያለምዳል ፤ ያገሩም ፡ ውሃ ፡ የጠጣ ፡ ሰው ፡ አይመለስም ፤ እዚያው ፡ ይቀራል ።

483 አቶ ፡ ገብረ ፡ ማርያም ፡ ተሰቅሏል ፡ ዳዊቱ ፡
—አውርዳችሁ ፡ ስጧት ፡ ተያገመች ፡ እቱ ።

ሠ ፡ ዳዊት ፡ ለመድገም ፡ ከቻለች ፡ አውርዳችሁ ፡ ስጧት ።
ወ ፡ እኅቱም ፡ ተከትላው ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ጠፋች ፤ በሞት ፡ ተደገመች ።

484 አነስ ፡ አነስ ፡ ብሏል ፡ ፈረስ ፡ አሳቢው ፡
—መጣብርህን ፡ ሸጠህ ፡ ግዛ ፡ ተጣፋው ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ መጣብርህን ፡ ሸጠህ ፡ ጣፋ ፡ ግዛ ።
ወ ፡ (ተጣፋ) ፡ ተሻኰት ፤ ተጋደል ።

485 አንለፍ ፡ በዚያ ፡ እኩል ፡ አንይ ፡ መንገዱን ፤
—መኰንን ፡ ጌታችን ፡ ያለፈበትን ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ)፡

ሠ ፡ ጌታችን ፡ መኰንን ፡ የሄደበትን ፡ መንገድ ፡ አንመልከተው ፤ ወዴት ፡ ሄደ ፡ ብሎ ፡ መመርመር ፡ አይገባንም ።
ወ ፡ ጌታችን ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ የሞተበትን ፡ ሕይወቱ ፡ ያለፈበትን ፡ አደጋ ፡ የደረሰበትን ፡ መንገድ ፡ ባናየው ፡ ይሻላል ።

486 አንበሳና ፡ ጐፈር ፡ የዚያ ፡ ሁሉ ፡ ሰልፍ ፡
—ግርም ፡ ያደርገኛል ፡ የብሩ ፡ መርገፍ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ከአንበሳው ፡ ጐፈር ፡ ከመረሻቱ ፡ ተካባና ፡ ተላንቃ ፡ ሁሉ ፡ የብሩ ፡ መርገፍ ፡ ያስገርመኛል ፤ ያስደንቀኛል ።
ወ ፡ የራስ ፡ ብሩ ፡ መሞት ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ረግፎ ፡ መቅረት ፡ እጅግ ፡ ያሳዝነኛል ፤ አንዠቴን ፡ ይበላዋል ።

487 አንተ ፡ ለሽልማት ፡ ምን ፡ አስቸኰለህ ፤
—መቼም ፡ ቢሆን ፡ መርገፍ ፡ ላንተ ፡ አይቀርብህ ።

ሠ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ መሸለምህ ፡ ፈረስ ፡ በቅሎ ፡ ከነመሣሪያው ፡ ከነመርገፉ ፡ ማግኘትህ ፡ አይቀርምና ፡ አትቸኵል ።
ወ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ሰው ፡ ነህና ፤ መሞትና ፡ ዐፈር ፡ መሆን ፡ አይቀርልህም ።

488 አንተ ፡ ልጅ ፡ አጥብቀህ ፡ ልጓሙን ፡ ያዘው ፡
—በቅሎ ፡ አያውቅምና ፡ እንዳንት ፡ ያለ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ በቅሎ ፡ መቀመጥ ፡ ልጓም ፡ መጨበጥ ፡ እንዳንተ ፡ ያለ ፡ ልጅ ፡ አይሆንለትም ፤ ትወድቃለህ ፡ ይቅርብህ ።
ወ ፡ እንዳንተ ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ አልተወለደም ፤ አልተፈጠረም ።

(1) ባ፲፱፻፳፯ ፡ ዓ ፡ ም ፡ በነሐሴ ፡ ወር ፡ መሳፍንቱ ፡ መኳንንቱና ፡ ወይዛዝሩ ፡ ለጦር ፡ ርዳታ ፡ ይሆን ፡ ዘንድ ፡ የበቅሎ ፡ ዶቃ ፡ የጐፈር ፡ ጕብጕብ ፡ አቍዳማ ፡ ቢተዋ፡ ማልደያ ፡ ጫማ ፡ ሙጣ ፡ ማፈኛ ፡ የብር ፡ ሰገባ ፤ ሽሆር ፡ አሸን ፡ ክታብ ፡ ወለባ ፡ የእጅና ፡ የእግር ፡ ድኰትና ፡ አንባር ፡ ጠልሰም ፡ የእግር ፡ አልቦ ፡ ድሪና ፡ ቀለበት ፡ ጌጣቸውን ፡ በፈቃዳቸው ፡ በሰጡ ፡ ጊዜ ፡ የተገጠመ ።

489 አንተ ፡ ማዶ ፡ ሁነህ ፡ ምንም ፡ አላየህም ፤
—ተቈላ ፡ ፍጥረትህ ፡ አንድ ፡ አልቀረልህም ።

ሠ ፡ የቈላው ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ ሳይቀር ፡ ሄደ ፤ ተወሰደ ።
ወ ፡ ሕዝብህ ፡ ተቸገረ ፤ ተቈላ ፡ ተሠቃየ ፤ መከራውን ፡ አየ ፤ ግራ ፡ ገባው ።

490 አንተም ፡ ታውቀዋለህ ፡ ያልጋውን ፡ መወደድ ፤
—እንግዛህም ፡ ቢሉ ፡ ተዋጋው ፡ አትውረድ ። (ነ ፡ ተ ፡ አ) ፡

ሠ ፡ ዋጋ ፡ አትቀንስ ፤ አትበለጥ ፤ ዝቅ ፡ አድርገህ ፡ አትሽጥ ።
ወ ፡ በጦርነት ፡ ገጥመህ ፡ ጠላትህን ፡ ተዋጋው ፤ አገርህን ፡ አታስወስድ ፤ መንግሥትህን ፡ አትልቀቅ ።

491 አንተም ፡ እንዳትተወኝ ፡ እንዳልቀር ፡ ዐውቃለሁ ፤
—በጊዜ ፡ ውሰደኝ ፡ ጨለማ ፡ እፈራለሁ ።

ሠ ፡ ሳይመሽ ፡ ሳይጨልም ፡ ውሰደኝ ፤ በብርሃን ፡ እቤቴ ፡ ልግባ ።
ወ ፡ ሳልገሥጽ ፤ አእምሮዬ ፡ ሳይሳሳተኝ ፤ የማይቀረው ፡ ሞት ፡ በጊዜ ፡ ይውሰደኝ ።

492 አንተንም ፡ ብቀድምህ ፡ አንተም ፡ ብትቀድመኝ ፡
በዳሞቱ ፡ መንገድ ፡ እንድትጠብቀኝ ፤
—እሱ ፡ ነው ፡ ጐዳናው ፡ ሁሉን ፡ አገናኝ ።

ሠ ፡ ማናቸውም ፡ መንገደኛ ፡ የሚያልፈው ፡ በዳሞቱ ፡ መንገድ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ኬላ ፡ ያለ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ሌላ ፡ ማለፊያ ፡ የለውም ።
ወ ፡ ጌታም ፡ ሆነ ፡ ድኻ ፡ ልጅ ፡ ሆነ ፡ ሽማግሌ ፡ በሞት ፡ ጊዜ፡ መንገዱ ፡ ለሁሉም ፡ እኩል ፡ ነው ።

493 አንተ ፡ የምታውቀው ፡ ብቻ ፡ መዋልን ፤
—ልጄ ፡ ለመድከው ፡ ወይ ፡ ታዞ ፡ መኖርን ። (ዘለ ፡ ቊ ፡ 566 ፡ 1090) ፡

ሠ ፡ ታዛዥነትን ፡ ለመድከውን ፡ ለጌታ ፡ አድሮ ፡ መኖርን ፡ ዐወቅህበትን ።
ወ ፡ በዐዞ ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ መኖርን ፡ ለመድከው ፡ ወይ ፤ ዐዞ ፡ በላህን ።

494 አንተ ፡ የኔ ፡ ወንድም ፡ በቶሎ ፡ አትመጣም ፡ ወይ ፤
—ከተማሰው ፡ ገብቶ ፡ አይመለስም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ እከተማ ፡ ገብቶ ፡ አይመለስምን ፤ በዚያው ፡ እንዴት ፡ ይቀራል ።
ወ ፡ ሞቶ ፡ ከተማሰ ፡ ጕድጓድ ፡ ገብቶ ፡ ተቀበረ ፤ ግብአተ ፡ መሬት ፡ ተደረሰለት ፤ እንግዲህ ፡ አይመለስም ።

495 አንቱ ፡ ሞኝ ፡ እኔ ፡ ሞኝ ፡ ሁላችን ፡ እንስሳ ፤
—ብዙ ፡ ስንጫወት ፡ ሞትን ፡ ሳናነሣ ።

ሠ ፡ በጨዋታችን ፡ ላይ ፡ ሞትን ፡ ሳናስታውስ ፡ ቀረን ፤ ስለ ፡ ርሱ ፡ ም ንም ፡ አልተነጋገርንም ።

ወ ፡ ሞት ፡ በድንገት ፡ ደረሰ ፤ ሳናስበው ፡ መጥቶ ፡ ለያየን ።

496 አንቺ ፡ ሴት ፡ ቸኵለሽ ፡ ባልሽን ፡ እንዳትንቂው ፤
የድኻ ፡ ልጅ ፡ ብለሽ ፡ ትውልዱን ፡ ሳታውቂው ፤
—ባላባትነቱን ፡ መርምረሽ ፡ ተረጂው ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 508) ፡

ሠ ፡ የባላባት ፡ ልጅነቱን ፡ ዕወቂው ፤ የትልቅ ፡ ሰው ፡ ወገን ፡ መሆኑን ፡ ተረጂው ፤ ቀላል ፡ ሰው ፡ መስሎሽ ፡ እንዳትንቂው ።

ወ ፡ ባል ፡ እንደ ፡ አባት ፡ የሚያዝን ፡ የሚረዳ ፡ መሆኑን ፡ ዕወቂው ።

497 አንኮበር ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ ቍንዲ ፡ አልታይ ፡ አለኝ ፡
—በጉም ፡ ተሸፍኖ ፡ እየተሰወረኝ ። (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ ጉም ፤ ጭጋግ ፡ ሸፍኖት ፡ ደመና ፡ ከልሎት ፡ አልታይም ፡ አለኝ ፡ እሳ።

ወ ፡ የበጉ ፡ ሥጋ ፡ ተሸፍኖ ፡ ከመጋረጃው ፡ ግቢ ፡ እየታየኝ ፡ እንደ ፡ ጐመ ዠሁ ፡ ሳልቀምሰው ፡ ቀረሁ ።

498 አንኮበርን ፡ ትቼ ፡ ስሄድ ፡ በምናኔ ፡
—አመሰግናለሁ ፡ ሳማ ፡ አልሄድም ፡ እኔ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 39) ፡ (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ እያማሁ ፡ አልሄድም ፤ እውነቱን ፡ ተናግሬ ፡ የሚያደርጉኝን ፡ እቀበ ላለሁ ።

ወ ፡ ሳማ ፡ ሰንበት ፡ ገዳም ፡ አልሄድም ፤ እሱን ፡ መሸም ፡ አልፈቅድም ።

499 አንድ ፡ ላም ፡ አለችኝ ፡ ሆዴ ፡ የሚወዳት ፤
—እናት ፡ በቅሎ ፡ ባገኝ ፡ በለወጥሁባት ።

ሠ ፡ ለኮርቻ ፡ የምትሆን ፡ የደረጀች ፡ በቅሎ ፡ ባገኝ ፤ ጥገት ፡ ላም ፡ ሰጥቼ ፡ በቅሎዋን ፡ እወስድ ፡ ነበር ።

ወ ፡ እናት ፡ እንደ ፡ እኽል ፡ የምትበቅል ፡ ብትሆን ፡ እንዴት ፡ ደስ ፡ ባ ለኝ ፡ ነበር ።

500 አንድ ፡ ልጅ ፡ ብወልዳት ፡ ተሳዳቢ ፡ ሆነች ፤
—እርስዎንም ፡ ራስ ፡ ባሪያ ፡ ትልዎታለች ።

ሠ ፡ ርስዎን ፡ እንኳን ፡ ታላቁን ፡ ራስ ፡ ባሪያ ፡ እያለች ፡ ለመስደብ ፡ የማ ትመለስ ፡ ናት ።

ወ ፡ አገልጋይ ፡ ይስጡኝ ፡ እያለች ፡ ትለምንዎታለች ።

501 አንድም ፡ ዳኛ ፡ የለ ፡ አብረው ፡ ከመጧቸው ፤
—ሙሉጌታ ፡ ሄዷል ፡ ሊያፈጣጥማቸው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ሊያፈጣጥም ፡ የቀጠሮውን ፡ ቀን ፡ ሊወስን ፡ ዳኛው ፡ ተልኮ ፡ ሄዷል ።

ወ ፡ የጦር ፡ አበ ፡ ጋዙ ፡ ራስ ፡ ሙሉጌታ ፤ ሰራዊቱን ፡ ሊያዋጋ ፡ ጠላትን ፡ ሊያስጨፈጭፍና ፡ ሊፈጅ ፡ ወደ ፡ ጦር ፡ ግንባር ፡ ሄዷል ።

502 አንድ ፡ እቅፍ ፡ ጭራሮ ፡ ሳልሰጥ ፡ ዐይኔ ፡ ሲያይ ፤
—ሌላው ፡ በሠራው ፡ ቤት ፡ ያስገባኛል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ባልሠራሁት ፡ ቤት ፡ ማን ፡ ያስገባኛል ፤ በሰው ፡ ቤት ፡ ማን ፡ ያስቀ ምጠኛል ።

ወ ፡ አንዱ ፡ በሠራው ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ሌላው ፡ ገነት ፡ መግባት ፡ አይችልም ።

503 አንድ ፡ እንኳ ፡ ሰው ፡ ሳይቀር ፡ ለጐበዝ ፡ ሰብሳቢ ፡
—ወጥተን ፡ ደክመን ፡ መጣን ፡ አልተገኘም ፡ ካቢ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ሕዝቡ ፡ ለሥራ ፡ ድንጋይ ፡ ለማቀበል ፡ ቢወጣ ፡ ገንቢ ፡ አል ተገኘም ።

ወ ፡ ለነፍሱ ፡ አስቦ ፡ ሥጋውን ፡ በድሎ ፡ ወደ ፡ ካቢ ፡ ገዳም ፡ የሚሄድ ፡ ታጣ ።

504 አንድ ፡ እንጀራ ፡ ለኔ ፡ መስተዋቴ ፡ ነሽ ፤
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ ታሳይኛለሽ ።

ሠ ፡ የእንጀራው ፡ ሰበከት ፡ እንደ ፡ መስተዋት ፡ ፊቴን ፡ ያሳየኛል ።

ወ ፡ በማጣት ፡ በመቸገር ፡ እየሰዉ ፡ ደጅ ፡ በቆምኩና ፡ በለመንኩ ፡ ጊዜ ፡ የመጽዋቹ ፡ ርጎራጌና ፡ ጭካኔ ፡ በየፊቱ ፡ ተገልጦ ፡ ይታየኛል ።

505 አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተቈርጦ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተላጭቶ ፡
—እንግዲህ ፡ የሚያምር ፡ ምን ፡ ራስ ፡ ተገኝቶ ። (ቀኛ ፡ ጎ ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ ያለጠጕር ፡ ምን ፡ ያምራል ፤ ምን ፡ ደስ ፡ ያሰኛል ።

ወ ፡ ካንተ ፡ ወዲያ ፡ ለጋስ ፡ ሰራዊት ፡ አስተዳዳሪ ፡ ፍርድ ፡ ዐዋቂ ፤ ምን ፡ ራስ ፡ ይገኛል ፤ አንተን ፡ የሚያኽል ፡ ጌታ ፡ ከወዴት ፡ ይመጣል ።

506 አንድ ፡ ጨው ፡ ነበረኝ ፡ ሳልሸምትበት ፡
—ገበያው ፡ ተፈታ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት።

ሠ ፡ የተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ገበያ ፡ ተበተነ ፤ ሕዝቡ ፡ እቤቱ ፡ ገባ ።

ወ ፡ የሰራዊት ፡ ጌታ ፡ የነበረው ፡ ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ሞተ ፤ ተቀ በረ ።

507 አንጥረኛው ፡ ብዙ ፡ በቴዎድሮስ ፡ ቤት ፡
—ባላልቦ ፡ አደረጉት ፡ ይህን ፡ ሁሉ ፡ ሴት ። (1)

ሠ ፡ ሴቱን ፡ ሁሉ ፡ የእግር ፡ አልቦ ፡ ሸለሙት ፤ አስጌጡት ።
ወ ፡ ሴቱን ፡ ያለባል ፡ አስቀሩት ፤ ወንድ ፡ ወንዱን ፡ ገደሉት ።

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ጐንደርን ፡ አጥፍተው ፡ ወደ ፡ ደብረ ፡ ታቦር ፡ ሲሄዱ ፡ ቍጥራቸው ፡ ፭፻ ፡ በሚሆኑ ፡ በሚሸሹ ፡ ሰዎች ፡ ላይ ፡ ድንገት ፡ ደረሱና ፡ ሴት ፡ ሴቱን ፡ አስቀርተው ፡ ወንድ ፡ ወንዱን ፡ አስገደሉት ፤ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ በሬሳው ፡ ላይ ፡ ከቀሩት ፡ ሴቶች ፡ በሐ ዘን ፡ የተነካች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ የገጠመችው ።

508 አኖረው ፡ ነበረ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ንቄ ፤
—ባላባት ፡ መሆኑን ፡ እኔ ፡ የት ፡ ዐውቄ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 496) ፡

ሠ ፡ የታላቅ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ መሆኑን ፡ ወገኑን ፡ ትውልዱን ፡ አልተረዳሁም ፤ አላወቅሁም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ባል ፡ እንዳባት ፡ ረዳት ፡ አሳቢ ፡ መሆኑን ፡ አላወቅሁም ፡ ነበር ። ባል ፡ አባት ፡ መምሰሉን ፡ መቼ ፡ ተረዳሁት ።

509 አኖራት ፡ ነበረ ፡ በክብር ፡ በተድላ ፤
—ባልጋ ፡ ሄደችብኝ ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ልበላ ።

ሠ ፡ ባልጋ ፡ ተሞላቃ ፡ ሄደች ፤ ተንዘልዝላ ፡ ኰበለለች ።

ወ ፡ ሞታ ፡ አስከሬኗ ፡ በአልጋ ፡ ሆኖ ፡ ተጓዘ ፤ በቃሬዛ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተወሰደ ፤ ምን ፡ ላደርግ ፡ እችላለሁ ።

510 አክርማ ፡ ለመቅጨት ፡ ሲነሡ ፡ ሲወድቁ ፡
—መወጠን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ መስፋትም ፡ አያውቁ ።

ሠ ፡ ስፌት ፡ መስፋት ፡ አያውቁም ፤ የእጅ ፡ ሥራ ፡ አልተማሩም ።

ወ ፡ አያድጉም ፤ በልጅነታቸው ፡ ይሞታሉ ፤ አንዱን ፡ ሳይዙት ፡ ይቀጫሉ ፤ እቁም ፡ ነገር ፡ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ አይደርሱም ።

511 አወይ ፡ ባለጌነት ፡ እግዜርን ፡ ማማረር ፡
—ሌላ ፡ ሰው ፡ ይመስል ፡ እናት ፡ አለማፈር ።

ሠ ፡ እናትን ፡ አለመፍራት ፡ አለማክበር ፡ አይገባም ፤ ብልግና ፡ ነው ።

ወ ፡ ዓለም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የነበረችው ፡ እናት ፡ ሞተችብኝ ፤ ዐፈር ፡ ሆነች ።

512 አዋዜ ፡ አልኩህ ፡ እንጂ ፡ ሥጋማ ፡ ምን ፡ ገዶ ፤
—ረቡ ፡ የጋድ ፡ ለት ፡ ድፍን ፡ ጐዣም ፡ ታርዶ ።

ሠ ፡ ረቡ ፡ የጋድ ፡ ቀን ፡ በድፍን ፡ ጐዣም ፡ ከብት ፡ ታረደ ፤ ሥጋ ፡ በሥጋ ሆነ ።

ወ ፡ ረቡ ፡ ለት ፡ የጋድ ፡ ቀን ፤ በጐዣም ፡ እልቂት ፡ ሆነ ፤ ብዙ ፡ ሰው ፡ ታረደ ፡ ሞተ ።

513 አውሬ ፡ እናድን ፡ ብሎ ፡ ጐዣሜ ፡ ተጣራ ፡
—ምናልባት ፡ ሰው ፡ ቢሆን ፡ እኔስ ፡ ሆዴ ፡ ፈራ ።

ሠ ፡ አውሬ ፡ እንቀሰቅሳለን ፡ ብሎ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ አደጋ ፡ እንዳያደርስ ፡ እሠጋለሁ ፤ የሰው ፡ ሕይወት ፡ በከንቱ ፡ እንዳያልፍ ፡ እፈራለሁ ።

ወ ፡ ምናልባት ፡ እግዚአብሔር ፡ እንሥቶት ፡ ተኸ ፡ የሆነ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ቂሙን ፡ እንዳይወጣብኝ ፡ እሠጋለሁ ።

514 አውሬው ፡ በረከተ ፡ ዱሩን ፡ ቀሰቀሰው ።
—እንዳልሸኝህ ፡ እንኳ ፡ ራሴ ፡ እምፈርሰው ።

ሠ ፡ ራሴ ፡ እፈራለሁ ፤ እሠጋለሁ ፤ አውሬው ፡ ከፍቷል ፤ በየዱሩ ፡ አያስተ
ላልፍም ።

ወ ፡ ራሴ ፡ ሖች ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ነኝ ፤ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ከሞት ፡ የሚያመ
ልጥ ፡ አለመኖሩን ፡ እገነዘባለሁ ።

515 አዝማሪና ፡ ዶሮ ፡ የላቸው ፡ አዝመራ ፡
—ታበላቸዋለች ፡ እናታቸው ፡ ጭራ ።

ሠ ፡ እየቈፈረች ፡ እየቧጠጠች ፡ የሚበላውን ፡ እያወጣች ፡ ትመግባቸዋ
ለች ።

ወ ፡ አዝማሪ ፡ ጭራ ፡ በመከርከር ፡ መሰንቆ ፡ በመጫወት ፡ ትዳሩን ፡ አሸ
ንፎ ፡ ሕይወቱን ፡ ይጠብቃል ።

516 አዝን ፡ የነበረ ፡ ልጄ ፡ በማጣቱ ፡
—ዛሬስ ፡ አገኘ ፡ አሉ ፡ ባሕር ፡ ሆነ ፡ ቤቱ ።

ሠ ፡ ሀብት ፡ አገኘ ፤ ባለጸጋ ፡ ሆነ ፤ ትዳሩ ፡ ንብረቱ ፡ ተስፋፋ ።

ወ ፡ ከባሕር ፡ ገብቶ ፡ ሞተ ፤ ማዕበል ፡ አስጥሞት ፡ ዐረፈ ።

517 አያሌ ፡ አገር ፡ ሳለ ፡ እነማይ ፡ በረንታ ፡
—ዲማ ፡ በትቢቱ ፡ በኀይሉ ፡ ተፈታ ።

ሠ ፡ ዲማ ፡ እንደ ፡ ኰራ ፡ ሳይዋረድ ፡ በኰልበቱ ፡ ከጭቈና ፡ ወጣ ።

ወ ፡ ዲማ ፡ በኀይሉ ፡ ገዥነት ፡ ተጕዳ ፤ ተመዘበረ ፤ ተበዘበዘ ።

518 አያስፈልገንም ፡ የማዘን ፡ ብድር ፤
—ብዙ ፡ ማዘን ፡ አለ ፡ ባገራችን ፡ ዱር ።

ሠ ፡ በጫካችን ፡ በዱራችን ፡ ብዙ ፡ የማእዘን ፡ ዕንጨት ፡ ይገኛል ፤ ለጠ
ርብ ፡ ለመቃን ፡ ለሳንቃ ፡ ኵበን ፡ ጥድ ፡ ዝግባ ፡ አለ ።

ወ ፡ ባገራችን ፡ ማዘን ፡ መተከዝ ፡ አለ ፤ መጾም ፡ መጸለይ ፡ ሕግ ፡ ነው ።

519 አያችሁልኝ ፡ ወይ ፡ የዚያን ፡ ሰው ፡ እኅት ፤
—ቆማ ፡ ሣር ፡ ታያለች ፡ የሌላትን ፡ ከብት ።

ሠ ፡ ድርቆሹን ፡ ቆማ ፡ ታያለች ፤ ልክ ፡ ልኩን ፡ ትመለከታለች ።

ወ ፡ በቁሟ ፡ ፍዳዋን ፡ ታያለች ፤ መከራዋን ፡ ትቀበላለች ፤ ቁም ፡ ስቅ
ሏን ፡ ያሳያታል ።

520 አያውቁም ፡ ነበረ ፡ ሰውን ፡ ማሳዘን ፡
—ዛሬስ ፡ አስለቀሱት ፡ ትንሽ ፡ ትልቁን ።

ሠ ፡ ልዑል ፡ እስከ፡ዛሬ ፡ ሰው ፡ አያሳዝኑም ፡ ድኻ ፡ አይበድሉም ፡ ነበር ፤
ዛሬ ፡ የነካቸውን ፡ አናውቅም ፤ ሕዝቡን ፡ ያሳዝኑታል ፤ የደም ፡ እንባ፡
ያስለቅሱታል ።

ወ ፡ የልዑልነታቸው ፡ ዕረፍት ፡ እጅግ ፡ አሳዛኝ ፡ ሆነ ፤ ትንሽ ፡ ትልቁን ፡
አስለቀሰው ።

521 አይሮፕላናችን ፡ ከሄደ ፡ ዘገየ ፡
—የያዘውን ፡ ዕቃ ፡ ጥሎስ ፡ እንደሁ ፡ ማ ፡ አየ ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የጫነውን ፡ ዕቃ ፡ ከተላከበት ፡ አድርሶ ፡ ይጣለው ፡ አይጣለው ፡ ማን፡ አየ ፤ ማን ፡ ዐወቀ ።

ወ ፡ ማየ ፡ የሚባለው ፡ አይሮፕላን ፡ ነጂ ፡ የያዘውን ፡ ቦምብ ፡ በጠላት ፡ ላይ ፡ ሳይጥለው ፡ የቀረ ፡ አይመስልም ።

522 አይበረክትላት ፡ የያዘችው ፡ ሁሉ ፤
—ያንን ፡ የሰው ፡ ሸክላ ፡ ሰብራው ፡ መጣች ፡ አሉ ።

ሠ ፡ የተዋሰችውን ፡ ሸክላ ፡ ሰበረችው ፤ የሰው ፡ እንስራ ፡ አደቀቀች ።

ወ ፡ ባል ፡ አይቆምላትም ፤ ደግሞ ፡ አሁን ፡ ያገባችው ፡ አዲሱ ፡ ባሏ ፡ ዐረፈን ።

523 አይታለብበት ፡ አይጮኽበት ፡ ላም ፤
— ምነው ፡ እመጫቷን ፡ ከንፍሮ ፡ ገዳም ። (2) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 792) ፡

ሠ ፡ ወተት ፡ ከሌለበት ፡ ላም ፡ ከማይገኝበት ፡ ለምን ፡ እመጫቷን ፡ አስቀመጧት ።

ወ ፡ በወሊድ ፡ የሞተችውን ፡ እመጫት ፡ አገዳም ፡ ቀበሯት ።

524 አይዋ ፡ ተሰማን ፡ ሄጄ ፡ አዋየዋለሁ ፤
— በቅሎ ፡ ጠፋው ፡ ሲሉ ፡ ማታ ፡ ሰምቻለሁ ። (3)

ሠ ፡ በቅሎ ፡ ጠፋበት ፡ ማለትን ፡ ሰምቻለሁና ፡ ሄጄ ፡ ላዋየው ፤ ላጽናናው ።

ወ ፡ ወጣት ፡ ልጅ ፡ ስለ ፡ ሞተበት ፡ ሄጄ ፡ ከለቅሶው ፡ ልድረስ ፤ ከሐዘኑ ፡ ላረጋጋው ።

525 አይዙም ፡ ወይ ፡ ጥላ ፡ እንደ ፡ ሰዉ ፡ ሁሉ ፤
— በዚህ ፡ በረሞጫ ፡ በፀሐይ ፡ በሰሉ ።

ሠ ፡ በፀሐይ ፡ ኀይል ፡ ተቃጠሉ ፤ ሙቀቱ ፡ ጐዳዎ ፤ አደከመዎ ።

ወ ፡ በልጅዎ ፡ በፀሐይ ፡ (ልዕልት) ፡ ሞት ፡ ሐዘኑ ፡ ጠነከረብዎ ፤ ጸጸቱ ፡ ካንዠትዎ ፡ የማይወጣ ፡ ሆነ ።

---

(1) በአንችም ፡ ጦርነት ፡ ጊዜ ፡ ባ፲፱፻፳፪ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ካዲስ ፡ አበባ ፡ የተላከውን ፡ አይሮፕላን ፡ የሚነዳው ፡ በራሪ ፡ «ማየ» ፡ የሚባለው ፡ ፈረንሳይ ፡ ቦምብ ፡ መጣል ፡ አለመጣሉን ፡ ስለ ፡ መጠያየቅ ፡ የተገጠመ ።

(2) የራስ ፡ ከበደ ፡ ሚስት ፡ ወይዘሮ ፡ ምንትዋብ ፡ ወሌ ፡ በወሊድ ፡ ምክንያት ፡ ሞተው፡ ደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ ሲቀበሩ ፡ የተለቀሰ ።

(3) በጌምድር ፡ ውስጥ ፡ ተሰማ ፡ ጐሹ ፡ የሚባል ፡ ባለጠጋ ፡ ሰው ፡ ነበር ፤ መካን ፡ ሆኖ ፡ ሲኖር ፡ በስተርጅና ፡ ያገኘውን ፡ ልጅ ፡ እያንቀባረረ ፡ አሳድጎ ፡ ለአካለ ፡ መጠን ፡ ካደረሰው ፡ በኋላ ፡ ይህ ፡ ልጅ ፡ አውሬ ፡ አደን ፡ ሄዶ ፡ በድንገት ፡ ስለ ፡ ሞተ ፡ አክሥቱ ፡ ያለቀሰችው ።

526 አይዞሽ ፡ ብሎ ፡ ወስዶ ፡ እንደውነቱ ፡ ሁሉ ፡
— ከባዶ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ቀን ፡ ጥሏት ፡ ሄደ ፡ አሉ ።

ሠ ፡ ከአውላላ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ጥሏት ፡ ዐጕል ፡ ቦታ ፡ ብቻዋን ፡ ትቷት ፡ ሄዷል ፡ አሉ ።

ወ ፡ አንገቷን ፡ ቀልቷት ፤ ቈራርጦና ፡ በጣጥሷት ፡ ሄደ ።

527 አይጣል ፡ አይጣል ፡ እያልን ፡ ስንለምነው ፡
— ሳናስበው ፡ ድንገት ፡ ጣለብን ፡ ምነው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እንዳይዘንም ፡ እግዚአብሔርን ፡ ብንለምንም ፡ ዳምኖ ፡ አልቀረም ፤ የፈራነው ፡ ዝናምና ፡ በረዶ ፡ ዘነመ ።

ወ ፡ ያላሰብነውን ፡ ያልጠረጠርነውን ፡ ዱብ ፡ ዕዳ ፡ ፈጣሪያችን ፡ ምነዋ ፡ አመጣብን ፤ ቦምብ ፡ ወደቀብን ።

528 አደባባይ ፡ ቆሜ ፡ አያለሁ ፡ ዝም ፡ ብዬ ፤
— ማቅን ፡ የለበሰ ፡ አገኛለሁ ፡ ብዬ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ በርኖስ ፡ የለበሰ ፡ ዝተት ፡ የደረበ ፡ አገኛለሁ ፡ በማለት ፡ አደባባይ ፡ ቆሜ ፡ እመለከታለሁ ።

ወ ፡ ቅን ፡ ሐሳብ ፡ ያለው ፡ በጎ ፡ ፈቃድ ፡ ያልተለየው ፡ እሁን ፡ ማንን ፡ አገኛለሁ ፡ ብዬ ፡ እፈልጋለሁ ።

529 አደባባይ ፡ ቆሞ ፡ አበጀሁ ፡ ቢላችሁ ፤
— ይህን ፡ ባለ ፡ ጊዜ ፡ ምን ፡ ትሉታላችሁ ።

ሠ ፡ ይኸንን ፡ የመሰለ ፡ ቃል ፡ ቢናገራችሁ ፡ ምን ፡ መልስ ፡ ትሰጡታላችሁ ።

ወ ፡ ይኸንን ፡ ዘመናይ ፤ እንደ ፡ ልቡ ፡ ተናጋሪ ፤ የፈቀደውን ፡ አድራጊ ፤ ምን ፡ ልታደርጉት ፡ ትችላላችሁ ። ዘመን ፡ የረዳውን ፡ አትጋፉት ፤ ዐርፋችሁ ፡ ተቀመጡ ።

530 አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ ቡና ፡ ቢወደድ ፤
— ከጅማ ፡ ሰው ፡ ካለ ፡ ይመጣል ፡ በግድ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ ላይ ፡ ቡና ፡ ቢወደድም ፡ ጫኚ ፡ ከተገኘ ፡ ከጅማ ፡ ማምጣት ፡ ይቻላል ፤ ጅማ ፡ የቡና ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ አይቸግርም ።

ወ ፡ ከዳተኛ ፡ ለመንግሥቱ ፡ የማይታዘዝ ፡ ሽፍታ ፡ ባገር ፡ ካለ ፡ በግድ ፡ ተይዞ ፡ ይመጣል ፤ አምልጦ ፡ ለመቅረት ፡ አይችልም ።

531 አዲስ ፡ አዲሱ ፡ ልብስ ፡ ዋጋው ፡ እየበዛ ፡
— እንዴት ፡ እንሆናለን ፡ ልብስ ፡ ሳንገዛ ።

ሠ ፡ አሮጌ ፡ ጨርቅ ፡ መግዛት ፡ አለብን ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ ውራጅ ፡ መልበስ ፡ ያሻናል ።

ወ ፡ ያለፈውን ፡ ልብ ፡ ለማድረግ ፡ የቀድሞውን ፡ ለመገንዘብ ፡ ካልቻልን ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ማሰብ ፡ ምን ፡ ያደርግልናል ።

532 አዳም ፡ ከሚባለው ፡ ከሱ ፡ ተፈጥሬ ፡
— ለሰው ፡ አስባለሁ ፡ የራሴን ፡ አኑሬ ።

ሠ ፡ የራሴን ፡ ጕዳይ ፡ ትቼ ፡ ለሰው ፡ እለፋለሁ ፤ እጥራለሁ ።
ወ ፡ የነፍሴን ፡ ነገር ፡ ለራሴ ፡ ሳላውቅ ፡ ለሰው ፡ መካሪና ፡ አሳቢ ፡ መሆኔ ፡ ያስገርማል ።

533 አዳምጠኝ ፡ ወንድሜ ፡ ጕዳቴን ፡ ልንገርህ ፤
— ዘሬ ፡ ጠፍቷልና ፡ ከበቀለ ፡ ወዲህ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ የዘራሁት ፡ በቅሎ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ጠፋ ፤ አዝመራዬ ፡ በቡቃያነቱ ፡ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ።
ወ ፡ ልጄ ፡ በወጣትነቱ ፡ ሞተ ፤ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ ሳይደርስ ፡ ቀረ ።

534 አዳራሹ ፡ ሰፊ ፡ በሩ ፡ አልጠበባችሁ ፤
— በተራ ፡ በተራ ፡ ምነው ፡ መግባታችሁ ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ በሩ ፡ ሳይጠብ ፡ መግቢያ ፡ ሳይጠፋ ፡ ለምን ፡ አንድ ፡ ባንድ ፡ በመከታተል ፡ እየገባችሁ ፡ ጊዜ ፡ ትወስዳላችሁ ።
ወ ፡ በራብተኛ ፡ በችግረኛ ፡ ሰው ፡ ፋንታ ፡ ለምን ፡ ትገባላችሁ ፤ የድኻውን ፡ ጕዳይ ፡ ለምን ፡ ታሰናክሉበታላችሁ ።

535 አዳራሹ ፡ ዝግ ፡ ነው ፡ እልፍኙ ፡ ተከፍቷል ፤
— ያን ፡ የራስ ፡ ዐሊን ፡ ቤት ፡ ማን ፡ ይገባበታል ።

ሠ ፡ በራስ ፡ ዐሊ ፡ ቤቶች ፡ ማን ፡ ሊኖርባቸው ፡ ሊቀመጥባቸው ፡ ይችላል ።
ወ ፡ በግዛታቸው ፡ ማን ፡ ይተካበታል ፤ እንደሳቸው ፡ አድርጎ ፡ ሕዝቡን ፡ ማን ፡ ያስተዳድረዋል ።

536 አዳራሽ ፡ መጋበዝ ፡ ለመደና ፡ ሰው ፡
— እዳስ ፡ መብላት ፡ ሆነ ፡ የሚያስለቅሰው ።

ሠ ፡ እዳስ ፡ መብላት ፡ መጋበዝ ፡ ያጸጽተው ፡ ያሳዝነው ፡ ዠመር ።
ወ ፡ ሰውን ፡ የሚያሳዝነውና ፡ የሚያስለቅሰው ፡ የበላው ፡ የጠጣው ፡ ስጦታውና ፡ ቸርነቱ ፡ እያሳሰበው ፡ ነው ።

537 አዳራሽና ፡ እልፍኝ ፡ ብከለከልም ፡
— ምንም ፡ ቢቸግረኝ ፡ እዳስ ፡ አልገባም ።

ሠ ፡ ከዳስ ፡ ከዛኒጋባ ፡ ከድንኳን ፡ አልገባም ።
ወ ፡ ምንም ፡ ቢቸግረኝ ፡ ገንዘብ ፡ አልበደርም ፤ ዕዳ ፡ ገብቼ ፡ ለልጆቼ ፡ ችግር ፡ አላቈይም ።

538 አዳራሽ ፡ ገብቼ ፡ አልፎክርም ፡ ወይ ፤
እልፍኝ ፡ ተጠርቼ ፡ አልፎክርም ፡ ወይ ፤
— እንደኔ ፡ ማን ፡ አለ ፡ ባላባት ፡ ገዳይ ። (1)

ሠ ፡ የትልቅ ፡ ሰው ፡ ልጅ ፡ ገዳይ ፤ ባለጐሣ ፡ ድል ፡ አድራጊ ፡ ነኝ ።
ወ ፡ የሚያስብልኝ ፡ የሚያዝንልኝ ፡ ባሌ ፡ ሞተብኝ ፤ ዕድሌ ፡ እንዳባቴ ፡
ደግ ፡ የነበረ ፡ ባለቤቴን ፡ ገደለብኝ ።

539 አዳጊዎች ፡ ናቸው ፡ ልጆችዎ ፡ ሁሉ ፤
ትንሹን ፡ ትልቁን ፡ መለየት ፡ አይችሉ ፤
ምንም ፡ አልታወቀ ፡ አልተረጋገጠ ፤
— ባካል ፡ ሆነ ፡ በመልክ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ በለጠ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ከመካከላቸው ፡ ማንኛው ፡ ታላቅ ፡ እንደ፡ ሆነ ፡ ማወቅ ፡ አይቻልም።
ወ ፡ በለጠን ፡ የመሰለ ፡ በመልክም ፡ በአካልም ፡ የላቀ ፡ ማን ፡ ተገኝቶ ።

540 አገሩም ፡ ይፈታ ፡ ይደረብ ፡ ታቦቱ ፤
— ደግሞ ፡ እንደ ፡ ኪዳኑ ፡ ከቀረ ፡ ማጠንቱ ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ኪዳኑ ፡ ሁሉ ፡ ጸሎተ ፡ ዕጣኑ ፡ ከታጐለ ፡ ታቦቱ ፡ ይደረብ ።
ወ ፡ መምሬ ፡ ኪዳኑም ፡ መምሬ ፡ ማጠንቱም ፡ ከሞቱ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡
ይዘጋ ፡ ታቦቱ ፡ ይዳበል ።

541 አገራችን ፡ ቈላ ፡ መስክ ፡ የለ ፡ በደጅ ፤
— እንዲያው ፡ ዐፈር ፡ ላፈር ፡ እንጫወት ፡ እንጅ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ እያፈሩ ፡ ላይ ፡ ተቀምጠንም ፡ ቢሆን ፡ እንጫወት ፤ እሆነው ፡ ቦታ ፡
ዐረፍ ፡ ብለን ፡ እናውጋ ።
ወ ፡ ሻችና ፡ ሻች ፡ እስኪያልፉ ፡ እስኪሞቱ ፡ ይጫወታሉ ።

542 አገሬ ፡ ተቃጥሎ ፡ ደርሼ ፡ ድንገት ፡
— አንድ ፡ ቤት ፡ አጠፋሁ ፡ የምገባበት ።

ሠ ፡ አንድ ፡ ቤት ፡ ከቃጠሎ ፡ አዳንሁ ፤ ከሳት ፡ አተረፍሁ ።
ወ ፡ የምገባበት ፡ ቤት ፡ ጠፋ ፤ የምጠጋበት ፡ አጣሁ ።

543 አገሬን ፡ አገሬን ፡ የምትል ፡ ወፍ ፡ አለች ፤
— እኔን ፡ እኔን ፡ መስላ ፡ ታሳዝነኛለች ።

ሠ ፡ እንደኔ ፡ ካገሯ ፡ የወጣች ፡ ስደተኛ ፡ በመሆኗ ፡ ታሳዝነኛለች ።
ወ ፡ እንደኔው ፡ ፍጡር ፡ በመሆኗ ፡ ሞት ፡ ስለማይቀርላት ፡ ታሳዝነኛ
ለች ።

---

(1) ጐሹ ፡ ኀይሉ ፡ የሚባል ፡ አንድ ፡ ባላባት ፡ መቼም ፡ ለባሕርዩ ፡ ተስማሚ ፡ የምትሆን፡ ሴት ፡ ማግኘት ፡ አልችልም ፡ በማለት ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ሚስት ፡ ሳያገባ ፡ ከኖረ ፡ በኋላ ፡ ተመክሮ ፡ የሚያሳድጋት ፡ አንዲት ፡ ልጃገረድ ፡ ዐጨ ፤ እንደ፡ታሰበውም ፡ አግብቶ፡ በሰላም ፡ ሲኖር ፡ ሞት ፡ አይቀርምና ፡ በድንገት ፡ ተቀድሞ ፡ ሞተ ፤ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ እን ዳባት ፡ የምትቈጥረውን ፡ አሳዳጊ ፡ ባሏን ፡ በማጣቷ ፡ ሚስቲቱ ፡ የገጠመችው ።

544 አገሬን ፡ ዘረፈው ፡ እያለው ፡ ደስ ፡ ደስ ፤
— ሞኙ ፡ በጌምድሬ ፡ ፋንታው ፡ እስኪደርስ ።

ሠ ፡ የበጌምድር ፡ ሰው ፡ የርሱ ፡ ተራ ፡ ጊዜ ፡ እስኪደርስ ፡ አገሬን ፡ ደስ ፡ እያለው ፡ ዘረፈው ።
ወ ፡ ጀግናው ፡ ፋንታ ፡ ሲመጣ ፡ እሱም ፡ በተራው ፡ ይበዘበዛል ።

545 አገርሽ ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ ብጠይቃት ፡
— ከምከም ፡ ብላ ፡ ሣቀች ፡ ነገሩ ፡ ቢደንቃት ።

ሠ ፡ ከት ፡ ብላ ፡ ልቧ ፡ እስቲፈርስ ፡ ሣቀች ።
ወ ፡ አገሬ ፡ ከምከም ፡ ነው ፡ ብላ ፡ የከምከም ፡ ተወላጅ ፡ መሆኗን ፡ አስረዳችኝ ።

546 አገውን ፡ በቍርበት ፡ ጐዣምን ፡ በከብት ፡ (1)
—በመላ ፡ ፈታቸው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሳይሞት ።

ሠ ፡ በዘዴና ፡ በብልኀት ፡ ድል ፡ አደረጋቸው ።
ወ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሳይቀር ፡ ሁሉንም ፡ ፈታቸው ፤ ነጻ ፡ አወጣቸው ።

547 አጠረ ፡ ቁመቴ ፡ ወንድሞቼን ፡ ባይ ፤
—እያደገ ፡ ማነስ ፡ እንዲህ ፡ ኖሯል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ በዕድሜ ፡ ትልቅ ፡ ሆኖ ፡ ማጠር ፡ አለን ፤ ሰው ፡ እንዴት ፡ ከርሞ ፡ ጥጃ ፡ ይሆናል ።
ወ ፡ ተሹሞ ፡ መሻር ፡ አግኝቶ ፡ ማጣት ፡ አለ ፤ ከክብር ፡ በኋላም ፡ መዋረድ ፡ ለካ ፡ ኑሮሯልን ።

548 አጥር ፡ ቀደው ፡ ወጡ ፡ ነውረኛ ፡ መስለው ፤
—እረኛ ፡ ሳይሰጡት ፡ ለዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ለከብቱ ፡ እረኛ ፡ ሳይቀጥሩለት ፡ ተመልካች ፡ ሳያደርጉለት ፡ ሾልከው ፡ ሄዱ ።
ወ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሳይሾሙለት ፡ መሪ ፡ ሳያደርጉለት ፡ ድንገት ፡ ሞተው ፡ አስከሬናቸው ፡ በጓሮ ፡ በኩል ፡ ወጥቶ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ሄደ ።

549 አጥብቆ ፡ ጨነቀኝ ፡ ልቤ ፡ ተበትኖ ፤
—እንጀራዬ ፡ ሸዋ ፡ ቤቴ ፡ ጐንደር ፡ ሆኖ ።   (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ መኖሪያዬ ፡ ጐንደር ፡ ምግቤ ፡ ያለው ፡ ከሸዋ ፡ ሆኖ ፡ ተጨንቄያለሁ ፤ የማደርገው ፡ ጠፍቶኛል ።
ወ ፡ ትዳሬ ፡ ንብረቴ ፡ ያለው ፡ ጐንደር ፡ ነው ፤ ገንዘብ ፡ የማገኘው ፡ ቅርስ ፡ የማፈራው ፡ ግን ፡ ሸዋ ፡ ላይ ፡ ነው ፤ ኑሮዬ ፡ እዚያና ፡ እዚህ ፡ በመሆኑ ፡ ግራ ፡ ገባኝ ።

---

(1) ከጦር ፡ መላ ፡ ይረታል ፡ እንደሚባለው ፤ ደጃች ፡ ዘውዱ ፡ የአገውን ፡ ገዥ ፡ ደጃች ፡ ኤልያስን ፡ ሲወጉ ፡ የከብት ፡ ቆዳ ፡ በግልገል ፡ በቅሎ ፡ ዥራት ፡ እያሰሩ ፡ ሌሊት ፡ በጠላታቸው ፡ ሰፈር ፡ ሰደው ፡ የአገው ፡ ጦር ፡ ርስ ፡ በርሱ ፡ ተላልቆ ፡ በቀላሉ ፡ ድል ፡ በመሆኑ ፡ የተነገረ ።

550 አፈር ፡ መልሱ ፡ እንጂ ፡ ድንጋይ ፡ ለምናችሁ ።
—የቀለም ፡ ቀንድ ፡ ነው ፡ ትሰብሩታላችሁ ። (1)

ሠ ፡ የቀለም ፡ መበጥበጫውን ፡ ቀንድ ፡ እንዳትሰብሩት ፡ ተጠንቀቁ ።
ወ ፡ ድንጋዩን ፡ ዐፈሩን ፡ ዝግ ፡ ብላችሁ ፡ መልሱ ፤ የዕውቀት ፡ ምንጭ ፡
የነበረውን ፡ የሊቁን ፡ አስከሬን ፡ ትጐዱታላችሁ ።

551 አፈርሳለሁ ፡ ቤቴን ፡ መሥራት ፡ ይመስል ፤
—ቀን ፡ በጣለ ፡ ጊዜ ፡ የት ፡ ይደረሳል ።

ሠ ፡ ቤቴን ፡ አፈርሳለሁ ፤ አሁን ፡ ዝናም ፡ ቢጥል ፡ የት ፡ ልደርስ ፡ ነው ።
ወ ፡ ቀን ፡ ሲያጋልጥ ፡ ዘመን ፡ ሲያዋርድ ፡ ጊዜ ፡ ሲጥል ፡ የሚገቡበትን ፡
ያሳጣል ፤ የሚያደርጉት ፡ ይጠፋል ።

552 አፈር ፡ ተሸክሜ ፡ ከብዶኝ ፡ እያየኝ ፡
አትድከም ፡ ይለኛል ፡ ይኸ ፡ የሰው ፡ ሞኝ ።

ሠ ፡ ዐፈር ፡ ተሸክሜ ፡ ከብዶኝ ፡ እያየኝ ፡ እንደ ፡ ማገዝ ፡ በርታ ፡ ይለኛል።
ወ ፡ ዐፈር ፡ የሚሆን ፡ ሥጋን ፡ ለብሼ ፡ ስጨነቅ ፡ ስጠበብ ፡ እያየኝ ፡ ሞት ፡
የሚቀርልኝ ፡ ይመስል ፡ ያጽናናኛል ።

553 አፌ ፡ አልተናገረ ፡ በጆሮዬ ፡ አልሰማሁ ፤
—እንዲያው ፡ ታሰርኩና ፡ በወሬ ፡ ተፈታሁ ። (መዲ ፡ ቍ ፡ 103) ፡

ሠ ፡ አንድ ፡ ወር ፡ ታስሬ ፡ ተፈታሁ ፤ የወር ፡ እስራቴን ፡ ጨርሼ ፡ ወጣሁ ።
ወ ፡ በስብከትና ፡ በፖለቲካ ፡ ተሸበርኩ ፤ ተስፋ ፡ ቈረጥሁ ።

554 አፍንጫዬን ፡ ጠላ ፡ ለምን ፡ ሸተተው ፤
—እቤት ፡ መጠንሰሼን ፡ ማረጌን ፡ ስተው ።

ሠ ፡ መጥመቄን ፡ መጠንሰሴን ፡ ስተው ፡ ጠላ ፡ አማረኝ ፤ ውል ፡ ውል ፡
አለኝ ።
ወ ፡ ማዕርጌ ፡ ሲቀር ፡ ከሥልጣን ፡ ስሻር ፡ ጠላት ፡ ተነሣብኝ ፤ ባለጋራ ፡
በዛብኝ ።

555 ኢየሱስ ፡ ናዝራዊ ፡ ለካ ፡ በጐተና ፡ ተከፍክፎ ፡ ኖሮ ፡
—ይኸው ፡ ባንተ ፡ ጊዜ ፡ ተሠራ ፡ ዘንድሮ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ በጐተና ፡ በጐፈሬ ፡ ኖሮ ፡ ኖሮ ፡ ገና ፡ ዛሬ ፡ ጠጕሩን ፡ ሽሩባ ፡ ተሠራ ፤
ቈንዳላ ፡ ሆነ ።
ወ ፡ በሣር ፡ ክዳን ፡ ይኖር ፡ የነበረው ፡ የጐንደር ፡ ኢየሱስ ፡ ቤተ ፡ ክር
ስቲያን ፡ ባንተ ፡ ዘመን ፡ (ዐፄ ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ) ፡ ተሠራ ፤ ቈርቈሮ ፡
ለብሶ ፡ ያማረ ፡ ሆነ ።

---

(1) የማኅደረ ፡ ማርያም ፡ ተወላጅ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ ለትምህርት ፡ ንቁ ፡ ነበርና ፡ ከጐንደር ፡ ድጓውን ፡ ጾመ ፡ ድጓውን ፡ ምዕራፉን ፡ ዝማሜውን ፡ መረግዱን ፡ ጽፋቱን ፤ ከጐዣም ፡ ቅኔውን ፡ ወረቡን ፡ ለዘቡን ፤ ከዙራምባ ፡ ዝማሬ ፡ መዋሥእቱን ፡ ተምሮ ፡ ከ ጨረሰ ፡ በኋላ ፡ በማይታወቅበት ፡ አገር ፡ ሞቶ ፡ እንዳልባሌ ፡ ሰው ፡ ሲቀበር ፡ አይታ ፡ እኅቱ ፡ የገጠመችው ።

556 ኢጣሊያን ፡ ሥዩምን ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ጠላው ፤
—መረቡን ፡ አስጥሎ ፡ ዓሣ ፡ ባበላው ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 388) ፡ ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ መረብን ፡ አስጥሎ ፡ ዓሣ ፡ ባበላው ፡ ጣሊያን ፡ ለምንድነው ፡ ሥዩ ምን ፡ (ልዑል ፡ ራስ) ፡ የጠላው ።

ወ ፡ ጣሊያን ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ሥዩምን ፡ የጠላው ፡ በጦር ፡ ኀይል ፡ ወ ግቶ ፡ አስጨንቆ ፡ የመረብን ፡ ወንዝ ፡ ስላስለቀቀው ፡ ነው ።

557 እኽል ፡ በፊት ፡ ሲሸሽ ፡ በሬ ፡ ሲያባርር ፡
—ሁሉም ፡ ተከታትለው ፡ ጠፉ ፡ አሉ ፡ ካገር ። (1) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 558 ፡ 561 ፡ 563 ፡ 564) ፡

ሠ ፡ ተያይዘው ፡ አገር ፡ ጥለው ፡ ጠፉ ፤ ኰበለሉ ።

ወ ፡ እኽል ፡ ጠፋ ፤ ከብት ፡ ታጣ ፤ ረኃብ ፡ በዛ ፤ ቀውጢ ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ መጣ ፤ እልቂት ፡ ሆነ ።

558 እኽል ፡ ታሞል ፡ አሉ ፡ ሂደን ፡ እንየው ፤
—የማይተርፍ ፡ እንደሆን ፡ እኛ ፡ እንድንቀድመው ።

ሠ ፡ ቀድመነው ፡ እኛ ፡ እፊት ፡ እፊት ፡ እንሂድ ፤ ርሱ ፡ በኋላ ፡ ይምጣ ።

ወ ፡ እኽል ፡ ካገር ፡ ሊጠፋ ፡ ነው ፡ ተብሏልና ፡ የምንቀምሰው ፡ አጥተን ፡ በረኃብና ፡ በጭንቅ ፡ እንዳንባላ ፡ ቀድመን ፡ እንሙት ።

559 እኽል ፡ አላስበላ ፡ አላስጠፋ ፡ አትክልት ፤
—ወገን ፡ ጠባቂውን ፡ ለምን ፡ አሰሩት ።

ሠ ፡ እኽል ፡ ሳያስበላ ፡ አትክልት ፡ ሳያጠፋ ፡ እረኛውን ፡ በአፈ ፡ ላማ ፡ ለምን ፡ አሰሩት ።

ወ ፡ ጠባቂያችንን ፡ አሳቢያችንን ፡ ለምን ፡ ገነዙት ፡ ይሆን ፤ በሞት ፡ መቅደምስ ፡ መች ፡ ይገባው ፡ ነበር ።

560 እኽል ፡ አትበላም ፡ ወይ ፡ ልጄ ፡ ማታ ፡ ማታ ፤
—አንዠቴን ፡ በላችው ፡ ጐትታ ፡ ጐትታ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 382) ፡

ሠ ፡ ልጄ ፡ ጡቴን ፡ እየጠባች ፡ አንዠቴን ፡ ጐተተችው ፤ አስራበችኝ ።

ወ ፡ የልጄ ፡ ሞት ፡ አንገበገበኝ ፤ አንዠቴን ፡ በላው ፤ ሐዘኔ ፡ መሪር ፡ ሆነ ።

561 እኽል ፡ ኰበለለ ፡ ሂደ ፡ በነፋስ ፤
—ተከተለው ፡ በሬ ፡ እንዳይመለስ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 557 ፡ 558 ፡ 563 ፡ 564) ፡

ሠ ፡ እኽሉን ፡ ነፋስ ፡ ወሰደው ፤ እንዳይመለስም ፡ በሬ ፡ እየተከተለ ፡ በመግፋት ፡ አጋዘው ።

ወ ፡ እኽል ፡ ጠፋ ፤ ራብ ፡ ሆነ ፤ የከብት ፡ እልቂት ፡ ተከተለ ።

---

(1) ባ፲፰፻፹፩ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የከብት ፡ እልቂት ፡ ሆኖ ፡ ሕዝቡ ፡ ተጨንቆ ፡ ሳለ ፡ ወዲያው ፡ ተከታትሎ ፡ ባ፲፰፻፹፬ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የነፋስ ፡ በሽታ ፡ (ክፉ ፡ ቀን) ፡ መጥቶ ፡ ሰዉን ፡ ስለ ፡ ፈጀው ፡ በጊዜው ፡ የነበሩት ፡ ደራስያን ፡ በየበኩላቸው ፡ የኀሊናቸውን ፡ ስሜት ፡ የገለጹባቸው ።

562 እኽል ፡ የመሰለኝ ፡ በሩቁ ፡ ሳየው ።
—አሁን ፡ ቀረብ ፡ ብል ፡ ለካ ፡ ያ ፡ ሣር ፡ ነው ፡

ሠ ፡ ያ ፡ በሩቅ ፡ የማየው ፡ እኽል ፡ የመሰለኝ ፡ ለካ ፡ ሣር ፡ ኖሯል ።
ወ ፡ ለካ ፡ መከራ ፡ አሳር ፡ ኖሯል ፤ ተፈጥሮ ፡ ጭንቅ ፡ ነው ፤ ሰው ፡ መሆን ፡ ዕዳ ፡ ነው ።

563 እኽል ፡ ዱር ፡ አደረ ፡ ብቻውንም ፡ ዋለ ፤
—ጠላት ፡ እንደሌለው ፡ ሰው ፡ እንዳልገደለ ።     (ዘለ ፡ ቍ ፡ 557 ፡ 558 ፡ 561 ፡ 564) ፡

ሠ ፡ ሰው ፡ እንዳልገደለ ፡ በእጁ ፡ ነፍስ ፡ እንዳልጠፋበት ፡ አሳቡን ፡ ጥሎ ፡ ዋለ ፤ እዱርም ፡ ብቻውን ፡ አደረ ።
ወ ፡ በእኽል ፡ ችግር ፡ በምግብ ፡ ጥፋት ፡ ሰው ፡ ያልሞተ ፡ ይመስል ፡ አሁን ፡ አገር ፡ ምድሩ ፡ እኽል ፡ ብቻ ፡ ሆነ ፤ በቈላ ፡ በደጋው ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ ተገኘ ።

564 እኽል ፡ ዘምቶ ፡ ገባ ፡ እኛም ፡ አየነው ፤
—አያሌ ፡ ሰው ፡ ቀረ ፡ ሳይገናኘው ።     (ዘለ ፡ ቍ ፡ 557 ፡ 558 ፡ 561፡ 563) ፡

ሠ ፡ ሰው ፡ ሳይገናኘው ፡ ሳያየው ፡ ቀረ ፤ ከዘመቻው ፡ አያሌ ፡ ሰው ፡ እንኳን ፡ ደኅና ፡ ገባህ ፡ ሳይለው ፡ ቀረ ።
ወ ፡ በምግብ ፡ እጦት ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ እኽል ፡ እንዳማረው ፡ ሳያገኝ ፡ ሳይበላ ፡ ሞተ ።

565 እኅቴን ፡ ለማየት ፡ ሄጄ ፡ ተጠርቼ ፤
—ቶሎ ፡ ብዬ ፡ መጣሁ ፡ መርገፏን ፡ አይቼ ።

ሠ ፡ መርገፍ፡ያለው፡ጌጧን፡አይቼ ፡ አሸን ፡ ክታቧን ፡ ተመልክቼ፡መጣሁ።
ወ ፡ የእኅቴን ፡ ሞት ፡ ተረድቼ ፡ መቃብሯን ፡ አይቼ ፡ እርሜን ፡ አውጥቼ ፡ ተመለስሁ ።

566 እኅቶችህ ፡ የሉ ፡ ወይ ፡ እናትህ ፡ የሉ ።
—ማን ፡ ሠራልህና ፡ ዐዘ ፡ በላህ ፡ አሉ ።     ( ዘለ ፡ ቍ ፡ 493 ፡ 1090) ፡

ሠ ፡ ያዘ ፡ ወጥ ፡ ማን ፡ ሠራልህና ፡ በላህ ፡ እኅቶችህ ፡ እናትህ ፡ የሉ ።
ወ ፡ ዐዘ ፡ ወስዶ ፡ በላህ ፡ ወይ ።

567 እሑድም ፡ ቅዳሜም ፡ ግብር ፡ ሲያበላን ፡
መንገድ ፡ ሲያስኬደን ፡
—ሰንበት ፡ የማይል ፡ ሰው ፡ ምን ፡ አጋጠመን ።

ሠ ፡ በዓል ፡ የማያውቅ ፡ እሑድን ፡ የማያከብር ፡ ሰንበት ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የማይረዳ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ አጋጠመን ፤ እንዴት ፡ ያለውን ፡ ፍጡር፡ አመጣብን ።
ወ ፡ ዕድሜ ፡ የሌለው ፡ የማይሰነብት ፡ ሰው ፡ በምን ፡ ፈጣሪያችን ፡ አስተዋወቀን ፤ አላመደን ።

568 እመቤቴ ፡ ወልዳ ፡ የጌታዬ ፡ እናት ፡
—ምን ፡ ይገባ ፡ ላይ ፡ ልሂድ ፡ የተጠራሁ ፡ ለት ።

ሠ ፡ እመቤቴ ፡ ወልዳለች ፡ አሉ ፤ ያራስ ፡ ጥሪ ፡ ምን ፡ ይገባላት ፡ ለማየት ፡ ለመጐብኘት ፡ ልሂድ ፤ ምን ፡ ልውሰድላት ።

ወ ፡ በሞት ፡ ጊዜ ፡ የትኛውን ፡ በጎ ፡ ምግባሬን ፡ ነው ፡ ከአምላኬ ፡ ፊት ፡ ይገባ ፡ የምቀርበው ።

569 እመንታ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ አንድ ፡ ቤት ፡ ነበረኝ ፤
—አላፊው ፡ አግዳሚው ፡ ያፈርሰው ፡ መሰለኝ ።

ሠ ፡ ቤቴን ፡ በመንገዱ ፡ የሚሄደው ፡ ሁሉ ፡ የሚያፈርስብኝ ፡ መሰለኝ ፤ ይዞታው ፡ አስፈራኝ ።

ወ ፡ የሰውን ፡ ፈራሽነትና ፡ በስባሽነት ፡ ተገነዘብሁት ፤ ከንቱነቱም ፡ ይሰማኝ ፡ ዠመር ።

570 እማራለሁ ፡ ብሎ ፡ ዝምሮ ፡ ፊደል ፡
—ከዋ ፡ አድርሶት ፡ ሄደ ፡ ይህ ፡ የልጅ ፡ ችኩል ።

ሠ ፡ ፊደል ፡ ዠምሮ ፡ «ዋ» ፡ ከሚለው ፡ ዘር ፡ ሲደርስ ፡ ጥሎት ፡ ሄደ ፤ ሳይዘልቀው ፡ ቀረ ፤ በዥምር ፡ ተወው ።

ወ ፡ ተፈጥሮው ፡ አሳዛኝ ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ፤ ዕድሜው ፡ አጥሮ ፡ ለዋይታ ፡ ለለቅሶ ፡ ሆነ ።

571 እንቢልታ ፡ መለከት ፡ የሚነፋው ፡ የት ፡ ነው ፤
—አንድም ፡ በስርቆሽ ፡ በር ፡ አንድም ፡ በግቢ ፡ ነው ። (ማ፡ ወ፡ እ)፡

ሠ ፡ እንቢልታ ፡ መለከት ፡ የሚሰማው ፡ በጓሮ ፡ በኩል ፡ ወይም ፡ በግቢ ፡ ውስጥ ፡ ነው ፤ ከሁለቱ ፡ ቦታ ፡ ባንዳቸው ፡ ላይ ፡ ነው ።

ወ ፡ እንቢልታ ፡ የሚያስነፉ ፡ ነጋሪት ፡ የሚያስመቱ ፡ በጋብቻ ፡ ሥልጣን ፡ ያገኙ ፡ ወይም ፡ ያላግባብ ፡ በተገኘ ፡ ገንዘብ ፡ ወገን ፡ ጥግ ፡ ያበጁ ፡ ናቸው ።

572 —እንቢ ፡ አልሰማም ፡ ብሎ ፡ ጥላ ፡ ሁን ፡ ቢሉት ፡
—ጠውልጎ ፡ ደረቀ ፡ ወደቀ ፡ መሬት ።

ሠ ፡ ከጥላ ፡ ሥር ፡ ተቀመጥ ፡ ከዛፍ ፡ ሥር ፡ ሁን ፡ ቢሉት ፡ እንቢ ፡ ብሎ ፡ የፀሐዩ ፡ ሐሩር ፡ ጐዳው ፤ አደከመው ።

ወ ፡ ጥላ ፡ ወገን ፡ ይሆናል ፡ ብለን ፡ ስንጠብቀው ፡ እመቃብር ፡ ገባ ፤ ዐፈር ፡ ሆነ ።

573 እራሴን ፡ (ራሴን) ፡ አንገቴ ፡ አልችለው ፡ ብለህ ፤
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ትጥለኛለህ ።

ሠ ፡ ምንስ ፡ ራሴ ፡ ትልቅ ፡ ቢሆን ፡ ቢከብድ ፡ አንገቴ ፡ አልችል ፡ ብለህ ፡ ባደባባይ ፡ ትጥለኛለህ ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ምነው ፡ በየሰዉ ፡ ፊት ፡ ቆሜ ፡ እንድለምን ፡ አደረግሽኝ ፤ አጥቼ ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ አሳየሽኝ ።

574 እራቤን ፡ (ራቤን) ፡ ጕዳቴን ፡ ዠሮዋ ፡ እየሰማ ፡
—ባሳዝነው ፡ ብላ ፡ ሰጠችኝ ፡ አክርማ ።

ሠ ፡ መራቤን ፡ መጠማቴን ፡ እያወቀች ፡ ይዘን ፡ ብላ ፡ ምግቡን ፡ አቈይታ ፡ ሰጠችኝ ።

ወ ፡ ርቦኝ ፡ በአክርማ ፡ በተሰፋ ፡ ባዶ ፡ መሶብ ፡ አቀረበችልኝ ፤ ለምን ፡ ብላ ፡ ነው ፡ እንዲህ ፡ ያሳዘነችኝ ።

575 እራቴን ፡ አይሰጠኝ ፡ ይህ ፡ አዛዡ ፡ ምን ፡ ይላል ፤
—ሰው ፡ ሁሉ ፡ በወቅቱ ፡ በጊዜው ፡ ይበላል ።

ሠ ፡ ሰው ፡ በተወሰነው ፡ ሰዓት ፡ ይመገባል ፤ ያለሰዓቱ ፡ አይበላም ።

ወ ፡ ሰው ፡ ጊዜ ፡ ሲያጋጥመው ፡ ዘመን ፡ ሲያመቸው ፡ ሀብት ፡ ያገኛል ፤ ቅርስ ፡ ያበጃል ።

576 እርሱ ፡ ምን ፡ ቸገረው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ቢጕላላ ፤
—መርጦ ፡ ከተማውን ፡ ከያዘ ፡ በኋላ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 128 ፡ 427) ፡

ሠ ፡ የመረጠውን ፡ የፈቀደውን ፡ ከተማ ፡ ካገኘ ፡ ወዲያ ፡ እሱ ፡ ሰው ፡ ቢጕላላ ፡ ወታደር ፡ ቢንገላታ ፡ ቁብ ፡ የለውም ፤ አያስብም ።

ወ ፡ የመርጦን ፡ ከተማ ፡ ከያዘ ፡ ሌላ ፡ ምን ፡ ይፈልጋል ፤ ይኸው ፡ አይበቃውምን ።

577 እርሳስ ፡ (ርሳስ) ፡ ለመጻፊያ ፡ ለማግኘት ፡ ስንጥር ፡
—ለካስ ፡ ከፊታችን ፡ ኖሯል ፡ መቃ ፡ ብር ።

ሠ ፡ የሸንበቆ ፡ ብር ፡ መኖሩን ፡ ገና ፡ አሁን ፡ አየነው ፤ መጻፊያውን ፡ አልተመለከትነውም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ለካ ፡ መሞት ፡ መቃብር ፡ ኖሯልን ፤ አሁን ፡ ገና ፡ ገባን ።

578 እርስቴን ፡ (ርስቴን) ፡ ሲያርስብኝ ፡ አያለሁ ፡ ዝም ፡ ብዬ ፤
—ዘር ፡ ሳይዙ ፡ መሬት ፡ ምን ፡ ያደርጋል ፡ ብዬ ።

ሠ ፡ የእኽል ፡ ዘር ፡ ሳይኖር ፡ ለመሬት ፡ መጓጓት ፡ ምን ፡ ያደርጋል ፤ ያለ ዘር ፡ መሬት ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

ወ ፡ ወራሽ ፡ የሚሆን ፡ ልጅ ፡ ከሌለ ፡ ርስት ፡ መሰብሰብ ፡ ሀብት ፡ ማከማቸት ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

579 እርግብና ፡ (ርግብና) ፡ ዋኔ ፡ አብረው ፡ ዘመቱና ፡
—እርግብ ፡ (ርግብ) ፡ ደኅና ፡ ገባች ፡ ዋኔን ፡ ገደሉና ።

ሠ ፡ ቡያዋ ፡ ሞተችና ፡ ርግብ ፡ ብቻዋን ፡ በደኅና ፡ ተመለሰች ፤ በሰላም ፡ ገባች ።

ወ ፡ ወየው ፡ እኔ ፡ ተበደልኩ ፤ ጥቃት ፡ በዛብኝ ፤ የዛሬ ፡ ሰዎች ፡ መተዛዘንን ፡ አንተ ፡ ትብስ ፡ አንተ ፡ ትብስ ፡ መባባልን ፡ ፈጽሞ ፡ ተዉት ፤ ሐዘን ፡ ትካዜ ፡ ጠፋ ።

580 እርጥብ ፡ የነበሩ ፡ ከውሃ ፡ ሲወጡ ፡
—አሁን ፡ እደጃችን ፡ መጠጥ ፡ ብለው ፡ መጡ ።

ሠ ፡ ሰውነታቸውን ፡ በፀሓይ ፡ አሞቁ ፤ ከርጥበቱ ፡ ደረቁ ።
ወ ፡ መጠጥ ፡ ጠላና ፡ ጠጅ ፡ ዐረቄ ፡ ፍለጋ ፡ መጡ ።

581 እሱ ፡ ባጭር ፡ በቅሎ ፡ ማልዶ ፡ ገሠገሠ ፤
—እኔ ፡ ኮርቻ ፡ አጣሁ ፡ ቀኛዝማች ፡ ታደሰ ።

ሠ ፡ ኮርቻ ፡ ቸገረኝ ፤ የፈረስ ፡ የበቅሎ ፡ ዕቃ ፡ አጣሁ ።
ወ ፡ ተመክቼበት ፡ የነበረው ፡ ልጄ ፡ ገና ፡ ባጭር ፡ ተቀጨ ፤ እሱም ፡ ሞተ ፤ እኔም ፡ ተሳቅቄ ፡ ቀረሁ ።

582 እሳት ፡ ፈጀው ፡ አሉ ፡ ጌታው ፡ ቤትዎን ፡
—ከገበያ ፡ በላይ ፡ የነበረውን ።

ሠ ፡ ቤትዎ ፡ ተቃጠለ ፤ ከገበያው ፡ በላይ ፡ የነበረው ፡ መኖሪያዎ ፡ በእሳት ፡ ነደደ ።
ወ ፡ ከገበያ ፡ ይበልጥ ፡ የሕዝብ ፡ መሰብሰቢያ ፡ የሀብት ፡ መገኛ ፡ የነበረው ፡ ቤትዎ ፡ በመሞትዎ ፡ ፈረሰ ፤ ቀረ ።

583 እስላም ፡ ነው ፡ እስላም ፡ ነው ፡ እስላም ፡ ነው ፡ እያሉ ፡
—ያማራ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ ሰውነቱ ፡ ሁሉ ።

ሠ ፡ ለምንድነው ፡ ሰውየውን ፡ እስላም ፡ ነው ፡ የሚሉት ፤ አኳኋኑ ፡ ሥነ ፡ ምግባሩ ፡ ሁሉ ፡ የአማራ ፡ ይመስል ፡ የለምን ።
ወ ፡ ሰዎቹ ፡ እንደሚሉት ፡ ጐስቋላ ፡ አይደለም ፤ ጽዳት ፡ ያለው ፡ ሰውነቱ ፡ ያማረ ፡ ነው ።

584 እስቴ ፡ ላይ ፡ ተቀምጠህ ፡ ሳይኖርብህ ፡ ችግር ፡
—እንዴት ፡ አንተ ፡ እያለህ ፡ ልጅህ ፡ ቆማ ፡ ትቅር ።

ሠ ፡ እስቴን ፡ ስትገዛ ፡ ችግር ፡ ሳይኖርብህ ፡ እንዴት ፡ አንተን ፡ ያኸል ፡ አባት ፡ እያላት ፡ ልጅህ ፡ ሳትዳር ፡ ትቅር ።
ወ ፡ ልጅህ ፡ «ቆማ» ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ አንተ ፡ እያለህ ፡ እንዴት ፡ ሄዳ ፡ ትቅር ።

585 እስቲ ፡ አትቸኩሉ ፡ ሂዱ ፡ ቀስ ፡ ብላችሁ ፤
—ይኸን ፡ የሰው ፡ ሸክላ ፡ ትሰብሩታላችሁ ።

ሠ ፡ የተውሰውን ፡ እንስራ ፡ እንዳይሰበር ፡ ተጠንቅቃችሁ ፡ አድርሱት ።
ወ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ሸክላ ፡ ተሰባሪ ፡ ነውና ፡ ቀስ ፡ ብላችሁ ፡ በማስተዋል ፡ ጠብቁት ።

586 እስቲ ፡ ጠይቁልኝ ፡ ቤቷን ፡ ጥላ ፡ አደረች ፤
—ሰዎች ፡ አይተዋታል ፡ ገበያ ፡ ነበረች ። (1)

ሠ ፡ እገበያ ፡ ውላለች ፤ ከሸቀጥ ፡ ተራ ፡ ታይታለች ፤ እዚያ ፡ ነበረች ።
ወ ፡ ሻችቷ ፡ ቸር ፡ ሰው ፡ ሰብሳቢ ፡ እንግዳ ፡ ተቀባይ ፡ ነበረች ።

587 እስቲ ፡ ጠይቁልኝ ፡ ርቃ ፡ ሳትሄድ ፤
—እቴጌ ፡ ተዋበች ፡ እት ፡ እናት ፡ ገረድ ። (ዐፄ ፡ ቴ) ፡

ሠ ፡ እት ፡ እናት ፡ ገረድ ፡ መሆኗን ፡ ርቃ ፡ ሳትሄድ ፡ አረጋግጣችሁ ፡ ጠይቁልኝ ።

ወ ፡ እትም ፡ እናትም ፡ ገረድም ፡ ነበረች ፤ በአዛኝነቷ ፡ እንደ ፡ እናት ፡ በአገልግሎቷ ፡ እንደ ፡ ገረድ ።

588 እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ስዞር ፡ እኖራለሁ ፤
—ማዘኔን ፡ ቈርጬ ፡ ቤቴን ፡ እሠራለሁ ።

ሠ ፡ ከእንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ስዞር ፡ አልኖርም ፤ ማእዘኔን ፡ አዘጋጅቼ ፡ ቤቴን ፡ እሠራለሁ ።

ወ ፡ በሐዘንና ፡ በጸሎት ፡ ለመኖር ፡ ቈርጬ ፡ ለነፍሴ ፡ የሚበጃትን ፡ እሠራለሁ ።

589 እስከዚያው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሢሦ ፡ ማረሳችን ፤
—ኋላማ ፡ እንገባለን ፡ በየመሬታችን ።

ሠ ፡ ለጊዜው ፡ ተጋኸም ፡ ጢሰኛም ፡ ብንሆን ፡ በኋላ ፡ ወደየርስታችን ፡ እንሄዳለን ፤ በየመሬታችን ፡ እንመለሳለን ፤ እንዲሁ ፡ አንቀርም ።
ወ ፡ ሰው ፡ ኖሮ ፡ ኖሮ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ መግባቱ ፡ አይቀርም ፤ የዘላለም ፡ ርስቱ ፡ እሱ ፡ ነውና ።

590 እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ መቼ ፡ ተረዳሁት ፤
—ባላልጋ ፡ መሆኑን ፡ አሁን ፡ ነው ፡ ያወቅሁት ።

ሠ ፡ ባለአልጋ ፡ ባለመንግሥት ፡ መሆኑን ፡ ነጋሢነቱን ፡ ገና ፡ አሁን ፡ ዐወቅሁት ።

ወ ፡ ባል ፡ እንደ ፡ አልጋ ፡ ምቹ ፡ መሆኑን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አልተረዳሁትም ፡ ነበር ።

591 እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ምንም ፡ ሳያወሣ ፤
—በጣም ፡ ያስደንቃል ፡ ሞት ፡ በላ ፡ አሉ ፡ ካሳ ።

ሠ ፡ አፈ ፡ ላማ ፡ ተቀብሎ ፡ ተክሶ ፡ የማያውቀው ፡ ሞት ፡ ዛሬ ፡ ካሳ ፡ በላ ፡ አሉ ።

ወ ፡ ሞት ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ካሳን ፡ ወሰደ ።

(1) መልከ ፡ ጥፉ ፡ በሞያዋ ፡ ግን ፡ የሴት ፡ ቍንጮ ፡ የሆነች ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ነበረች ፤ ባሏን ፡ ባስተዳደር ፡ እጅግ ፡ ደስ ፡ ታሰኘው ፡ ነበርና ፡ የማይቀረው ፡ ሞት ፡ ስለ ፡ ለያቸው ፡ ባልየው ፡ መልካም ፡ ሥራዋንና ፡ ሞያዋን ፡ በማስታወስ ፡ በብዙ ፡ ጸጸት ፡ ሐዘኑን ፡ የገለጠበት ።

592 እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሲያገለግልዎ ፤
—ምን ፡ ተበደለና ፡ ዓለሙ ፡ ከዳዎ ።

1 ሠ ፡ አገልጋይዎ ፡ ዓለሙ ፡ ምን ፡ ቢያደርጉት ፡ ነው ፡ የከዳዎት ፤ ምን ፡ በድለውት ፡ ነው ፡ ጥሎዎት ፡ የሄደው ።

ወ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ የነበረው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የት ፡ ጠፋ ፤ ያ ፡ ሁሉ ፡ ዓለም ፡ ወዴት ፡ ደረሰ ።

2 ወ ፡ ዓለሙ ፡ ልጅዎ ፡ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ ሳይደርስ ፡ ምነው ፡ ሞት ፡ ፈጥኖ ፡ ወሰደው ።

593 እስኪ ፡ ልነሣና ፡ ሙሾ ፡ ላውጣለት ፤
—ለዚያ ፡ ለወንድሜ ፡ ለቀረው ፡ አለት ።

ሠ ፡ ያለእኅት ፡ ለቀረው ፡ ዘመድ ፡ ላጣው ፡ ወንድሜ ፡ ሙሾ ፡ ላውጣለት ፤ የልቅሶ ፡ ዜማ ፡ ልድረስለት ።

ወ ፡ ከጭንጫ ፡ ወድቆ ፡ አለት ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ተዘርሮ ፡ ለቀረው ፡ ወንድሜ ፡ ላልቅስለት ፤ እንባ ፡ ላፍስስለት ።

594 እስኪ ፡ ልጅ ፡ ፈልጉ ፡ ጠርቶ ፡ ይቀስቅሰው ፤
—እንደ ፡ ተኛ ፡ ቀረ ፡ ተረሳ ፡ ይኸ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ይህ ፡ ሰው ፡ እንደ ፡ ዘበት ፡ ጋደም ፡ አለና ፡ አሸልቦት ፡ ቀረ ፤ እንቅልፍ ፡ በዚያው ፡ ወሰደው ፤ እስኪ ፡ ልጅ ፡ ጥሩና ፡ ይቀስቅሰው ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ድንገተኛ ፡ ሞት ፡ ሞተ ፤ እንግዲህ ፡ መስፍኑ ፡ መ ረሳቱ ፡ መዘንጋቱ ፡ ነውን ።

595 እስኪ ፡ በሉ ፡ ስጡት ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፡ ፈተና ፤
—ቀን ፡ እኮ ፡ አጥፍቶታል ፡ ምኑን ፡ ተማረና ።　(ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ «ቀ» ፡ የሚባለውን ፡ የፊደል ፡ ዘር ፡ ረስቶታል ፤ ዘንግቶ ታል ፤ ጨርሶ ፡ አጥፍቶታል ።

ወ ፡ ያን ፡ የተማረ ፡ ሰው ፡ ቀን ፡ ጥሎታል ፤ ጊዜ ፡ አዋርዶታል ፤ ዘመኑ ፡ አልሆነውም ።

596 እስኪ ፡ ተመልከቱት ፡ የአምላክን ፡ ጸጋ ፤
—የሰው ፡ ሸክላ ፡ ሠሪ ፡ ሳይቀበል ፡ ዋጋ ።

ሠ ፡ ዋጋ ፡ ሳይጠይቅ ፡ ሳይቀበል ፡ ለሰው ፡ ሁሉ ፡ ሸክላ ፡ ሠራተኛ ፡ ነበር ።

ወ ፡ አምላክ ፡ ከሸክላ ፡ ከዐፈር ፡ ሰውን ፡ ይሠራል ፤ ሰውን ፡ እንደ ፡ ሸክላ ፡ ከዐፈር ፡ ይፈጥረዋል ።

597 እስኪ ፡ የኋላህን ፡ ዘወር ፡ ብለህ ፡ እየው ፤
—ጃንሆይ ፡ ይሉት ፡ ነበር ፡ አባትክን ፡ ቃኘው ።

ሠ ፡ ጃንሆይ ፡ ሕዝቡን ፡ ዘወር ፡ ብለህ ፡ ጐብኘው ፡ ይሉት ፡ እንደ ፡ ነበር ፡ አንተም ፡ ተመልከተው ፤ ያለፈውን ፡ ያባትክን ፡ ሥራ ፡ እየው ፤ አስ ታውሰው ።

ወ ፡ የራስ ፡ መኰንንን ፡ ፈረስ ፡ ቃኘው ፡ ብለው ፡ ይጠሩት ፡ ነበር ።

598 እሻሻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የእስራኤል ፡ ሞት ፤
—እንዲያ ፡ አልቅሰው ፡ ተድላን ፡ ለምን ፡ ቀበሩት ።

ሠ ፡ ተስፋ ፡ ትንሣኤ ፡ የሌለው ፡ ይመስል ፡ በመሪር ፡ ልቅሶና ፡ ሐዘን ፡ ለምን ፡ ቀበሩት ።

ወ ፡ ሰው ፡ እንዲያልቅ ፡ ሕዝብ ፡ እንዲበደል ፡ አገር ፡ እንዲጠፋ ፤ ተድላን፡ ለምን ፡ ቀበሩት ።

599 እቀድማለሁ ፡ ብሎ ፡ ሽማግሌውን ፤
—ዐፈር ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡ ወይ ፡ ሕፃን ፡ መሆን ።

ሠ ፡ ሽማግሌውን ፡ ለመቅደም ፡ ሲሮጥ ፡ ካፈር ፡ ላይ ፡ ወደቀ ፡ ባፍ ፡ ጢሙ፡ ተደፋ ።

ወ ፡ ሕፃኑ ፡ ካባቱ ፡ በፊት ፡ ሞቶ ፡ ተቀበረ ።

600 እቅርብ ፡ እንኳን ፡ አይደል ፡ ከዚያ ፡ ላይ ፡ ነው ፡ ቤቱ ፤
—ዐይኔን ፡ ሆዴ ፡ አጠፋው ፡ አለጎረ ፡ ቤቱ ። (1)

ሠ ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ሳይሆን ፡ ሳይቀራረብ ፡ ሆዴ ፡ ዐይኔን ፡ ደነቈለው ፤ ጓጕ ጠው ፡ የበላ ፡ ሆዴ ፡ እየባባ ፡ አስለቅሶ ፡ ዐይኔን ፡ አጠፋው ።

ወ ፡ ሆዴ ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ የዐይኔን ፡ ነዋሪዎች ፡ ፈጃቸው ፤ ገደላ ቸው ፤ አጠፋቸው ።

601 እባብ ፡ ሆነ ፡ ውቤ ፡ ሰውነቱን ፡ ትቶ ፤
—አላባቱ ፡ ሊነክስ ፡ ካቡን ፡ ተጠግቶ ። (2)

ሠ ፡ እባብ ፡ ካቡን ፡ ከለላ ፡ አድርጎ ፡ ግንቡን ፡ ተጠግቶ ፡ ሊናከስ ፡ መጣ ።

ወ ፡ አቡን ፡ አስመጥቶ ፡ ጳጳስ ፡ ይዞ ፡ ለመንገሥ ፡ ሞከረ ፤ ንጉሥ ፡ ለመ ሆን ፡ አሰበ ።

602 እባክህ ፡ ወንድሜ ፡ ልጠይቅህ ፡ ወሬ ፤
—ተቃጥሏል ፡ መሰለኝ ፡ ሸተተኝ ፡ አገሬ ።

ሠ ፡ ያገሬ ፡ ጠረን ፡ ተሰማኝ ፤ የቃጠሎው ፡ ሽታ ፡ ባፍንጫዬ ፡ ገባ ፤ ሸተ ተኝ ።

ወ ፡ አገሬ ፡ ናፈቀኝ ፤ የቤቱ ፡ የወንዙ ፡ ያበባው ፡ ሥዕል ፡ በፊቴ ፡ መጣ ፤ ትዝታው ፡ ለዐይኖቼ ፡ እንባን ፡ አተረፈ ።

603 እቤቴም ፡ አልገባ ፡ ለጥምቀት ፡ ለገና ፤
—ቡሖ ፡ ዕቃዬን ፡ ሁሉ ፡ ባዶ ፡ አረግሽውና ።

---

(1) በጐዣም ፡ ዐይኔ ፡ ሆዴ ፡ የሚባሉ ፡ ቀበሌዎች ፡ ይገኛሉ ። አንድ ፡ ጊዜ ፡ በእንዚህ ፡ ቦታዎች ፡ የሚኖሩት ፡ ሰዎች ፡ ተጣሉና ፡ የዐይኔን ፡ ኗሪዎች ፡ የሆዴ ፡ አገር ፡ ሰዎች ፡ አጠፏቸው ፤ ስለዚህ ፡ የዐይኔ ፡ ቀበሌ ፡ ሰው ፡ የገጠመው ።

(2) ትልቁ ፡ ደጃች ፡ ውቤ ፡ ለመንገሥ ፡ ቊርጥ ፡ አሳብ ፡ አድርገው ፡ የሚቀባቸው ፡ አቡን ፡ ጳጳስ ፡ በማስመጣታቸው ፡ የተገረመ ፡ ሰው ፡ የተናገረው ።

ሠ ፡ ቤቱን ፡ የሚላስ ፡ የሚቀመስ ፡ አሳጣሽው ፤ ምንም ፡ የሌለበት ፡ አደረ ግሽው ፤ መግቢያ ፡ አሳጣሽኝ ፡፡

ወ ፡ ወተቱን ፡ ንጠሽ ፡ ቅቤውን ፡ አውጥተሽ ፡ ምነው ፡ አሬራውን ፡ ብቻ ፡ ተውሽልኝ ፡፡

604 እታጠቀው ፡ ብዬ ፡ ጐራዴ ፡ ብገዛ ፡
—እሱም ፡ ወዘወዘኝ ፡ አሽሻጣጩ ፡ በዛ ፡፡

ሠ ፡ ልታጠቀው ፡ የገዛሁት ፡ ጐራዴ ፡ እጅግ ፡ ረዘመ ፤ አሽሻጣጩ፡ ስለ፡ በዛ ፡ ይነቀንቀኝ ፡ ይወዘውዘኝ ፡ ዠመር ፤ ከዐቅሜ ፡ በላይ ፡ ሆነ ፡፡

ወ ፡ እሱም ፡ አጠቃኝ ፤ አንገላታኝ ፤ አሽሻጣጩም ፡ በዛ ፤ ትንሽ ፡ ት ልቁ ፡ አንጓጠጠኝ ፤ ያፌዝብኝ ፡ ዠመር ፡፡

605 እትህ ፡ የናትህ ፡ ልጅ ፡ እንከን ፡ የሌለብኝ ፡
—አንተ ፡ ዐፈር ፡ ስትበላ ፡ ምናኔ ፡ ቀረብኝ ፡፡

ሠ ፡ አንተ ፡ ርስት ፡ ስታገኝ ፡ በናትም ፡ ባባትም ፡ አንድ ፡ የሆንኩት ፡ እኅትህ ፡ ለምን ፡ አጣሁ ፤ ሳይደርሰኝ ፡ ቀረ ፡፡

ወ ፡ አንተ ፡ ዐፈር ፡ ስትሆን ፡ እኔ ፡ መመነን ፡ ተሳነኝ ፤ ካንተ ፡ በኋላ ፡ በዓ ለም ፡ መቈየት ፡ ይገባኝ ፡ ኖሯልን ፡፡

606 እነችብሎችን ፡ እነሱን ፡ አያርገኝ ፤
—ጥለውት ፡ ገቡ ፡ አሉ ፡ አንድ ፡ እንግዳ ፡ ቢገኝ ፡፡

ሠ ፡ አንድ ፡ እንግዳ ፡ ቢመጣ ፡ ለማብላት ፡ ነፍገው ፡ ትተውት ፡ ወደ፡ ቤት፡ ገቡ ፤ ምንኛ ፡ የሚያሳዝኑ ፡ ናቸው ፡፡

ወ ፡ እንግዳ ፡ የሚባለውን ፡ ሰው ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ጥለውት ፡ መመለሳቸው ፡ እጅግ ፡ የሚያስተዛዝብ ፡ ነው ፡፡

607 እነዚህን ፡ በጎች ፡ ምን ፡ በታተናቸው ፤
—ተኵላው፡እጅግ፡ ከፍቷል ፡ ና ፡ ኀይሌ፡ አንዳርጋቸው ፡፡ (አ ፡ እ)፡

ሠ ፡ በጎቹን ፡ ሰብስበህ ፡ በጊዜ ፡ አስገባ ፤ ተኵላው ፡ ከፍቷል ፡፡

ወ ፡ ጀግናው ፡ ኀይሌ ፡ አንዳርጋቸው ፤ ጠላት ፡ መጥቷልና ፤ በተለመደው ፡ ጀግንነትህ ፡ ጠላትን ፡ ተምቾ ፡ ምታው ፡፡

608 እነግርህ ፡ ነበረ ፡ ይህንን ፡ በፊት ፤
—አንተ ፡ ስትታሰር ፡ የኛን ፡ መፈታት ፡፡

ሠ ፡ አንተ ፡ ስትታሰር ፡ እኛ ፡ ከእስራት ፡ እንለቀቃለን ፡ ከወህኒ ፡ ቤት ፡ እንወጣለን ፡ ብለንህ ፡ ነበርን ፡፡

ወ ፡ አንተ ፡ በሞት ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ስትለይ ፡ እኛ ፡ እንበተናለን ፡ ጥግ ፡ ደጋፊ ፡ ሰብሳቢ ፡ እናጣለን ፡ ብለን ፡ ስንነግርህ ፡ ነበር ፤ ይኸው ፡ ደረሰ ፡፡

609 እነግርብሻለሁ ፡ ሥሥትሽን ፡ ለሁሉ ፤
—እንዴት ፡ አላመጥሽው ፡ ውሃ ፡ በላሽ ፡ አሉ ፡፡

ሠ ፡ እንዴት ፡ አድርገሽ ፡ ውሃውን ፡ እንደ ፡ እንጀራ ፡ በጥርስሽ ፡ ትበያ
ለሽ ፤ ታላምጫለሽ ።
ወ ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ ወሰደሽ ፤ ማዕበል ፡ አሰመጠሽ ።

610 እኒህን ፡ መጻሕፍት ፡ ማን ፡ ይሸከማቸው ፤
—ጎይሌ ፡ ተቀንሷል ፤ እኔም ፡ አልችላቸው ።

ሠ ፡ መጽሐፎቹን ፡ ለመሸከም ፡ አልቻልኩም ፤ ጕልበቴ ፡ ደክሟል ፤ ዐ
ቅሜ ፡ ተቀንሷል ።
ወ ፡ ድጋፍ ፡ ምርኵዝ ፡ ይሆነኛል ፡ ያልኩት ፡ «ጎይሌ» ፡ በሞት ፡ ተለይ
ቶኛል ።

611 እናርጅ ፡ እንቀመጥ ፡ እናውጋም ፡ መልካም ፡ ነው ፤
—ወደ ፡ ዳሞት ፡ መሄድ ፡ መንገዱ ፡ ክፉ ፡ ነው ።

1 ሠ ፡ እናርጅ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ (ጐዣም) ፡ እንቀመጥ ።
ወ ፡ ዕድሜያችን ፡ እስኪገፋ ፡ እንኑር ።

2 ሠ ፡ እናውጋም ፡ (ጐዣም) ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ጥሩ ፡ ነው ።
ወ ፡ ማውጋቱ ፡ የቀድሞውን ፡ እያስታወሱ ፡ ነገርን ፡ ለትውልድ ፡ ማስ
ጠናቱ ፡ መልካም ፡ ነው ።

3 ሠ ፡ የዳሞት ፡ መንገድ ፡ አስቸጋሪ ፡ አሰቃቂ ፡ ነው ።
ወ ፡ የሞት ፡ ዕዳ ፡ ክፉ ፡ ነው ፤ እንደሱ ፡ የሚያሠጋ ፡ የሚያስጨንቅ ፡
የለም ።

612 እናታችን ፡ መነን ፡ የት ፡ ትሄጃለሽ ፤
—የሙቶቹን ፡ ልጆች ፡ አለምን ፡ ትተሽ ።

ሠ ፡ አባት ፡ እናት ፡ የሌላቸውን ፡ የድኾች ፡ ልጆች ፡ ያለምናምን ፡ እንዲ
ያው ፡ ትተሻቸው ፡ የት ፡ ትሄጃለሽ ።
ወ ፡ የሟቾች ፡ መኖሪያ ፡ የሆነችውን ፡ ዓለም ፡ ትተሽ ፡ እናታችን ፡ መነን ፡
ሄድሽን ።

613 እናቴ ፡ ቤት ፡ ሄጄ ፡ የመጣሁበትን ፡ ገና ፡ ሳልናገር ፡
—በሆድህ ፡ ምን ፡ አለ ፡ ብላ ፡ ትለኝ ፡ ነበር ።

ሠ ፡ የምትነግረኝ ፡ ምን ፡ ምስጢር ፡ አለህ ፤ በሆድህ ፡ ምን ፡ የደበቅኸው ፡
ነገር ፡ አለ ፡ ብላ ፡ ትጠይቀኝ ፡ ነበር ።
ወ ፡ ባዶ ፡ ሆድህን ፡ ነህ ፡ እኽል ፡ ቅመስ ፡ እያለች ፡ በሰዓቱ ፡ ትመግበኝ ፡
ጕዳቴን ፡ ታውቅልኝ ፡ ነበር ።

614 እናቴ ፡ ነይ ፡ ወዲህ ፡ ባንቺ ፡ አይተኩሰው ፡
—ነፍጠኛው ፡ ዘለቀ ፡ ታሦ ፡ በባሻው ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ነፍጠኛው ፡ እንዳይተኵስብሽ ፡ ሰወር ፡ በይ ፤ ወደኔ ፡ ነይ ፤ ከፊቱ ፡
ገለል ፡ በይለት ።
ወ ፡ ባንቺ ፡ በርጎርጎቷ ፤ ባዛኝዋ ፡ እግር ፡ ማንን ፡ ይተኳል ።

615 እናቴን ፡ አርግጌ ፡ ሆዴ ፡ ይላወሳል ፤
—ሳልገላገላት ፡ የኔም ፡ ቀን ፡ ይደርሳል ።

ሠ ፡ ለደግነትሽ ፡ ወደር ፡ የሌለው ፡ እምዬ ፡ ሞትሽብኝ ፤ ሐዘንሽ ፡ በሆዴ ፡ ተፀነሰ ።

ወ ፡ በናቴ ፡ ሞት ፡ ሳዝን ፡ ስተክዝ ፡ በሐዘን ፡ ስቀጠቀጥ ፤ የኔም ፡ ዕለተ ፡ ሞት ፡ ይመጣል ።

616 እናቴ ፡ ገበያ ፡ ለምን ፡ ትሄጃለሽ ፤
—እኔም ፡ አለቅሳለሁ ፡ ላንቺም ፡ ዋጋ ፡ የለሽ ።

ሠ ፡ አንቺም ፡ በከንቱ ፡ ትለፊያለሽ ፤ እኔም ፡ በብቸኝነቴ ፡ ሳለቅስ ፡ እውላለሁ ፤ ጥለሽኝ ፡ ገበያ ፡ መሄድሽ ፡ ይቅር ፤ የዛሬን ፡ እቤት ፡ ዋይ ።

ወ ፡ እምዬ ፡ በሞትሽ ፡ ባዝን ፡ ብተክዝ ፡ ለድካምሽ ፡ ዋጋ ፡ አይገኝለትም ፤ ብድርሽ ፡ ሊከፈል ፡ አይቻልም ፤ ወሮታሽ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤ የሚመለስ ፡ አይደለም ።

617 እናት ፡ አባት ፡ ንቃ ፡ ወጥታ ፡ ከፈቃድ ፤
—እዩዋት ፡ ይህችን ፡ ልጅ ፡ ባልጋ ፡ ስትሄድ ።

ሠ ፡ እዩዋት ፡ ባለጌ ፡ ሆና ፡ ከናት ፡ ካባቷ ፡ ፈቃድ ፡ ወጥታ ፡ ስትኰበልል ፤ የወላጆቿን ፡ ምክር ፡ ጥሳ ፡ ስትሄድ ፡ ተመልከቷት ።

ወ ፡ ሞታ ፡ በአልጋ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ለመቀበር ፡ ተጓዘች ።

618 እናንት ፡ መኳንንቶች ፡ በምን ፡ ወጥ ፡ በላችሁ ፤
—እኛም ፡ በሽሯችን ፡ እናንተም ፡ ባሣችሁ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ መኳንንቶች ፤ እናንተ ፡ በዓሣ ፡ ወጥ ፡ ስትመገቡ ፡ እኛ ፡ በሽሮ ፡ በላን ፤ እንደ ፡ እናንተ ፡ ዓሣ ፡ ሳናገኝ ፡ ቀረን ።

ወ ፡ ከኛ ፡ ከጦም ፡ አዳሪዎቹ ፡ እናንተ ፡ መኳንንቶቹ ፡ ይልቅ ፡ ችግረኞች ፡ መስላችሁ ፡ ትገኛላችሁ ፤ ልመናው ፡ ደጅ ፡ ጥናቱ ፡ በናንተ ፡ ባሰ ፤ ተራ ፡ አልሰጥ ፡ አላችሁ ።

619 እናንት ፡ መኳንንቶች ፡ አልጋ ፡ ላይ ፡ ያላችሁ ፡
—እሥር ፡ ብርሌ ፡ አለ ፡ ትሰብሩታላችሁ ።

ሠ ፡ እናንተ ፡ አልጋ ፡ ላይ ፡ ያላችሁ ፡ መኳንንቶች ፤ ከአልጋው ፡ ሥር ፡ ያለውን ፡ ብርሌ ፡ እንዳትሰብሩ ፡ ተጠንቀቁ ።

ወ ፡ እስረኛውን ፡ ደጃዝማች ፡ ብርሌን ፡ አታጥቁት ፤ አትጨቍኑት ።

620 እናዝሬት ፡ ለመሄድ ፡ በብሾፍቱ ፡ በኩል ፡
—በመኪና ፡ አለፉ ፡ የሐረሩ ፡ ልዑል ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ የሐረሩ ፡ መስፍን ፡ በመኪና ፡ ተቀምጠው ፡ በቢሾፍቱ ፡ በኩል ፡ ሄዱ፤ በዚያ ፡ አድርገው ፡ አለፉ ።

ወ ፡ የሐረር ፡ ገዥ ፡ የነበሩት ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ በመኪና ፡ አደጋ ፡ ሞቱ፤ እቢሾፍቱ ፡ አጠገብ ፡ ዐረፉ ።

621 እኔ ፡ ምን ፡ ቸገረኝ ፡ ቢሰበር ፡ ዋዲያቱ ፤
—ደቂ ፡ አለ ፡ ጌታዬ ፡ የበላሁበቱ ።

ሠ ፡ ጌታዬ ፡ የበሉበት ፡ ወጭት ፡ አለ ፤ እሱ ፡ እንደ ፡ ዋዲያቱ ፡ አልተሰ በረም ።

ወ ፡ ያበላኝ ፡ ያጠጣኝ ፡ የነበረው ፡ ጌታዬ ፡ ሞተ ፤ ወየው ፡ ወየው ፡ ዐፈር ፡ ሆነና ፡ ቀረ ።

622 እኔስ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ ያ ፡ የቆመው ፡ ሰው ፤
—ለካስ ፡ ዐፈር ፡ ኖሯል ፡ ሰው ፡ የመሰለው ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ሰው ፡ መስሎ ፡ የታየኝ ፡ ዲብ ፡ ኖሯል ፤ የተቈለለ ፡ ዐፈር ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፤ ለካ ፡ ይህ ፡ የማየው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ ዐፈር ፡ ኗኝ ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ ፈራሽ ፡ በስባሽ ፡ ኖሯል ።

623 እኔስ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ ድኻ ፡ ነው ፡ ደካሚ ፤
—ለካስ ፡ ሁሉም ፡ ኖሯል ፡ ዐፈር ፡ ተሸካሚ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ዐፈር ፡ የሚሸከም ፡ ድኻ ፡ ብቻ ፡ ይመስለኝ ፡ ነበር ፤ ለካስ ፡ ሁሉም ፡ ዐፈር ፡ አጋዥ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ በሞት ፡ ዘንድ ፡ ሁሉም ፡ እኩል ፡ ነው ፤ ትንሹም ፡ ትልቁም ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ይገባል ፤ ካፈር ፡ በታች ፡ ይውላል ።

624 እኔስ ፡ ሰምቻለሁ ፡ ግራ ፡ እንደ ፡ ገባዎ ፤
—ባዶ ፡ ቤት ፡ እያለ ፡ አለመግባትዎ ።

ሠ ፡ ከቤት ፡ ሰው ፡ ሳይኖር ፡ ቈይታ ፡ ሳይያዝበት ፡ እደጅ ፡ መቆምዎ ፤ ግራ ፡ እንደ ፡ ገባዎ ፡ ያመለክታል ፤ ችግርዎንም ፡ ይገልጻል ።

ወ ፡ ቅቤው ፡ የወጣለት ፡ አሬራ ፡ ባዶ ፡ እያለ ፡ ለምን ፡ እቤት ፡ ገብተው ፡ አልተጋበዙም ።

625 እኔስ ፡ ቡናም ፡ የለኝ ፡ የወቄት ፡ እኩል ፤
—አንተ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ አፍላ ፡ ንጉሥ ፡ ሚካኤል ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ቡና ፡ አይቸግርህም ፤ አሁንም ፡ አሁንም ፡ በየሰዓቱ ፡ እየደጋ ገምህ ፡ አፍላ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ጥርኝ ፡ ቡና ፡ ስለሌለኝ ፡ ላፈላ ፡ አልቻል ሁም ።

ወ ፡ አንተ ፡ ንጉሥ ፡ ሚካኤል ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አታረጅ ፤ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ጕልማሳ ፡ ነህ ፤ ልጅ ፡ እንደ ፡ መሰልህ ፡ ትኖራለህ ፤ እርጅና ፡ አይ ታይብህም ።

626 እኔስ ፡ ብዬ ፡ ነበር ፡ ትዳር ፡ ትይዛለች ፤
—እሷም ፡ እንደ ፡ እኅቷ ፡ ቶሎ ፡ ባልጋ ፡ ሄደች ።

ሠ ፡ እሷም ፡ እንደ ፡ እኅቷ ፡ ባለጌ ፡ ሆና ፡ ከፈቃድ ፡ ወጥታ ፡ ሄደች ፤ ም ክር ፡ ጥሳ ፡ ኰበለለች ።

ወ ፡ እንደ ፡ እኅቷ ፡ ሞታ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ተወሰደች ።

627 እኔስ ፡ እሄዳለሁ ፡ አጣቢ ፡ ፍለጋ ፤
—በጣም ፡ አድፎብኛል ፡ የለበስኩት ፡ ሥጋ ።

ሠ ፡ ልብሴ ፡ በጣም ፡ አድፏል ፤ እላዬ ፡ ላይ ፡ ጨቅይቷል ፤ አጣቢ ፡ ፍለጋ ፡ ልሂድ ፤ የሚያለቀልቅልኝ ፡ ልፈልግ ።

ወ ፡ ሥጋዬ ፡ እግዚአብሔርን ፡ በመበደል ፡ ሰውን ፡ በማስቀየም ፡ በኀጢአት ፡ አድፏል ፤ የሚያስተሰርይ ፡ ቄስ ፡ ለመፈለግ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ልሂድ ።

628 እኔስ ፡ ፍረድ ፡ ቢሉኝ ፡ ሞት ፡ በደለኛ ፡ ነው ፤
—አንድ ፡ ሰው ፡ ለምስል ፡ ቆሞስ ፡ ቢቀር ፡ ምነው ።

ሠ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ለወሬ ፡ ነጋሪ ፡ ለላንቲካ ፡ ቆሞ ፡ ቢቀር ፡ ሳይሞት ፡ በሕይወት ፡ ቢኖር ፤ ምን ፡ ነበረበት ።

ወ ፡ ሞት ፡ አሁን ፡ ቆሞሱን ፡ ባይገድለው ፡ ጥቂት ፡ ቢያሰነብተው ፡ ምን ፡ ነበረ ፤ ለምን ፡ ቸኵሎ ፡ ወሰደው ።

629 እኔ ፡ ችግር ፡ ስሸሽ ፡ እሱ ፡ ሲያባርረኝ ፡
—አሰላ ፡ መጣና ፡ እመረመር ፡ ጣለኝ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አድብቶ ፡ መጥቶ ፡ እጕድባ ፡ ውስጥ ፡ ጥሎኝ ፡ ሄደ ፤ ከፈረፈር ፡ ከቶኝ ፡ አመለጠ ።

ወ ፡ ያልፍልኛል ፡ ብዬ ፡ አሰላ ፡ ብሄድ ፡ ችግሬ ፡ የማይወገድልኝ ፡ ሆነ ፤ እንዲያውም ፡ እየባሰ ፡ ሄደ ፤ ራሴን ፡ መቻል ፡ አልሆነልኝም ።

630 እኔ ፡ አላይም ፡ እንጂ ፡ አንተ ፡ ታየኛለህ ፤
—ባሞራ ፡ ሆድ ፡ ሆነህ ፡ በደጄ ፡ ታልፋለህ ።

ሠ ፡ ያሞራ ፡ ሆድ ፡ በሚባለው ፡ መንገድ ፡ ስትሄድ ፡ የምታልፈው ፡ በኔ ፡ ደጅ ፡ ነው ፤ ስታልፍ ፡ ስታገድም ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ሳታየኝ ፡ አትቀርም ።

ወ ፡ በበላህ ፡ አሞራ ፡ ሆድ ፡ ውስጥ ፡ ሆነህ ፡ በደጄ ፡ ታልፋለህ ፤ ሥጋህን ፡ የተካፈሉት ፡ አዕዋፈ ፡ ሰማይ ፡ በቤቴ ፡ ላይ ፡ እያንዣበቡ ፡ ያልፋሉ ።

631 እኔ ፡ አልበላም ፡ ሥጋ ፡ ባለጌ ፡ ያረደው ፤
—ጌታው ፡ በጕራዶ ፡ ታላወራረደው ።

ሠ ፡ ጌታዬ ፡ ካልባረከው ፡ ማንም ፡ ያረደውን ፡ ሥጋ ፡ አልበላም ፤ አራጁን ፡ ካላወቅሁት ፡ ሥጋውን ፡ አልቀምስም ።

ወ ፡ ጌታዬ ፡ ጠላቱን ፡ በጕራዶ ፡ ጨፍጭፎ ፡ ድል ፡ አድርጎ ፡ እቤቱ ፡ ካልገባ ፤ እኽል ፡ አልቀምስም ።

632 እኔ ፡ አምላክን ፡ ብሆን ፡ በጕልበቴ ፡ አልኰራም ፤
—ላላሰነብተው ፡ ላፈር ፡ ሰው ፡ አልሠራም ።

ሠ ፡ እኔ ፡ እሱን ፡ ብሆን ፡ ኖሮ ፡ ሠርቶ ፡ ለማፍረስ ፡ ክቦ ፡ ለመናድ ፡ ቤት ፡ አልሠራም ፡ ነበር ፤ ምንም ፡ ዐቅም ፡ ቢኖረኝ ፡ ተመክቼ ፡ ይህን ፡ አላደርገውም ፡ ነበር ።

ወ ፡ እኔ ፡ አምላክን ፡ ብሆን ፡ ኖሮ ፡ የሚፈርስ ፡ የሚበሰብስ ፡ አድርጌ ፡ ሰውን ፡ አልፈጥረውም ፡ ነበር ፤ ምንም ፡ ከሃሊ ፡ ብሆን ፡ ይህን ፡ አል ሠራም ፡ ነበር ፤ (ብስጭትና ፡ ሐዘን) ።

633 እኔ ፡ እማስናለሁ ፡ በከንቱ ፡ ዝም ፡ ብዬ ፤
ወይኔ ፡ እደክማለሁ ፡ በከንቱ ፡ ዝም ፡ ብዬ ፤
—ከብት ፡ የሚያፈርሰውን ፡ ቤት ፡ እሠራ ፡ ብዬ ።

ሠ ፡ ከብት ፡ ታኮ ፡ የሚጥለውን ፤ በቀንዱ ፡ የሚመነቃቅረውን ፡ ቤት ፡ እ ሠራለሁ ፡ ብዬ ፡ እለፋለሁ ፤ እጥራለሁ ፤ በከንቱ ፡ እደክማለሁ ።

ወ ፡ ካብት ፡ ወገን ፡ ያለው ፡ ሊያሸንፈኝ ፡ ሊያፈርስብኝ ፤ እንዲያው ፡ እደ ክማለሁ ።

634 እኔ ፡ እዘጋዋለሁ ፡ ቤቴን ፡ እንዳመሉ ፤
—ቢጠይቋችሁም ፡ ከፍቶት ፡ ሄደ ፡ በሉ ። (1)

ሠ ፡ የተጠየቃችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ በሩን ፡ ሳይዘጋው ፡ ሄደ ፡ ብላችሁ ፡ ንገ ሯቸው ።

ወ ፡ ተቀይሞ ፡ አኩርፎ ፡ ሄደ ፤ ሆድ ፡ ብሶት ፡ ተከፍቶ ፡ ካገር ፡ ወጣ ፡ ብላ ችሁ ፡ ንገሩ ።

635 እኔ ፡ እዚህ ፡ አላድርም ፡ አሁን ፡ እሄዳለሁ ፤
—ብዙ ፡ የሰው ፡ ሸክላ ፡ ከቤቱ ፡ አኑሪያለሁ ።

ሠ ፡ የሰው ፡ ማሰሮ ፡ ድስት ፡ እንስራ ፡ ከቤት ፡ ውስጥ ፡ አለ ፤ እሱን ፡ ጥዬ ፡ እኔ ፡ እዚህ ፡ አላድርም ።

ወ ፡ እንደ ፡ ሸክላ ፡ ተሰባሪ ፡ የሆኑ ፡ በጣም ፡ የሚያሳስቡ ፡ ብዙ ፡ ልጆች ፡ ከቤት ፡ ትቻለሁ ፤ በጣም ፡ እሠጋለሁ ፤ እነሱን ፡ ትቼ ፡ እኔ ፡ እዚህ ፡ ማምሸት ፡ አይሆንልኝም ።

636 እኔ ፡ እየመከርኩህ ፡ አንተ ፡ እየተቈጣህ ፡
—ለኔም ፡ መቀመጫ ፡ ላንተም ፡ መቆሚያ ፡ አጣህ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ጧሪ ፡ ቀባሪ ፡ አጣሁ ፤ የሚያኖረኝ ፡ የሚያስጠጋኝ ፡ ሰው ፡ ተቸ ገርሁ ፤ አንተም ፡ ዘዋሪ ፡ ዋቶ ፡ አዳሪ ፡ ሆንህ ፤ መቅኖ ፡ አጣህ ፤ እን ኳን ፡ ለኔ ፡ ለራስህ ፡ ሳትበቃ ፡ ቀረህ ።

ወ ፡ አንተም ፡ መቆሚያ ፡ መሄጃ ፡ እግር ፡ አጣህ ።

637 እኔ ፡ ከእኽል ፡ ጋራ ፡ ይቅርታም ፡ የለኝ ፤
—ሲያልቁ ፡ ዘመዶቼ ፡ ይብላኝ ፡ ያላለኝ ።

ሠ ፡ ከልብ ፡ ተቀይሜዋለሁ ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ አላነጋግረውም ፤ ይቅር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አልለውም ፤ ዘመዶቼ ፡ አልቀው ፡ ከለቅ ሶዬ ፡ አልመጣም ፤ አላዋየኝም ።

ወ ፡ የእኽል ፡ ማጣት ፡ ከማናቸውም ፡ ዐይነት ፡ ችግር ፡ የበለጠ ፡ ነው ፤ ዘመዶቼ ፡ ያለቁት ፡ በእኽል ፡ እጦት ፡ ነው ።

(1) ብላታ ፡ የኋላ ፡ እሸት ፡ የሚባሉ ፡ ሰው ፡ ሚስት ፡ አግብተው ፡ ልጆች ፡ ወልደው ፡ ንብ ረታቸውን ፡ አቃንተው ፡ በጤና ፡ ሲኖሩ ፡ ልጆቻቸው ፡ በፈንጣጣና ፡ በኮፍኝ ፡ እያሉ ፡ አለቁ ፤ ሚስታቸውም ፡ በወሊድ ፡ ሞቱ ፤ ከዚህ ፡ በኋላ ፡ ሐዘን ፡ ስለ ፡ ጠነከረባቸው ፡ ይህነን ፡ ግጥም ፡ጽፈው ፡ ከመዝጊያ ፡ ላይ ፡ ለጥፈው ፡ ጠፉ ፡ ይባላል ።

638 እኔ ፡ የማለቅሰው ፡ ለናቴ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤
—አይወጣም ፡ ከሆዴ ፡ ልጄማ ፡ አገሩ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ልጄ ፡ ከሀገሩ ፡ ከሆዴ ፡ አይሄድም ፤ ከተወለደበት ፡ አገር ፡ አይወጣም ፤ የናቱን ፡ ቦታ ፡ ለቆ ፡ የትም ፡ አይላወስም ።

ወ ፡ ለናቴ ፡ አዝናለሁ ፤ አለቅሳለሁ ፤ የልጄ ፡ ሞት ፡ ግን ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አይረሳኝም ፤ ከሆዴ ፡ አይወጣም ፤ ያንገበግበኛል ፤ ያቃጥለኛል ፤ አንዝቱን ፡ እንደ ፡ በላው ፡ ይኖራል ።

639 እኔ ፡ ድኻ ፡ መስሎኝ ፡ ተራቁቶ ፡ ባየው ፤
—ለካስ ፡ ጌታ ፡ ኖሯል ፡ የተሰቀለው ።

ሠ ፡ ዕራቁቱን ፡ ባየው ፡ ድኻ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፤ ለካስ ፡ የተሰቀለው ፡ ከበርቲ ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ የተረፈው ፡ ጌታ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ለካስ ፡ በመስቀል ፡ ላይ ፡ ዕራቁቱን ፡ ተሰቅሎ ፡ የዋለው ፡ ጌታችን ፡ ፈጣሪያችን ፡ ኖሯል ።

640 እንማከር ፡ እቴ ፡ ስለ ፡ ትዳራችን ፤
—ጣይቱ ፡ ሳትጠልቅ ፡ እንግባ ፡ አገራችን ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 315 ፡ 362)፡

ሠ ፡ በጊዜ ፡ ፀሐይ ፡ ሳትገባ ፡ ሳይመሽብን ፡ በብርሃን ፡ አሁኑኑ ፡ እንንዝ ፤ ሲታየን ፡ ወደ ፡ አገራችን ፡ እንሂድ ።

ወ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ አንድ ፡ ነገር ፡ ሳትሆን ፡ በመንግሥቷና ፡ በሥልጣኗ ፡ ሳለች ፡ ወደ ፡ ስፍራችን ፡ እንመለስ ።

641 እንሄዳለን ፡ ብለን ፡ ቆመን ፡ ብናስበው ፡
እጅግ ፡ ያለመጠን ፡ መንገዱ ፡ ረዥም ፡ ነው ፤
—እረ ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ሞያ ፡ ማደሪያ ፡ ነው ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ መንገዱ ፡ ሩቅ ፡ ነው ፤ ውሎ ፡ ገባ ፡ አይደረስም ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ አይገባም ፤ አውሎ ፡ ያሳድራል ።

ወ ፡ ዕውቀት ፡ የጅ ፡ ብልኀት ፡ የኑሮ ፡ ማሻሻያ ፡ ይሆናል ፤ ትምህርት ፡ መተዳደሪያ ፡ የንብረት ፡ መጠገኛ ፡ ነው ።

642 ዕንቅፋቱ ፡ ይምታህ ፡ እሾኹም ፡ ይውጋህ ፤
እንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ጫማ ፡ አልገዛልህ ፤
—የት ፡ አባትክ ፡ አንተ ፡ እግሬ ፡ ታዞረኛለህ ።

ሠ ፡ አሁንስ ፡ እግሬን ፡ እንኳ ፡ ጠላሁት ፤ ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ የሚያዞረኝና ፡ የሚያንከራትተኝ ፡ እሱ ፡ አይደለምን ።

ወ ፡ አንተ ፡ የትግሬ ፡ ሰው ፡ ወዴት ፡ ነው ፡ የምታንከራትተኝና ፡ እንደዚህ ፡ አገር ፡ ላገር ፡ የምታዞረኝ ።

643 እንባማ ፡ ይወጣል ፡ ለተራ ፡ ወዳጅ ፤
—ዐይኔ ፡ ደም ፡ አልቅሰህ ፡ ባሳየኸኝ ፡ እንጂ ።

ሠ ፡ እንባማ ፡ ለሆነ ፡ ላልሆነው ፡ ለማናቸውም ፡ ወዳጅ ፡ እኩል ፡ ይፈ
ሳል ፤ ለሚያውቁት ፡ ሁሉ ፡ ይወርዳል ፤ ዐይኔ ፡ ለዚህ ፡ ለወዳጄ ፡ ደም፡
አልቅስለት ።

ወ ፡ ዐይኔ ፡ (አገር) ፡ መከራ ፡ የተቀበልከውን ፡ ያኸል ፡ ብድርህን ፤ ቍጭ
ትህን ፡ ተወጥተህ ፡ ምነው ፡ ባሳየኸኝ ።

644 እንታገል ፡ አለኝ ፡ ያገሬ ፡ ቢንቀኝ ፤
—እኔ ፡ እንዳሸንፈው ፡ እንድጥለው ፡ ሲያውቀኝ ።

ሠ ፡ በትግል ፡ እንደማይችል ፡ ሆዱ ፡ እያወቀ ፡ እንታገል ፤ ግብግብ ፡ እን
ያያዝ ፡ ይለኛል ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ ጥሬ ፡ ግሬ ፡ የማይሆንልኝ ፡ መሆኑን ፡ ሳውቀው ፤ መሸነ
ፌን ፡ ስረዳው ፤ አገሬን ፡ ጥዬ ፡ ቤት ፡ ንብረቴን ፡ ትቼ ፡ መሄዴ ፡ ነው።

645 እንኳን ፡ ሰይፋን ፡ መዘህ ፡ በጅህ ፡ ጨብጠህ ፡
—ከመላው ፡ ኀይለኛ ፡ ሶምሶን ፡ አንተ ፡ ነህ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ሶምሶን ፤ ከመላው ፡ ከአዳም ፡ ዘር ፡ እንዳንተ ፡ ኀይልን ፡ ያገኘ ፡ ፍጥ
ረት ፡ የለም ፤ ልዩ ፡ ፍጡር ፡ ነህ ፤ የእግዚአብሔር ፡ ተአምር ፡ የታየ
ብህ ፡ ሰው ፡ ነህ ።

ወ ፡ ሶምሶን ፤ ሰይፋን ፡ የመሰለ ፡ አባት ፡ አለህ ፤ እጅግ ፡ ዕድለኛ ፡ ነህ ፤
ከደኅና ፡ ሰው ፡ ተወልደሃል ።

646 እንኳን ፡ በቡቃያ ፡ በድንበር ፡ አይደርሱ ፤
—ፈረሶችህ ፡ ዛሬ ፡ በወግ ፡ አስለቀሱ ።

ሠ ፡ ቡቃያ ፡ የማያጠፉት ፡ የሰው ፡ ድንበር ፡ የማያልፉት ፡ ፈረሶችህ ፤
ዛሬስ ፡ ሰዉን ፡ ሲያስቸግሩት ፡ ዋሉ ።

ወ ፡ ወዳጅ ፡ ዘመድህ ፡ ፈረሶችህን ፡ እያየ ፡ ኮርቻህን ፡ እየተመለከተ ፡
ሲያለቅስልህ ፡ ዋለ ።

647 እንኳን ፡ ነአኵተከ ፡ በስመ ፡ አብም ፡ ቸገረኝ ፡
—ዳዊት ፡ እንዴት ፡ ተማርክ ፡ እባክህ ፡ ንገረኝ ።

ሠ ፡ መዝሙረ ፡ ዳዊቱን ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ አጠናኸው ፡ በምን ፡ ዐይነት ፡
ዘዴ ፡ እንደ ፡ ቀጸልኸው ፡ እስቲ ፡ እባክህን ፡ አስረዳኝ ፤ ያጠናኑን ፡
መንገድ ፡ ንገረኝ ።

ወ ፡ ንጉሥ ፡ ዳዊት ፤ ይቅርታን ፡ ምሕረትን ፡ እንዴት ፡ አገኘህ ፤ ፈጣሪህ ፡
ምን ፡ ምን ፡ ብታደርግ ፡ ነው ፡ የታረቀህ ፤ አሁን ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ብሠራ ፡
በደሌ ፡ ይፋቅልኝ ፡ ይሆን ፤ እስቲ ፡ እባክህ ፡ አማልደኝ ።

648 እንኳን ፡ አገኘነው ፡ አብሮ ፡ አልተቀበረ ፤
—ጥንትም ፡ የሚያዝንልህ ፡ አንገቷ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ ደግ ፡ አንገቷ ፡ ለምልክት ፡ ተገኘ ፤ እንኳን ፡ አውሬ ፡ አልበላው ።

ወ ፡ ዱሮም ፡ የሚራራልኝና ፡ ወላላ ፡ የነበረው ፡ አንገቷ ፡ ነበር ፤ አሁ
ንም ፡ ከመላ ፡ ሰውነቷ ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ የቀረው ፡ እኔን ፡ ሲል ፡ ነው ።

649　እንደ ፡ ምን ፡ አልፎከር ፡ ምነው ፡ አልሸልል ፤
—ታግዬ ፡ ታግዬ ፡ አገሬን ፡ ስጥል ።　　　(ዘለ ፡ ቍ ፡ 708) ፡

ሠ ፡ ግብግብ ፡ ተያይዘን ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ተፍጨርጭሬ ፡ አገሬን ፡ ያኽል ፡ ሰው ፡ ስጥል ፡ መፎከር ፡ መሸለል ፡ አይገባኝምን ።

ወ ፡ ለፍቼ ፡ ለፍቼ ፡ ብዙ ፡ ቁም ፡ ነገር ፡ ያለው ፡ ውለታ ፡ ሠርቼ ፡ በመጨረሻው ፡ አገሬን ፡ ጥዬ ፡ ቀርበት ፡ ጠቅልዬ ፡ ስሄድ ፤ አያሳዝንምን ።

650　እንደ ፡ ምን ፡ አማረ ፡ አሻግረን ፡ ብናይ ፤
—የሰጐን ፡ ዕንቍላል ፡ በሚካኤል ፡ ላይ ።

ሠ ፡ በቅዱስ ፡ ሚካኤል ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ የሰጐን ፡ ዕንቍላል ፡ ያምራል ፤ ከጕልላቱ ፡ ጋራ ፡ ተስማምቷል ።

ወ ፡ የሊጋባ ፡ ሰጐን ፡ ልጅ ፡ በንጉሥ ፡ ሚካኤል ፡ ቤት ፡ እንደ ፡ ምን ፡ አድርጎ ፡ ሠለጠነ ፤ አማረበት ፡ ሥራውን ፡ ዐወቀ ።

651　እንደ ፡ ሳቢሳ ፡ ይበር ፡ መስሎት ፡ ነበር ፡ እንጂ ፤
—ክንፉን ፡ ሰብሮ ፡ ያዘው ፡ ያባ ፡ ጃሌ ፡ ልጅ ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ሳቢሳ ፡ የሚበር ፡ መስሎት ፡ ያባ ፡ ጃሌ ፡ ልጅ ፡ ያገኘውን ፡ ወፍ ፡ ክንፉን ፡ ሰብሮ ፡ ያዘው ።

ወ ፡ ያባ ፡ ጃሌ ፡ ልጅ ፡ ክንፉ ፡ የሚባለውን ፡ ሰው ፡ ድል ፡ አድርጎ ፡ ኀይሉን ፡ ሰባብሮ ፡ ተምችፐ ፡ መቶ ፡ ያዘው ።

652　እንደ ፡ ብሩ ፡ ጐሹ ፡ ካፍቀራ ፡ ገሥግሠው ፡
—እስቲ ፡ ማየትዎን ፡ ይነግሩታል ፡ ለሰው ።

ሠ ፡ ካፍቀራ ፡ ሄደው ፡ እንደ ፡ ብሩ ፡ ጐሹ ፡ ያዩትን ፡ ሁሉ ፡ እስቲ ፡ ለሰው ፡ እንዳይነግሩ ፤ ምስጢር ፡ እንዳያወጡ ።

ወ ፡ ካፍቀራ ፡ ሲወጡ ፡ «እስቴ» ፡ አገርዎን ፡ ማየትዎን ፡ ከተወለዱበት ፡ ቦታ ፡ መግባትዎን ፡ ያወሩልናል ፤ እስራትዎን ፡ ያወጉናል ።

653　—እንደ ፡ ተገኘ ፡ ነው ፡ በጊዜ ፡ መብላት ፤
አሁን ፡ ምን ፡ ያደርጋል ፡ የማታው ፡ እራት ።

ሠ ፡ ምግብ ፡ ሲገኝ ፡ በሆነው ፡ ሰዓት ፡ መብላት ፡ ነው ፤ ጊዜ ፡ ቢደርስ ፡ ባይደርስ ፡ ግድ ፡ የለም ፤ ምን ፡ ጊዜም ፡ የተገኘውን ፡ መመገብ ፡ ነው ።

ወ ፡ ካረጁ ፡ በኋላ ፡ ገንዘብ ፡ ለመሰብሰብ ፡ ከመጣጣር ፡ ጕልበት ፡ ሳይደክም ፡ እንደ ፡ «ተገኘ» ፡ መሰብሰብ ፡ ነው ።

654　እንደ ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ ሰው ፡ እንዳጣ ፡ ሲሳይ ፡
—ውሻ ፡ በላህ ፡ አሉ ፡ ይጣፍጣል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ተቸገርክና ፡ ተራብክና ፤ የውሻ ፡ ሥጋ ፡ በላህን ።

ወ ፡ ውሻ ፡ ነከሰህን ፤ ምን ፡ ነበር ፡ ብትጠነቀቅ ፡ ኖሮ ።

655 እንደ ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ አለየሁም ፡ ኰሩ ፤
ቢመጡ ፡ እንግሊዞች ፡ ምክር ፡ ሊማከሩ ፡
—ባርምሞ ፡ ሽኙዋቸው ፡ ሳያነጋግሩ ።

ሠ ፡ ቃል ፡ ሳይተነፍሱላቸው ፡ ክፉና ፡ ደግ ፡ ሳያነጋግሯቸው ፡ በዝምታ ፡ ሸኙዋቸው ።

ወ ፡ ራሳቸውን ፡ በመግደል ፡ ከአንደበታቸው ፡ አንዳች ፡ ነገር ፡ እንዳይ ሰጡ ፡ በሕይወታቸው ፡ እጃቸው ፡ እንዳይያዝ ፡ አደረጉ ።

656 እንደዚያ ፡ ሲጽፉ ፡ በብረቱ ፡ ብር ፤
—ዛሬስ ፡ ምነው ፡ ያዙ ፡ ያንን ፡ መቃ ፡ ብር ።

ሠ ፡ ምነው ፡ ዛሬስ ፡ የብረት ፡ ብሩን ፡ ትተው ፡ በሸንበቆ ፡ ብር ፡ ይጽ ፉሉ ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ አሳብ ፡ ቀረና ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ገቡን ፤ ዐፈር ፡ ተመለሰብዎትን ።

657 እንደ ፡ ዛሬው ፡ ሁሉ ፡ ቁመቴ ፡ ሳያጥር ፡
—በማዘን ፡ ላይ ፡ ቆሜ ፡ ይታየኝ ፡ ነበር ፡ ጀር ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ እንደ ፡ ዛሬ ፡ ሳላጥር ፡ ሳልጐብጥ ፡ እማእዘን ፡ ዕንጨት ፡ ላይ ፡ እየ ቆምሁ ፡ ጀርን ፡ አየው ፡ ነበር ።

ወ ፡ እንዳሁኑ ፡ ኀጢአተኛ ፡ ሳልሆን ፡ እግዚአብሔርን ፡ ሳልበድል ፡ ክ ፉና ፡ ደጉ ፡ ይገለጽልኝ ፡ ነበር ፤ ሁሉም ፡ በራእይ ፡ ይታየኝ ፡ ነበር ።

658 እንዲሁ ፡ እያፈሡ ፡ ሲሰጡ ፡ ኖረው ፡
ሒሳቡ ፡ እንደ ፡ ሞላ ፡ ብዙ ፡ ዓመት ፡ ሠርተው ፡
—የግንቦት ፡ ወር ፡ ብቻ ፡ ጐደለባቸው ። (ሰ ፡ ወ ፡ ኪ) ፡

ሠ ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ ዓመት ፡ ሲሠሩ ፡ ገንዘብ ፡ ጠፍቶባቸው ፡ ሒሳብ ፡ ተሳስቶባቸው ፡ አያውቁም ፡ ነበር ፤ ዛሬ ፡ ግን ፡ የግንቦት ፡ ወር ፡ ሒ ሳብ ፡ ጐደለባቸው ።

ወ ፡ ያምላክ ፡ ፍርጃ ፡ ቀን ፡ ጐደሎ ፡ ሆኖ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ኃ ፡ ሥ ፡ በግንቦት ፡ ወር ፡ ሞቱ ፤ የተቀጠበባቸውን ፡ ሰዓት ፡ ማለፍ ፡ ሳይሆን ላቸው ፡ ቀረ ፤ ባልታሰበ ፡ አደጋ ፡ ዐረፉ ።

659 እንግዲህ ፡ ነገሬን ፡ ከከንፈሬ ፡ አለቅም ፤
—የሰው ፡ ዶሮ ፡ አለና ፡ ካፍ ፡ ካፍ ፡ የሚለቅም ።

ሠ ፡ አንድ ፡ ከጎረ ፡ ቤት ፡ የሚመጣ ፡ የሰው ፡ ዶሮ ፡ አለ ፤ እኽል ፡ አያስ ጣም ፤ ውሎው ፡ ስጥ ፡ ሲጭር ፡ ነው ።

ወ ፡ ወሬ ፡ የሚለቅም ፡ ነገር ፡ የሚያዋሽክ ፡ ሰው ፡ አለ ፤ አንደበቴን ፡ ጠ ብቄ ፡ ከንፈሬን ፡ ሰብስቤ ፡ ልኑር ፤ መቀባጠሩ ፡ ይቅርብኝ ፡ (መዝ ፴፱ ፡ ፩) ።

660 እንዲህን ፡ ክፉ ፡ ነው ፡ ሰው ፡ ከተቸገረ ፤
—ቤቴ ፡ ሲያባርረኝ ፡ ወድቄ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ከተቸገረ ፡ ጨካኝ ፡ ነው ፤ ለሕይወቱም ፡ አይሣሣም ።
ወ ፡ ትዳሬ ፡ ንብረቴ ፡ አልሞላ ፡ ብሎ ፡ አሸንፎኝ ፡ ስዞር ፡ ስንከራተት ፡ አደጋ ፡ ወድቆብኝ ፡ ነበር ።

661 እንዲህ ፡ ውድ ፡ ነወይ ፡ አብራማ ፡ ውሃው ፤
—ከነደሙ ፡ በላሁ ፡ ሳልታጠበው ።

ሠ ፡ አብራማ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ውሃ ፡ ውድ ፡ በመሆኑ ፤ ደም ፡ የነካው ፡ እጄን ፡ ሳልታጠብ ፡ በላሁበት ፤ ከነደሙ ፡ ተመገብሁ ።
ወ ፡ ብድሬን ፡ ሳልወጣ ፡ ደሜን ፡ ሳልበቀል ፡ ከባለጋራዬ ፡ ጋራ ፡ አብሬ፡ በላሁ ፤ አብራማ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ደም ፡ አፍሳሽ ፡ ነፍሰ ፡ ገዳይ ፡ እንዳሻው ፡ ይኖራል ።

662 እንዲያው ፡ ዝም ፡ ማለት ፡ ነው ፡ ከንቱ ፡ መታከት ፤
—ከተሰማ ፡ ወዲያ ፡ ደጃዝማችነት ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ከተሰማ ፡ የበለጠ ፡ የደጃዝማችነት ፡ ማዕርግ ፡ የሚስማማውና ፡ የሚያምርበት ፡ መኰንን ፡ ይገኛል ፡ ብሎ ፡ ማሰብ ፡ መፈለግ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
ወ ፡ መምጣታቸው ፡ ከታወቀ ፡ ከተነገረ ፡ ከተሰማ ፡ በኋላ ፤ የደጃዝማችነት ፡ ማዕርግ ፡ መስጠትና ፡ መሾም ፡ ዋጋ ፡ የሌለው ፡ ነው ።

663 እንዳሰቡት ፡ ሁሉ ፡ አልደረሱም ፡ ዳውንት ፤
—ጨጨሆ ፡ ሲደርሱ ፡ ወረዱ ፡ አሉ ፡ መቄት ።

ሠ ፡ ጨጨሆ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ እንደ ፡ ደረሱ ፡ ወደ ፡ ዳውንት ፡ መጓዙን ፡ ትተው ፡ ወደ ፡ መቄት ፡ አቈልቍለው ፡ ሄዱ ፡ አሉ ፤ ወዳሰቡበት ፡ ቦታ ፡ በቀጥታ ፡ አልተጓዙም ።
ወ ፡ ጨጨሆ ፡ ላይ ፡ ሞተው ፡ ተቀበሩ ።

664 እንዳሻው ፡ ያደገው ፡ የጐዠም ፡ እረኛ ፡
—በሠራው ፡ ቤተ ፡ ክሲያን ፡ እሱ ፡ ገብቶ ፡ ተኛ ።

ሠ ፡ በሠራሁት ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡ ማን ፡ ከልካይ ፡ አለብኝ ፡ ብሎ ፡ ከሠራው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ ገብቶ ፡ ተኛ ፤ ቤቱ ፡ መኖሪያው ፡ አደረገው ።
ወ ፡ የጐዠሙ ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሕዝብ ፡ ጠባቂ ፡ ባሠራው ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ውስጥ ፡ ተቀበረ ።

665 እንዳናለቅስ ፡ እንኳን ፡ ባንድ ፡ ተሰብስበን ፡
—ሞትዎን ፡ በሽጉጥ ፡ ለምን ፡ አረጉብን ።

---

(1) ነጋድራስ ፡ ተሰማ ፡ እሸቴ ፡ የግርማዊነታቸው ፡ መምጣት ፡ ሲሰማ ፡ ጣሊያኖች ፡ የደጃዝማችነት ፡ ማዕርግ ፡ ሰጥተዋቸው ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ ስጦታውን ፡ ለማቃለል ፡ ያኸል ፡ የተናገሩት ።

ሥ ፡ ተሰብስበን ፡ እንዳናለቅስልዎና ፡ እንዳናዝንልዎ ፡ ሞትዎ ፡ ሳይነገር ፡ ተሸሽጎ ፡ እንዲቀር ፡ በምስጢር ፡ እንዲያዝ ፡ ለምን ፡ አደረጉ ።

ወ ፡ ጀግናው ፡ ቴዎድሮስ ፡ ሽኵጥዎን ፡ ጠጥተው ፡ ሞቱ ፡ ወይ ።

666 **እንዳንች ፡ አላየሁም ፡ ካለም ፡ የሚሸሽ ፤**
**—በስምንተኛው ፡ ሺሕ ፡ ትደነቂያለሽ ።** (1) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 911) ፡

ሥ ፡ በዛሬው ፡ ዘመን ፡ በስምንተኛው ፡ ሺሕ ፡ እንዳንቺ ፡ ያለ ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ የሚንቅ ፡ አላየሁም ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ትደነቂያለሽ ፡ ዓለምን ፡ ትተሽ ፡ በምናኔ ፡ ወደ ፡ ኢየሩሳሌም ፡ መሄድሽ ፡ በውነት ፡ ያስደንቃል ፤ ይገርማል ፤ ሐሳበ ፡ ብርቱ ፡ ነሽ ።

667 **እንዳያምረው ፡ ብሎ ፡ ድኻ ፡ ወዳጁን ፡**
**—መተማ ፡ አፈሰሰው ፡ ዮሐንስ ፡ ጠጁን ።**

ሥ ፡ ዮሐንስ ፡ ድኻ ፡ እንዳይጠማው ፡ ብሎ ፡ መተማ ፡ አውርዶ ፡ ጠጁን ፡ ሰጠው ፤ ዐደለው ።

ወ ፡ ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ ያገሬን ፡ ድንበር ፡ አላስደፍርም ፡ ብሎ ፡ መተማ ፡ ላይ ፡ ደሙን ፡ አፈሰሰው ፤ አንገቱን ፡ ለሰይፍ ፡ ሰጠ ።

668 **እንዴት ፡ አንድ ፡ መጠጊያ ፡ በቤቱ ፡ ያጣል ፡ ሰው ፤**
**—አላኰራኝ ፡ አለ ፡ ክንዴን ፡ ብንተራሰው ።**

ሥ ፡ በቤቱ ፡ ውስጥ ፡ ትራስ ፡ አጣሁ ፤ መከዳ ፡ (መጨጊያ) ፡ ተቸገርሁ ፤ እጄን ፡ ብንተራሰው ፡ ይዘቀዝቀኝ ፡ ዠመር ፤ ቀና ፡ አላደርግም ፡ አለኝ ።

ወ ፡ ካደግሁበት ፡ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ ለሥልጣን ፡ ከደረስኩበት ፡ ቤት ፡ እንዴት ፡ አንድ ፡ ተመልካችና ፡ አስታዋሽ ፡ ሰው ፡ አጣሁ ።

669 **እንዴት ፡ አደራችሁ ፡ እረ ፡ እንዴት ፡ ዋላችሁ ፡**
**አሁንም ፡ ቅድምም ፤**
**—ይህ ፡ ያሁኑ ፡ ጊዜ ፡ አያስተማምንም ።** (ራስ ፡ ኀ ፡ ተ ፡ ሃ) ፡

ሥ ፡ ሌቱም ፡ ቀኑም ፡ ስለማይታወቅ ፡ የማታውንም ፡ ሆነ ፡ የቀኑን ፡ ወይም ፡ የጧት ፡ ሰላምታ ፡ ለይቶ ፡ ለመስጠት ፡ አልተቻለም ።

ወ ፡ በዘመናችን ፡ መተማመን ፡ ጠፍቷል ፤ እምነት ፡ ቀርቷል ፤ አሁንም ፡ አሁንም ፡ መገላመጥ ፡ መጠርጠር ፡ ያሻል ፤ ነቅቶ ፡ መኖር ፡ ያስፈልጋል ።

670 **እንዴት ፡ ውላችኋል ፤ ንጉሥ ፡ ወዴት ፡ ዋሉ ፡**
**—እስከ ፡ ጊዜ ፡ ድረስ ፡ ገበያ ፡ ነበሩ ።** (አ ፡ በ) ፡

ሥ ፡ ከጧት ፡ ዠምሮ ፡ እስከ ፡ ቀትር ፡ እገበያ ፡ ነበሩ ፡ እስከ ፡ ሰዓት ፡ ከዚያ ፡ ተቀምጠው ፡ ውለዋል ።

(1) የንጉሥ ፡ ኀይለ ፡ መለኮት ፡ ሚስት ፡ የዚህን ፡ ዓለም ፡ ከንቱነት ፡ በመረዳት ፡ መንነው ፡ ቤተ ፡ መንግሥታቸውን ፡ ጥለው ፡ ኢየሩሳሌም ፡ ስለ ፡ ሄዱ ፡ የተገጠመ ።

ወ ፡ በመላ ፡ ሕይወታቸው ፡ እስከ ፡ ዕለተ ፡ ሞታቸው ፡ ድረስ ፡ ሕዝብ ፡ ሰ
ብሳቢ ፡ ድኻ ፡ ረጂ ፡ ጕዳይ ፡ ፈጻሚ ፡ ነበሩ ።

671 እንዴት ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ነው ፡ የሌለው ፡ እምነት ፤
—እውነት ፡ ሞቷል ፡ ብለው ፡ ይለኛል ፡ ሐሰት ።

ሠ ፡ መሞቱ ፡ መቀበሩ ፡ ርግጥ ፡ ነው ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ መለየቱ ፡ የታ
መነ ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ ብነግረው ፡ ይጠራጠራል ፤ ይህ ፡ ወሬ ፡ ሐሰት ፡
ነው ፡ ይለኛል ።

ወ ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ ጠፍቷል ፤ ርግጠኛነት ፡ ታጥቷል ፤ ከሰው ፡ አንደ
በት ፡ የሚወጣው ፡ ሐሰት ፡ ብቻ ፡ ሆኗል ፡ ብለው ፤ አላምንህም ፡ ይለ
ኛል ።

672 እንዴት ፡ ያለች ፡ ልጅ ፡ ናት ፡ የማታውቅ ፡ ይሉኝታ ፤
—ታስጨንቀኛለች ፡ እናት ፡ ይዛ ፡ ጠፍታ ።

ሠ ፡ ልጅ ፡ ከናቷ ፡ ጋራ ፡ ኰብልላብኝ ፡ ተቸግሬያለሁ ፤ የማደርገው ፡ ጠፍ
ቶብኛል ፤ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ሁለቱም ፡ በመጥፋታቸው ፡ ግራ ፡ ገብቶኛል።

ወ ፡ በወሊድ ፡ የናቷን ፡ ሕይወት ፡ አጥፍታ ፡ የሞተችው ፡ ሕፃን ፡ ታሳዝ
ነኛለች ፤ አንገሮቴን ፡ ትበላዋለች ።

673 እንዴት ፡ ይጠለቃል ፡ ካባ ፡ ቀሚሳቸው ፤
—የእቴጌ ፡ ዘመዶች ፡ ብቻው ፡ ራስ ፡ ናቸው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የእቴጌ ፡ ዘመዶች ፡ ራሳም ፡ ናቸው ፤ ጭንቅላታቸው ፡ ትልልቅ ፡
ነው ፤ ካባ ፡ ቀሚስ ፡ አያስገባም ፤ አያስጠልቅም ።

ወ ፡ የእቴጌ ፡ ዘመዶች ፡ ሁሉም ፡ ራሶች ፡ ናቸው ፤ ዘመዳሞቹ ፡ በሙሉ ፡
የራስነት ፡ ማዕርግ ፡ አግኝተዋል ፤ ከታላቅ ፡ ክብር ፡ ደርሰዋል ።

674 እንጀራ ፡ መጋገር ፡ ናርዶስ ፡ ታውቃለች ፤
—አብሶ ፡ ሐረጓ ፡ በጣም ፡ ታሣሣለች ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ናርዶስ ፡ አበዛነት ፡ ትችላለች ፤ ይልቁንም ፡ ሐረጓ ፡ (ሐረገ ፡ ወይን) ፡
እጅግ ፡ ታሳምራለች ፤ ይቀናበርላታል ፤ በሥሡ ፡ መጋገሩን ፡ ታውቅ
በታለች ።

ወ ፡ ናርዶስ ፡ ደመ ፡ ግቡ ፡ ናት ፤ በተለይ ፡ ሐረገ ፡ ወይን ፡ በጣም ፡ ታጓ
ጓለች ፤ ታሣሣለች ።

675 እንጀራ ፡ ተጋግሮ ፡ ቡሖ ፡ ዕቃው ፡ ባዶ ፡ ነው ፤
—የደጃች ፡ ትኩ ፡ ቤት ፡ መለቃለቁ ፡ ነው ።

ሠ ፡ በደጃች ፡ ትኩ ፡ ቤት ፡ ምንም ፡ ሊጥ ፡ የለም ፤ ተጋግሮ ፡ አልቋል ፤
ቡሖ ፡ ዕቃው ፡ ባዶውን ፡ ሆኖ ፡ በመታጠብ ፡ ላይ ፡ ነው ።

ወ ፡ የደጃች ፡ ትኩ ፡ ቤተ ፡ ሰቦችን ፡ ሞት ፡ አጠቃቸው ፤ ዘመዳሞች ፡ ተከ
ታትለው ፡ ሞቱ ፤ ዘር ፡ ሊያጡ ፡ ነው ።

676 እንጀራ ፡ አልፈልግም ፡ ምን ፡ ያደርግልኛል ፤
—ቈርጬ ፡ እሄዳለሁ ፡ ሥጋው ፡ ይበቃኛል ።

ሠ ፡ እንጀራ ፡ አልሻም ፤ ጠግቢያለሁ ፤ ሥጋ ፡ ባገኝ ፡ ግን ፡ የሚበቃኝን ፡ ያኽል ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ ሙዳ ፡ ቈርጬ ፡ እሄድ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ሥጋዊ ፡ ኑሮ ፡ ይበቃኛል ፤ ይህን ፡ ዓለም ፡ ትቼ ፡ የነፍሴን ፡ ነገር ፡ አጥብቄ ፡ ለመያዝ ፡ መንኜ ፡ እሄዳለሁ ።

677 እንጀራው ፡ ተጋግሮ ፡ ሞልቶ ፡ ከቤትህ ፡
—በምን ፡ ምክንያት ፡ ነው ፡ ውሃ ፡ የበላህ ።

ሠ ፡ እንጀራ ፡ ከቤትህ ፡ ሞልቶ ፡ አንተ ፡ ውሃ ፡ ተጐንጭተህ ፡ አንፎርሻ ፡ ጠጥተህ ፡ የዋልኸው ፡ ለምንድነው ።

ወ ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ የውሃ ፡ ሙላት ፡ ወሰደህ ፤ ጐርፍ ፡ ማዕበል ፡ አሰጠመህ ።

678 እንጀራው ፡ ተጋግሮ ፡ ወጡ ፡ ሳይቀርብልን ፡
—የት ፡ ሄደች ፡ ጣይቱ ፡ ሳታሳልፍልን ።

ሠ ፡ መሶብ ፡ ሳትሠራልን ፡ ማእድ ፡ ሳታቀርብልን ፡ ሳታስተናግደን ፡ አሳላፊዋ ፡ ወዴት ፡ ሄደች ።

ወ ፡ ራሳችንን ፡ ሳታስችለን ፡ ርስት ፡ ጕልት ፡ ሳትተክለን ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ምነው ፡ ሞተችብን ።

679 እንግዳ ፡ መጥቶብኝ ፡ አሁን ፡ ምን ፡ ልሆን ፡ ነው ፤
—ያንን ፡ ሽሮ ፡ ለሱ ፡ ቢሰጡልኝ ፡ ምነው ።

ሠ ፡ እንግዳ ፡ መጥቶብኝ ፡ የማቀርበው ፡ ቸግሮኛል ፤ እባክዎ ፡ ያንን ፡ ሽሮ ፡ ወጥ ፡ ይስጡልኝ ፡ አብልቼ ፡ ልስደደው ።

ወ ፡ ያንን ፡ ሰው ፡ ሽረው ፡ ሹመቱን ፡ ለወንድሜ ፡ ለእንግዳ ፡ ቢሰጡልኝ ፡ ምን ፡ ቸገራቸው ።

680 እንግዲህ ፡ ለምነው ፡ የጌታ ፡ ወዳጅ ፤
—ከውሃ ፡ ይሰጣል ፡ አስለምዶ ፡ ጠጅ ።

ሠ ፡ ጠጅ ፡ ሲሰጥ ፡ ኖሮ ፡ በመጨረሻው ፡ ውሃ ፡ የሚያጠጣ ፡ የጌታ ፡ ወዳጅ ፡ እንግዲህ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አላበጅም ።

ወ ፡ በክብር ፡ በማዕርግ ፡ አኑሮ ፡ በሥልጣን ፡ አሳድጎ ፤ እንደ ፡ ገና ፡ የቍልቍሊት ፡ ከነበረበት ፡ አውርዶ ፡ በግዞት ፡ የሚያስቀምጥ ፡ ጌታ ፡ ቢቀርስ ፡ ምን ፡ አለ ።

681 እንግዲህ ፡ መቃብር ፡ ጠንክረህ ፡ ተማር ፤
—ድጓ ፡ ተሸክሞ ፡ ገባልህ ፡ መምህር ።

ሠ ፡ የድጓ ፡ መምህር ፡ መጣልህ ፤ ጠንክረህ ፡ ተማር ፤ በርትተህ ፡ አንቀጹን ፡ አጥና ፤ አባባሉን ፡ ቀጽል ።

ወ ፡ መምህር ፤ ሞት ፡ የማይቀር ፡ ሆነና ፡ ሞተ ፤ ተቀበረ ።

682 እንግዲህ ፡ መዝራት ፡ ነው ፡ እኽሉን ፡ በያይነቱ ፤
—ዝናቡ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሞላ ፡ በመሬቱ ።

ሠ ፡ ዝናቡ ፡ አጥግቦ ፡ ጣለ ፤ በመሬቱ ፡ ላይ ፡ ትንጣለለ ፤ እንግዲህ ፡ ዘር ፡ መዝራት ፡ ነው ፤ አዝመራ ፡ መዠመር ፡ ነው ።

ወ ፡ «ዝናቡ» ፡ ሞቶ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወረደ ፤ ግባተ ፡ መሬት ፡ ተፈጸመ በት ።

683 እንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ልናገር ፡ ባዋጅ ፤
—የጥበቡ ፡ ሠሪ ፡ ጠቅል ፡ ነው ፡ ባለጅ ።

ሠ ፡ የጥበብ ፡ ኩታ ፡ የሚሠራ ፡ ጥሩ ፡ ሸማኔ ፡ የእጅ ፡ ዕውቀት ፡ ያለው ፡ ባለጅ ፡ ጠቅል ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ወ ፡ ዕውቀትን ፡ ጥበብን ፡ ያመጣልን ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ «ኃይለ ፡ ሥላሴ» ፡ ነው ፤ የሥልጣኔያችን ፡ የብልኅነታችን ፡ ምክንያት ፡ እሱ ፡ ነው ።

684 እንግዲህ ፡ አልመጣም ፡ ምን ፡ አደርጋለሁ ፤
—ደኅና ፡ ይሰንብቱ ፡ ልትወጡ ፡ ከሆንሁ ።

ሠ ፡ ይህን ፡ ቦታ ፡ መልቀቅዎና ፡ እደጋ ፡ መውጣትዎ ፡ ከሆነ ፡ ሁለተኛ ፡ አልመጣም ፤ ደኅና ፡ ይሁኑ ።

ወ ፡ ቅጠላቅጠል ፡ እየቀቀሉ ፡ የሚያበሉ ፡ የልት ፡ ወጥ ፡ የሚጋብዙ ፡ ከ ሆነ ፡ ዳግመኛ ፡ እቤትዎ ፡ አልደርስም ።

685 እንግዲህ ፡ አልደርስም ፡ ከገበዙ ፡ ደጅ ፤
—እኔ ፡ መጋቢ ፡ አለ ፡ ብዬ ፡ ነበር ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ የሚያበላ ፡ የሚያጠጣ ፡ ያለ ፡ መስሎኝ ፡ መጣሁ ፡ እንጂ ፤ እን ዲህ ፡ ድኻ ፡ ተመልካች ፡ አለመኖሩን ፡ ባውቅ ፡ ኖሮ ፡ እግሬንም ፡ አላ ነሣም ፡ ነበር ።

ወ ፡ እኔ ፡ የገዳሙ ፡ መጋቢ ፡ ያለ ፡ መስሎኝ ፡ ለመጠየቅ ፡ መጣሁ ፡ እንጂ ፤ እሱ ፡ መሞቱን ፡ ሰምቼ ፡ ብሆን ፡ ኖሮ ፡ እዚህ ፡ ገዳም ፡ አልመጣም ፡ ነበር ።

686 እንግዲህ ፡ አልደግምም ፡ ዳዊት ፡ ይበቃኛል ፤
—ንግግሩ ፡ ሁሉ ፡ ጸጸት ፡ ሆኖብኛል ።

ሠ ፡ በዳዊት ፡ መዝሙር ፡ ሁለተኛ ፡ አልጸልይም ፤ ቃሉ ፡ ንግግሩ ፡ ሐዘ ንን ፡ ጸጸትን ፡ በልብ ፡ ላይ ፡ ይቀርጻል ፤ የሰውን ፡ ከንቱነት ፡ ይገል ጻል ።

ወ ፡ «የዳዊትን» ፡ ነገር ፡ ዳግም ፡ አላነሣውም ፤ የነበረውን ፡ አሳብ ፡ ቁም ፡ ነገሩንና ፡ ምክሩን ፡ ሳስታውሰው ፡ ያሳዝነኛል ፤ የሱ ፡ ሞት ፡ እጅግ ፡ ያስለቅሰኛል ።

687 እንግዲህ ፡ ረዳት ፡ የት ፡ አገር ፡ አግኝቼ ፤
—እኖራለሁ ፡ እንጂ ፡ ካቡን ፡ ተጠግቼ ።

ሠ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ምንም ፡ ተስፋ ፡ ያጣሁ ፡ ከሆንሁ ፡ ካንድ ፡ ካብ ፡ ሥር ፡ ተጠግቼ ፡ ከታዛ ፡ ከዛኒጋባ ፡ ሕይወቴን ፡ አሳልፋለሁ ።

ወ ፡ እንግዲህ ፡ የሚረዳኝ ፡ ወገን ፡ አጋርና ፡ ጥግ ፡ አላገኘሁምና ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ አቡን ፡ ተጠግቼ ፡ እኖራለሁ ።

688 እንግዲህ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ ምን ፡ ያሳስበኛል ፤
—አዝመራዬ ፡ እንደሆን ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ተከቷል ።

ሠ ፡ ዘር ፡ ዘርቼ ፡ ጨርሻለሁ ፤ አዝመራዬን ፡ አጠናቅቂያለሁ ፤ ወደ ፡ ኋላ ፡ አልቀረሁም ።

ወ ፡ ልጄ ፡ «አዝመራ» ፡ እንደሆን ፡ ሞቷል ፤ ለየትኛው ፡ ዓለም ፡ ነው ፡ የማስበው ፡ የምጨነቀውና ፡ የምጠበበው ።

689 እንጠይቀው ፡ ወሬ ፡ መቅደላን ፡ እንደ ፡ ሰው ፤
—ያን ፡ የሰው ፡ አንበሳ ፡ ወዴት ፡ አደረሰው ።

ሠ ፡ ያንን ፡ የሰው ፡ ለማዳ ፡ አንበሳ ፡ የት ፡ ወሰደው ፤ ወዴት ፡ አደረሰው ።

ወ ፡ ጀግናው ፡ እንደ ፡ አንበሳ ፡ አስፈሪ ፡ የነበረው ፡ ቴዎድሮስ ፡ ከመቅደላ ፡ ወዴት ፡ ጠፋ ፤ የት ፡ ሄደ ።

690 ዕንጨቱ ፡ ተጓሮ ፡ ቋሚው ፡ እየኰራ ፡
—አለማገር ፡ ቀረች ፡ ቤቴ ፡ ተዠምራ ።

ሠ ፡ ቤቴ ፡ ሳትማገር ፡ በዥምር ፡ ቀረች ፤ ሳታልቅ ፡ በውጥን ፡ ተተወች ።

ወ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚገኝባት ፤ ዓለም ፡ የሚታይባት ፡ አገሬ ፡ ቀረች ፤ በጠላት ፡ ተወረረች ።

691 —ዕንጨት ፡ ሳይቆምበት ፡ ማዘን ፡ ሳይገባበት ፡
ባዶ ፡ ጭቃ ፡ ብቻ ፡ እንዴት ፡ ይሠራል ፡ ቤት ።

ሠ ፡ ቋሚ ፡ ሳይኖረው ፡ ማእዘን ፡ ሳይገባበት ፡ ጭቃ ፡ ብቻውን ፡ ምን ፡ ቤት ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ ማዘን ፡ መተከዝ ፡ ጾም ፡ ጸሎት ፡ ከሌለበት ፡ ቤት ፡ እንዴት ፡ ይጸናል፤ ከክፉ ፡ ነገር ፡ ይጠበቃል ።

692 እንጸድቃለን ፡ ብለን ፡ ቈርበን ፡ የነበረ ፡
—እሷም ፡ አፈረሰች ፡ እኔም ፡ ተውኩት ፡ ቀረ ።

ሠ ፡ እሷም ፡ ከኔ ፡ ሳትረጋ ፡ ቀረች ፤ ቍርባኑን ፡ አፈረሰች ፤ የሥጋ ፡ ወደሙን ፡ ሕግ ፡ አልጠበቀችም ።

ወ ፡ እሷም ፡ ዐፈር ፡ ሆነች ፤ ሞተች ፤ ተቀበረች ።

693 እኖራለሁ ፡ እንጂ ፡ ደጃፌን ፡ ዘግቼ ፤
—ምንም ፡ ቢቸግረኝ ፡ አልሄድም ፡ ከፍቼ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ቤቴን ፡ ክፍቱን ፡ ጥዬ ፡ አልሄድም ፤ በሩን ፡ መስኮቶቹን ፡ ሳልዘጋ ፡ ከቤቴ ፡ አልወጣም ፤ ክፉ ፡ ሆኜ ፡ አልሄድም ።

ወ ፡ ምንም ፡ ችግር ፡ ቢበዛብኝ ፡ ባጣ ፡ ብነጣ ፡ የፍቼን ፡ ከተማ ፡ ትቼ ፡ ወደ ፡ ውጭ ፡ አልሄድም ።

694 እኒህ ፡ ካህናቶች ፡ ይጓደዱበታል ፤
—ሰው ፡ ከሞተ ፡ ወዲያ ፡ እንዲያውም ፡ ይፈታል ።

ሠ ፡ እኘህ ፡ ካህናት ፡ ምን ፡ እንዲህ ፡ ያደርጋቸዋል ፤ የሞተ ፡ ሰው ፡ ክር
ስቲያን ፡ ከሆነ ፡ ገንዘብ ፡ ባይኖረውም ፡ መፍታት ፡ ይገባቸዋል ።

ወ ፡ ሰራዊት ፡ ቢሰበሰብ ፡ መሪ ፡ ከሞተ ፡ ጦር ፡ ድል ፡ ይሆናል ፤ ሰልፍ ፡
ይፈታል ።

695 እኛም ፡ አንለቅህ ፡ ዕወቀው ፡ ቍርጡን ፤
—ተወልወል ፡ ሳትወጣ ፡ ከሀገራችን ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አንለቅህም ፤ ቍርጡን ፡ ዕወቀው ፡ ትወለወላለህ ።

ወ ፡ ወልወል ፡ አገራችንን ፡ ካለቀቅህ ፡ ትወጋለህ ፡ ዕወቀው ።

696 እኛስ ፡ ሄደን ፡ ነበር ፡ ደጎና ፡ አገር ፡ መስሎን ፤
—ተመልሰን ፡ መጣን ፡ ጕጕት ፡ በዝቶብን ።

ሠ ፡ ሽኮኮና ፡ ጕጕት ፡ የበዛበት ፡ አገር ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ለመቈየት ፡ አልተቻለ
ንም ፤ ተመልሰን ፡ መጣን ።

ወ ፡ ባይሆንልን ፤ መጓጓቱ ፡ ደጅ ፡ ጥናቱ ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ማየቱ ፡ ቢሰለ
ቸን ፡ ሁሉንም ፡ ትተነው ፡ ወዳገራችን ፡ ተመለስን ።

697 እኛስ ፡ ማን ፡ ነበርን ፡ እናንተስ ፡ ማናችሁ ፤
—አውራውን ፡ ጐዳና ፡ የከለከላችሁ ። (ራስ ፡ ኀ ፡ ተ ፡ ሃ) ፡

ሠ ፡ ለምንድነው ፡ ጥርጊያውን ፡ መንገድ ፡ የምትከለክሉት ፤ ማለፊያ ፡
ማግደሚያውን ፡ የምትዘጉት ፡ የምታጥሩት ።

ወ ፡ ለምንድነው ፡ እኔን ፡ የሚያኽለውን ፡ ያገሩን ፡ አውራ ፡ እንዳላልፍ ፡
ያገዳችሁኝ ፤ እናንተስ ፡ ማን ፡ ሆናችሁና ፡ ነው ፡ ልትከለክሉኝ ፡ የደ
ፈራችሁት ።

698 እኛ ፡ በብረት ፡ ብር ፡ መጻፍ ፡ ስንገሥምር ፡
—ምነዋ ፡ መያዝህ ፡ ጎሩይ ፡ መቃ ፡ ብር ። (ጌ ፡ ዐ) ፡

ሠ ፡ እኛ ፡ እንኳ ፡ በብረት ፡ ብር ፡ ስንጽፍ ፡ ለምን ፡ አንተ ፡ የሸንበቆ ፡
ብር ፡ ያዝህ ፤ በመቃ ፡ መጻፍ ፡ ገሥመርህ ።

ወ ፡ ጎሩይ ፡ (ብላቴን ፡ ጌታ) ፡ ሞትክና ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወረድክን ፤
ያንተ ፡ ነገር ፡ እንዲሁ ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ።

699 እኛን ፡ ሲሉ ፡ መጥተው ፡ አትጨክኑባቸው ፤
—ማርካችሁ ፡ ገፉችሁ ፡ ባዶ ፡ አታስቀሯቸው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ያለ ፡ የሌለውን ፡ ዘርፉችሁ ፡ ወስዳችሁ ፡ ባዶ ፡ እጃቸውን ፡ አትተዋ
ቸው ።

ወ ፡ እኛን ፡ እንወጋቸዋለን ፡ እንገዛቸዋለን ፡ ብለው ፡ ከመጡ ፡ በምርኮ ፡
ብቻ ፡ ባድዋ ፡ ላይ ፡ ሳትወስኑ ፡ እንዳይተርፉ ፡ አድርጋችሁ ፡ ጨር
ሷቸው ።

700 እኛ ፡ አገር ፡ ተቀምጦ ፡ በክርስቲያን ፡ ስም ፡
—ዓሣ ፡ ማ ፡ ይበላል ፡ በሑዳዴ ፡ ጦም ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 929)፡ (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አርባ ፡ ጦም ፡ ሑዳዴን ፡ ዓሣ ፡ የሚመገብ ፡ ማንም ፡ የለ ፤ ሁሉም ፡ ጢሚ ፡ ነው ፤ ዓሣ ፡ መብላት ፡ ክልክል ፡ ነው ።

ወ ፡ በዐቢይ ፡ ጾም ፡ ውስጥ ፡ ያሣማ ፡ ሥጋን ፡ ይመገባል ፤ ክርስቲያንነቱ ፡ ቀርቷል ፤ ጾም ፡ መግደፍ ፡ የተገኘውን ፡ መብላት ፡ ሆኗል ።

701 እወርዳለሁ ፡ ቈላ ፡ አልውልም ፡ ከቤቴ ፤
—እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ተከፍቶ ፡ ማጀቴ ። (ን ፡ ሣ ፡ ሥ) ፡

ሠ ፡ ጓዳዬ ፡ ባዶ ፡ ሆኗል ፤ ምንም ፡ ነገር ፡ በቤቴ ፡ የለም ፤ ወደ ፡ ቈላ ፡ ወርጄ ፡ የሆነውን ፡ አመጣለሁ ፤ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ በችግር ፡ እኖራለሁ ።

ወ ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ማጀቴ ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ተጫውቶብኝ ፡ አልገዛም ፡ ብሎኝ ፡ ይኖራል ፤ ሄጄ ፡ አስገብሬው ፡ እመጣለሁ ።

702 ዕውሩ ፡ በመሪ ፡ አንካሳው ፡ በምርኵዝ ፡ የተከተለዎ ፡
—እኽል ፡ አይበቅልም ፡ ወይ ፡ ንጉሥ ፡ አገርዎ ።

ሠ ፡ አገርዎ ፡ እኽል ፡ አይሆንም ፡ ወይ ፤ የሚበላ ፡ የለም ፡ ወይ ፤ ሕዝብዎ ፡ በሙሉ ፡ ለምን ፡ አገሩን ፡ ጥሎ ፡ ወጣ ።

ወ ፡ ዕውሩና ፡ አንካሳው ፡ የተከተለዎ ፡ ለጦርነት ፡ ነው ፤ ወይስ ፡ ምግብ ፡ ፍለጋ ፡ ነው ።

703 እዚያ ፡ ማዶ ፡ ሆና ፡ ትጠራለች ፡ እናት ፤
—ና ፡ ብላ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላም ፡ ጕዳይ ፡ የላት ።

ሠ ፡ እቤትህ ፡ ና ፡ ማለቷ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ምንም ፡ የምሠራላት ፡ ነገር ፡ የለም ፤ የምፈጽምላት ፡ ጕዳይ ፡ አይኖርም ።

ወ ፡ ና ፡ ቍርስ ፡ አድርግ ፤ አፍህን ፡ አሻሽ ፤ ባዶ ፡ ሆድህን፡ አትንከራተት፤ ብላ ፡ ነው ፡ አሁን ፡ የምትጣራው ፤ ሌላ ፡ ምንም ፡ ጕዳይ ፡ የላትም ።

704 ዕዝራ ፡ በመሰንቆ ፡ ዳዊት ፡ በበገና ፡
—እግዜርም ፡ እንደ፡ ሰው ፡ ይወዳል ፡ ምስጋና ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ መመስገን ፡ የማይወድ ፡ የለም ፤ እግዜር ፡ እንኳ ፡ ምስጋና ፡ እንዲያቀርቡለት ፡ ይፈቅዳል ፤ በፍጥረቱ ፡ አፍ ፡ እንዲመሰገን ፡ ይሻል ።

ወ ፡ ምስጋና ፡ (ቀኛዝማች) ፡ በሰውም ፡ በእግዚአብሔርም ፡ ዘንድ ፡ የተወደደ ፡ ነው ፤ በሕዝብ ፡ ዘንድ ፡ መወደድ ፡ አለው ፤ ሁሉም ፡ ይፈቅዱታል ።

705 እየሮጠ ፡ ሄደ ፡ ጨርቁን ፡ እንጠልጥሎ ፤
—የምድር ፡ ግብር ፡ ተራ ፡ ደርሶብኛል ፡ ብሎ ።

ሠ ፡ የገባሩ ፡ መሬቴ ፡ ወር ፡ ተራ ፡ ደርሶብኛል ፡ ብሎ ፡ ቸኵሎ ፡ ሄደ ።

ወ ፡ «ወትገብእ ፡ ውስተ ፡ መሬት» ፡ ያለው ፡ ቃል ፡ በፋንታው ፡ ደርሶበት ፡ በሕፃንነቱ ፡ ሞተ ፤ ተቀበረ ።

706 እየበዛ ፡ ሄደ ፡ ዘንድሮስ ፡ በራቸው ፤
—እንግዲህ ፡ ንጉሡ ፡ ምን ፡ ራስ ፡ አላቸው ።

ሠ ፡ በራነታቸው ፡ እየጨመረ ፡ እየገፋ ፡ ሄደ ፤ ምንም ፡ ጠጉር ፡ አልቀራቸው ።

ወ ፡ የንጉሡ ፡ ራሶች ፡ መሳፍንቶችም ፡ በሙሉ ፡ ተከታትለው ፡ ሞቱ ፤ ንጉሡ ፡ ብቻቸውን ፡ ቀሩ ።

707 እዩልኝ ፡ ያንን ፡ ልጅ ፡ ጌጥ ፡ አልጠግብ ፡ ባይ ፤
—መርገፍ ፡ ጨመረበት ፡ በጥበቡ ፡ ላይ ።

ሠ ፡ ያ ፡ ልጅ ፡ ማጌጥ ፡ መሽቀርቀር ፡ ይወዳል ፤ አሁንም ፡ በጥበቡ ፡ ኩታ ፡ ላይ ፡ መርገፍ ፡ ደርቦበታል ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፤ ያንን ፡ ሁሉ ፡ ዕውቀት ፡ ይዞት ፡ ሞተ ፤ እንደ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ ተቀበረ ።

708 እዩልኝ ፡ አገሬን ፡ ሳልጥለው ፡ ሲጥለኝ ፤
—ብዙ ፡ ዘመኑ ፡ ነው ፡ ትግል ፡ ከዠመረኝ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 649) ፡

ሠ ፡ መታገል ፡ መፈታተን ፡ ከዠመረኝ ፡ አያሌ ፡ ዘመን ፡ ሆኖታል ፤ የሚከታተለኝ ፡ ከብዙ ፡ ቀን ፡ ዠምሮ ፡ ነው ።

ወ ፡ ብለፋ ፡ ብወጣ ፡ ብወርድ ፡ ሀብት ፡ አላገኝ ፤ አላልፍልኝ ፡ አለ ፤ እንግዲህ ፡ አገሬን ፡ ለቅቄ ፡ ወደ ፡ ሌላ ፡ ቦታ ፡ ልዙር ።

709 እዩት ፡ ተመልከቱት ፡ የባሌን ፡ ክፋቱን ፡
—አሁን ፡ ቃል ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ አይጠራም ፡ ወይ ፡ ሚስቱን ።

ሠ ፡ ቃል ፡ የገባ ፡ ተስፋ ፡ የሰጠ ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ የተናገረውን ፡ ይዘነጋል ፤ ቃሉን ፡ ያጥፋል ።

ወ ፡ እዩት ፡ የባሌን ፡ ክፋት ፤ የሰማኒያ ፡ የቃል ፡ ኪዳን ፡ ሚስቱን ፡ አያስታውሰኝም ፤ በሞት ፡ አያስከትለኝም ፤ እንደ ፡ ፈቀደው ፡ ጥሎኝ ፡ ይሄዳል ።

710 እያለለት ፡ መልኬ ፡ ካንገቴ ፡ በላይ ፡
—እጅ ፡ እጄን ፡ ያየኛል ፡ ዓለም ፡ አታላይ ።

ሠ ፡ ዋሾው ፡ ዓለም ፡ ሊታይ ፡ የሚገባውን ፡ ፊቴን ፡ አንገቴን ፡ ትቶ ፡ እጄን ፡ ይመለከተዋል ።

ወ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የገንዘብን ፡ ኀይል ፡ ይጠይቃል ፤ በያለበት ፡ ገንዘብ ፡ ገንዘብ ፡ ነው ።

711 እያሉ ፡ ካህናቱ ፡ ያርባ ፡ አራቱ ፡ ደብር ፡
—እንዴት ፡ ያለፍታት ፡ ተቀበረ ፡ ጐንደር ።

ሠ ፡ ሰውየው ፡ ጸሎት ፡ ሳይደርስለት ፡ እግዜር ፡ ይፍታህ ፡ ሳይባል ፡ እጐንደር ፡ ላይ ፡ ተቀበረ ።

ወ ፡ ጐንደርን ፡ ያኽል ፡ አገር ፡ እንዴት ፡ ሆኖ ፡ ድል ፡ ይመታ ፤ በጠላት ፡ ይፈታ ፤ እንደማያገግም ፡ ሆኖ ፡ ይጥፋ ።

712 እያመሰገነ ፡ ደጃዝማች ፡ ካሳን ፡
—ጋላ ፡ ባባ ፡ ሄደ ፡ ሊገባ ፡ አገሩን ።

ሠ ፡ ጋላ ፡ ሆድ ፡ ባሰው ፤ በትንሽ ፡ በትልቁ ፡ ነገር ፡ እየባባ ፡ አገሩ ፡ ሊመለስ ፡ ነው ፤ አብሮ ፡ መኖር ፡ አልሆነለትም ፤ ኩርፍተኛ ፡ ሆነ ።
ወ ፡ ባባ ፡ የተባለው ፡ ጋላ ፡ ደጃዝማች ፡ ካሳን ፡ ፈራ ፤ አልመከት ፡ አለ ፤ ገበረ ።

713 እያነጋገረኝ ፡ ቢጠይቀኝ ፡ ወሬ ፡
—አላውቅም ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ አለመናገሬ ።

ሠ ፡ የማልናገረውና ፡ የማላወራው ፡ የማውቀው ፡ ነገር ፡ ባይኖር ፡ ነው ።
ወ ፡ አፈን ፡ ዘግቼ ፡ ክፉ ፡ በጎ ፡ ሳልመልስ ፡ የምኖረው ፡ በቅም ፡ በማጣቴ ፡ ኀይል ፡ ባለማግኘቴ ፡ ነው ።

714 እያየን ፡ ያለፍነው ፡ ቈርቈሮ ፡ ከዳን ፡ ነው ፤
—ወደ ፡ ፊትስ ፡ ያለው ፡ ያ ፡ ሣሩ ፡ የማነው ።

ሠ ፡ እፊታችን ፡ ያለው ፡ የሣር ፡ ከዳን ፡ ቤት ፡ የማነው ፡ ያን ፡ ደግሞ ፡ የሠራው ፡ ማን ፡ ይሆን ።
ወ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚመጣውን ፡ መከራና ፡ ሥቃይ ፡ አሳር ፡ ተቀባዩ ፡ ማነው ።

715 እጅግም ፡ ሳይበዛ ፡ ድኻ ፡ ሳይበድሉ ፡
—ኩርቶ ፡ ማደር ፡ ነበር ፡ ራስን ፡ ሳይጥሉ ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ሰውነትን ፡ ሳያጕሳቍሉ ፡ አልባሌ ፡ ሳይመስሉ ፡ ራስን ፡ ነቃ ፡ አድርጎ ፡ መኖር ፡ ነበር ።
ወ ፡ ራስን ፡ ሳይክዱ ፡ እምነቱ ፡ ቢስ ፡ ሳይሆኑ ፡ መገኘት ፡ ነበር ፤ ታማኝነትን ፡ ሳያጠፉ ፡ ኩርቶ ፡ መኖር ፡ ነበር ።

716 እጅግ ፡ ሥራ ፡ ዐዋቂ ፡ ትናንት ፡ ተቀበረች ፡
—መድኀኒቱን ፡ ምሳ ፡ ታበላኝ ፡ ነበረች ። (ዐ፤ ፡ ቴ) ፡

ሠ ፡ አብነቱን ፡ መድኀኒቱን ፡ ቈፍራ ፡ ታመጣልኝ ፡ ነበር ።
ወ ፡ የረኃብ ፡ መድኀኒት ፡ የድካም ፡ ማደሻ ፡ የሆነውን ፡ ምግብ ፡ በጊዜ ፡ ትሰጠኝ ፡ ነበር ።

717 እጅግ ፡ ቢመሰገን ፡ የሥራህ ፡ እርምጃ ፡
—ዛሬስ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ አወጣህ ፡ መሄጃ ። (1) (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ በባሕር ፡ ውስጥ ፡ መንገድ ፡ አወጣህ ፤ አልክ ፡ አልክና ፡ በውሃ ፡ ውስጥ ፡ ለውስጥ ፡ ትሄድ ፡ ዠመር ።
ወ ፡ በርትተህ ፡ ከባሕር ፡ ውስጥ ፡ ሰጥሞ ፡ የነበረውን ፡ ጀልባ ፡ አወጣህ ፡ መርከቡ ፡ ያለአገልግሎት ፡ አልቀረም ።

(1) ራስ ፡ እንዳርጋቸው ፡ መሳይ ፡ ጐንደር ፡ በነበሩበት ፡ ጊዜ ፡ በጣና ፡ ባሕር ፡ ውስጥ ፡ ጠላቶች ፡ (ጣሊያኖች) ፡ አስጥመውት ፡ የነበረውን ፡ ጀልባ ፡ ሲያስወጡ ፡ የተደረሰ ።

718 እጅግ ፡ ተታለዋል ፡ ዘመዶቿ ፡ ሁሉ ፡
—ሲያወሩ ፡ ሰማሁኝ ፡ ሞታለች ፡ እያሉ ።

ሠ ፡ ዘመዶቿ ፡ እውነት ፡ ሳይሆን ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለይታለች ፡ ሞታለች ፡ ተቀብራለች ፡ እያሉ ፡ ሲናገሩ ፡ ሰምቻለሁ ።

ወ ፡ ሞታ ፡ ተቀብራ ፡ ሳለች ፡ በሕይወት ፡ እንዳለች ፡ አድርገው ፡ ሲናገሩ ፡ ሰማኋቸው ።

719 እገዛለሁ ፡ ብሎ ፡ ተስማምቶ ፡ ነበረ ፤
—መልካም ፡ በቅሎ ፡ ልጇ ፡ ሳይቀመጥ ፡ ቀረ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ልጇ ፡ ጥሩ ፡ ሠጋር ፡ በቅሎ ፡ ሳያገኝ ፡ ቀረ ፤ የጨዋ ፡ ደንብ ፡ ሳይደርሰው ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አለ ።

ወ ፡ ልጇ ፡ በመልካም ፡ አድጎ ፡ ተስፋ ፡ ሲደረግበት ፡ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ ሳይደርስ ፡ በከንቱ ፡ ቀረ ።

720 እግረኛ ፡ እንዳይሆን ፡ ይኸ ፡ ውጋዴን ፡
ጊዜው ፡ ሳያልፍበት ፡ በደጉ ፡ ዘመን ፡
—ከሕግ ፡ ቤት ፡ ገብቶ ፡ ምነው ፡ ቢወሰን ። (ብ ፡ መ ፡ ሐ ፡ ወ ፡ ቂ) ፡

ሠ ፡ ቃል ፡ ቢያስር ፡ የሕግ ፡ ሚስት ፡ ቢያጭ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ መንዘልዘሉ ፡ ቢቀርበት ፡ አይከፋም ።

ወ ፡ የውጋዴ ፡ የወሰን ፡ ጉዳይ ፡ አሁኑኑ ፡ ቢያልቅ ፡ ድንበሩ ፡ በቶሎ ፡ ቢወሰን ፡ ደግ ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ ነገር ፡ ውሎ ፡ ባያድር ፡ ይሻላል ።

721 እግረኞች ፡ በፍጥነት ፡ ሄዱ ፡ ገሠገሡ ፤
—ከጐንደር ፡ ለጋይንት ፡ በዝሁር ፡ ደረሱ ።

ሠ ፡ ከጐንደር ፡ የተነሡት ፡ እግረኞች ፡ «ዝሁር» ፡ በሚባለው ፡ አገር ፡ አቋርጠው ፡ ጋይንት ፡ ገቡ ።

ወ ፡ እግረኞች ፡ ገሥግሠው ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ ሳይፈጅባቸው ፡ በዚሁ ፡ ወር ፡ ከጐንደር ፡ ጋይንት ፡ ደረሱ ።

722 እግራቸው ፡ አንካሳ ፡ በቅሏቸው ፡ ሠጋር ፡
—አለማታ ፡ አይመጡም ፡ ምንም ፡ ቢቸግር ።

ሠ ፡ በጊዜ ፡ አይገቡም ፤ ካልመሸ ፡ ካልጨለመ ፡ ቤታቸውን ፡ አያስታውሱትም ።

ወ ፡ ከቶ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ለደግ ፡ ነገር ፡ አይመጡም ፤ አደጋ ፡ ለመጣል ፡ ሰላም ፡ ለመንሣት ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ።

723 እግርና ፡ እጅዋ ፡ ሲያምር ፡ የዚያች ፡ የወጣት ፡
—ተሸፍኖ ፡ ቀረ ፡ ዐፈሩ ፡ ዋጣት ።

ሠ ፡ የሚያምረው ፡ እጅ ፡ እግሯ ፡ ዐፈር ፡ ተጭኖት ፡ ዐቧራ ፡ አልብሶት ፡ አይታይም ።

ወ ፡ ያን ፡ መሳይ ፡ ጣቷን ፡ ዐፈር ፡ በላው ፤ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ እንዳልሆነ ፡ ሆነ ።

724 እግዚአብሔር ፡ ሲጣላኝ ፡ እግዜር ፡ ሲቈጣኝ ፡
—ዲያቆን ፡ ልጅ ፡ ነበረኝ ፡ አሳጣኝ ፡ አሳጣኝ ።

ሠ ፡ ቤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ የሚያገለግል ፡ ማጠንት ፡ የሚያሳጥን ፡ ጸሎተ ፡ ዕጣን ፡ የሚያደርስ ፡ ዲያቆን ፡ ልጅ ፡ ነበረኝ ።

ወ ፡ አንድ ፡ ዲያቆን ፡ ልጅ ፡ ነበረኝ ፤ ሞት ፡ ነጠቀኝ ፤ ፈጣሪዬ ፡ አሳይቶ ፡ ነሣኝ ።

725 እግዚአብሔርን ፡ በጧት ፡ ፈልጌ ፡ አገኘሁት ፤
—ማታ ፡ እመጣለሁ ፡ ቢል ፡ አጥብቄ ፡ ፈራሁት ።

ሠ ፡ ሲመሽ ፡ እመጣለሁ ፤ ማታ ፡ እጐበኝሃለሁ ፡ ቢለኝ ፤ ለምን ፡ ፈለገኝ ፡ በማለት ፡ ፈራሁት ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ መቅሠፍት ፡ አመጣለሁ ፡ መዓት ፡ አወርዳለሁ ፡ ቢል ፡ እጅግ ፡ ፈራሁ ፤ ደነገጥሁ ።

726 እግዚአብሔር ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ብፈልግ ፡ አጣሁት ፤
—ንገሩልኝ ፡ ሰዎች ፡ ቀን ፡ ያገኛችሁት ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 440) ፡

ሠ ፡ በብርሃን ፡ ሲሄድ ፡ ያገኛችሁት ፡ ድንገት ፡ ያጋጠማችሁ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፤ ይፈልግህ ፡ ነበር ፡ ብላችሁ ፡ ንገሩልኝ ።

ወ ፡ ዘመን ፡ ያነሣችሁ ፡ ሥልጣን ፡ ያገኛችሁ ፡ ጊዜ ፡ ያመቻችሁ ፡ ሰዎች ፡ አማልዱኝ ፤ ጕዳቴን ፡ ችግሬን ፡ ለበላይ ፡ አሳስቡልኝ ።

727 እግዚአብሔር ፡ ከዚያ ፡ ላይ ፡ በስንት ፡ ያሳርሳል ፤
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ ቤት ፡ ዘር ፡ ያመላልሳል ።

ሠ ፡ እዚያ ፡ ላይ ፡ ያለው ፡ ገበሬ ፡ በስንት ፡ ጥማድ ፡ ቢያሳርስ ፡ ነው ፡ እን ዲህ ፡ ዐሥር ፡ ጊዜ ፡ ዘር ፡ የሚያመላልሰው ፤ ነጋ ፡ ጠባ ፡ የዘር ፡ እኽል፡ የሚወስደው ።

ወ ፡ የዚህን ፡ ቤት ፡ ሰዎች ፡ ሞት ፡ ያጠቃቸዋል ፤ በየጊዜው ፡ ሐዘን ፡ ስለ ሚያገኛቸው ፡ ዘራቸው ፡ ሣሣብን ።

728 እግዜርና ፡ ንጉሥ ፡ ተጣልተው ፡ ቆመው ፡
ቅዱስ ፡ ሚካኤልን ፡ ዳኛ ፡ አስቀምጠው ፡

እግዜር ፡ በግራ ፡ ነው ፡ ንጉሡ ፡ በቀኝ ፤
—በል ፡ ፍጅና ፡ ስጠኝ ፡ ሲለው ፡ ሰማሁኝ ። (1)

ሠ ፡ በል ፡ እንግዲህ ፡ በፋንታህ ፡ በፍጆታህ ፡ ተናገርና ፡ ተራ ፡ ልቀቅልኝ ፡ አናግረኝ ፡ (የሙግት ፡ ሥነ ፡ ሥርዐት) ፡ ሲል ፡ ሰማሁት ።

ወ ፡ በደለኛውንና ፡ ነፍሰ ፡ ገዳዩን ፡ በሥጋ ፡ ቅጣት ፡ እየገደልክ ፡ እኔ ፡ በነፍሱ ፡ እንድቀጣው ፡ ላክልኝ ፡ ሲለው ፡ ሰምቻለሁ ።

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ «ምጽራሐ» ፡ ከሚባል ፡ ደሴት ፡ ገብተው ፡ ሴት ፡ ወንዱን ፡ ሕፃን ፡ ሽማግሌውን ፡ በሙሉ ፡ ስለ ፡ ፈጁት ፡ የበጌምድር ፡ ሴት ፡ በዚያ ፡ ስላለቁት ፡ ዘ መዶቿ ፡ ያለቀሰችው ።

729 እጠጣውም ፡ አይደል ፡ ጠጅ ፡ አምጡ ፡ ማለቴ ፤
——ሽታው ፡ ቢጣፍጠኝ ፡ እረጬው ፡ ለቤቴ ። (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ ጠጅ ፡ የለመንኩት ፡ ልጠጣው ፡ አይደለም ፡ ለሽታ ፡ ለመዐዛ ፡ ያ
ሽል ፡ ቤቴን ፡ ለመርጨት ፡ ነው ፡ እንጂ ።

ወ ፡ እባካችሁ ፡ ቸግሮኛል ፤ ለቤቴ ፡ የሚሆን ፡ ጨው ፡ በርበሬ ፡ ስጡኝ ፤
ጒርሻ ፡ ስጡኝ ፤ ዳርጉኝ ።

730 እጭ ፡ እጬን ፡ (ዕጭ ፡ ዕጬን) ፡ ይተዉት ፡ ይክረም ፡ አይሞኙ ፤
——ተከዳ ፡ ነውና ፡ ማሩን ፡ የሚያገኙ ።

ሠ ፡ ማር ፡ የሚገኘው ፡ ከዳ ፡ ከያዘ ፡ ዕጭ ፡ ካዋለ ፡ በኋላ ፡ ነው ።

ወ ፡ ይቅርታን ፡ የሚጠይቅዎ ፡ ምሕረትን ፡ የሚለምንዎ ፤ በዳይና ፡ ከዳ
ተኛ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

731 እረ ፡ መሽቷል ፡ መሽቷል ፡ ጨልሟል ፡ ጊዜው ፤
——ስለ ፡ ምነው ፡ በሩ ፡ የተከፈተው ።

ሠ ፡ በሩ ፡ ያልተዘጋው ፡ ደጃፉ ፡ ክፍቱን ፡ የሆነው ፡ ለምንድነው ፤ መለስ ፡
ብታደርጉት ፡ ምን ፡ ነበረ ።

ወ ፡ ስለ ፡ እግዚአብሔር ፡ እያልኩ ፡ ስለምን ፡ ነው ፡ በሩ ፡ የተከፈተው ።

732 እረ ፡ ስለ ፡ ምነው ፡ ገለባ ፡ እምትገዙ ፡
——ያ ፡ ሣር ፡ እንደሆነ ፡ ይበቃል ፡ ለብዙ ።

ሠ ፡ ያለው ፡ ሣር ፡ ለብዙ ፡ ከብት ፡ ይበቃል ፤ አያሌ ፡ ጊዜ ፡ ያበላል ፤ ለ
ምን ፡ ገለባ ፡ ትገዛላችሁ ።

ወ ፡ አሳራችን ፡ በዝቷል ፤ መከራው ፡ አላልቅም ፡ አለን ፤ ምን ፡ ማድረግ ፡
ይበጀናል ።

733 እረ ፡ ነጋ ፡ ነጋ ፡ እሜቴ ፡ መነን ፤
——መስኮቱን ፡ ክፈቺው ፡ እዩት ፡ ጣይቱን ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ሌሊቱ ፡ ነግቷል ፤ መስኮቱን ፡ ከፍተሽ ፡ መጋረጃውን ፡ ገልጠሽ ፡
እስቲ ፡ ጨረሯን ፡ እዩት ።

ወ ፡ እቴጌ ፡ መነን ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ የነበራትን ፡ ያስተዳደር ፡ ዘዴና ፡ የፖ
ለቲካ ፡ አመራር ፡ መመልከት ፡ ይጠቅምሻል ።

734 እረ ፡ አብስሉ ፡ በላኝ ፡ ከፉ ፡ ነው ፡ ውሻችሁ ፤
——ሐይ ፡ አትሉትም ፡ ወይ ፡ ምነዋ ፡ እያላችሁ ።

ሠ ፡ ውሻችሁ ፡ ክፉኛ ፡ ነከሰኝ ፡ በጣም ፡ ጐዳኝ ።

ወ ፡ ራብ ፡ ጸናብኝ ፡ ሊገለኝ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ቆማችሁ ፡ እያያችሁ ፡ ውሻችሁ ፡ ሲነክሰኝ ፡ለምን ፡ ዝም ፡ ትላላችሁ ?

ወ ፡ እህል ፡ እያላችሁ ፡ ጠኔ ፡ ሲገለኝ ፡ ለምን ፡ ትነፍጉኛላችሁ ።

735 እረ ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ የት ፡ ነው ፡ አገራችሁ ፤
—በማፈር ፡ በማፈር ፡ ትጫወታላችሁ ።

ሠ ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ለምን ፡ በመተፋፈር ፡ በመሰቀቅ ፡ ትጫወታላችሁ ።
ወ ፡ እናንተም ፡ እነሱም ፡ ሖኞች ፡ ስትሆኑ ፡ ለምን ፡ ዐፈር ፡ በሚሆነው ፡ በሰው ፡ ትጫወታላችሁ ።

736 እረ ፡ እሜት ፡ አበባ ፡ ሞኝ ፡ ናት ፡ ተላላ ፤
—እንግዳ ፡ ተቀባይ ፡ ዐፈር ፡ ልሁን ፡ ብላ ።

ሠ ፡ በማዘን ፡ በመራራት ፡ እንግዳን ፡ ትቀበል ፡ ነበር ፤ በሞቱ ፡ ይህችን ፡ ብላ ፡ ይህችን ፡ ጕረሥ ፡ እያለች ፡ እጥብቃ ፡ ያገኘችውን ፡ ሁሉ ፡ ትጋብዝ ፡ ነበር ።
ወ ፡ ዐፈር ፡ ለመሆን ፡ ለመፍረስ ፡ ለመበስበስ ፡ ሞተች ፤ ወደ ፡ መቃብር ፡ ገባች ።

737 እረ ፡ እናንተ ፡ ሆዬ ፡ ከብት ፡ ተወደደ ፤
—እዩት ፡ ይህን ፡ ጕብል ፡ ባጭር ፡ በቅሎ ፡ ሄደ ።

ሠ ፡ አህያ ፡ በምታኽል ፡ በድንክ ፡ በቅሎ ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ የሚሄደውን ፡ ልጅ ፡ ተመልከቱት ፤ ይህችን ፡ የሚነው ፡ እንዴት ፡ ከብት ፡ ቢወድ ፡ ነው ።
ወ ፡ ይህ ፡ ልጅ ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ ሳይበቃ ፡ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ ሳይደርስ ፡ በወጣትነቱ ፡ ተቀጨ ፤ አሳዛኝ ፡ ሞት ፡ ሞተ ።

738 ከሄዱበት ፡ አገር ፡ በደኅና ፡ ያምጣዎ ፤
—ለሣቅ ፡ ለደስታ ፡ ለጥርስ ፡ አለሁዎ ። (ይ ፡ በ) ፤

ሠ ፡ ከሚሄዱበት ፡ በሰላም ፡ ይመልስዎት ፤ ለሣቅ ፡ ለደስታ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያብቃን ፤ ከፋዎን ፡ አያስማን ።
ወ ፡ ርስዎ ፡ በደስታ ፡ ይምጡ ፡ እንጂ ፡ የዝናን ፡ ጥርስ ፡ አበረክትልዎታለሁ ፤ መታሰቢያ ፡ እጅ ፡ መንሻ ፡ አቀርብልዎታለሁ ።

739 ከልፍኝ ፡ አስወጥተው ፡ እዳስ ፡ አኑረው ፡
—ቅራሪውን ፡ ሰጡኝ ፡ ጠላነው ፡ ብለው ።

ሠ ፡ ውሃ ፡ ያልገባበት ፡ አሁን ፡ የተከፈተ ፡ ጠላ ፡ ነው ፡ ብለው ፡ እኸል ፡ ውሃ ፡ የማይል ፡ ቅራሪ ፡ ሰጡኝ ።
ወ ፡ ጥላቻውን ፡ ለመግለጽ ፡ ቅያሚያቸውን ፡ ለማስረዳት ፡ ብለው ፡ ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ድግስ ፡ ቅራሪ ፡ ሰጡኝ ።

740 ከመሸ ፡ ተነሣሁ ፡ ከተፈታ ፡ በሬ ፡
—እደርስም ፡ አይመስለኝ ፡ እንግዲህ ፡ አገሬ ።

ሠ ፡ ጊዜ ፡ መሽቷል ፤ ፀሓይ ፡ ተሸቈልቍሏል ፤ አሁን ፡ ብሄድ ፡ እቤቴ ፡ አልደርስም ፤ ዐጕል ፡ ቦታ ፡ እድራለሁ ።
ወ ፡ ሁለተኛ ፡ አገሬን ፡ አልረግጣትም ፤ እተወለድኩበት ፡ ቦታ ፡ አልደርስም ፤ በሰው ፡ አገር ፡ እየተንከራተትኩ ፡ እኖራለሁ ።

741 ከማያውቀው ፡ አገር ፡ ጊዜ ፡ መሽቶበት ፡
—ብቻውን ፡ አደረ ፡ እመቃብር ፡ ቤት ።

ሠ ፡ ዐጕል ፡ ቦታ ፡ መሽቶበት ፡ ደጅ ፡ ሰላም ፡ አደረ ፤ ሌሊቱን ፡ በመቃብር ፡ ቤት ፡ አሳለፈው ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ አዬ ፡ ሰው ፡ መሆን ፤ ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ሰራዊት ፡ ብቻውን ፡ በሞት ፡ ሄደ ፤ እመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፤ ዐፈር ፡ ተመለሰበት ።

742 ከሣር ፡ ከቅጠሉ ፡ ይበዛል ፡ ዐመሌ ፤
—ይህን ፡ ሁሉ ፡ ችሎ ፡ ይኖር ፡ ነበር ፡ ባሌ ።

ሠ ፡ ያ.ጉ ፡ ባሌ ፡ ከፋውን ፡ ዐመሌን ፡ ታግሦ ፡ ይኖር ፡ ነበር ፤ በመጥፎ ፡ ባሕርዬ ፡ አይመረረኝም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ባለቤቴ ፡ ኑሮው ፡ ባሌ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ነበር ።

743 ከሥጋው ፡ ሳልበላ ፡ ተጠይፌ ፡ ደሙን ፡
—ማን ፡ ይችለው ፡ ይሆን ፡ የላይ ፡ ቤት ፡ ራቡን ።

ሠ ፡ እዚያ ፡ ላይ ፡ ሰፈር ፡ ያሉ ፡ ሰዎች ፡ እኽል ፡ አያቀምሱም ፤ ላልበላ ፡ ላልጠጣ ፡ ሄጄ ፡ ዛሬ ፡ ራቡን ፡ እንዴት ፡ እችለው ፡ ይሆን ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ ወደሙን ፡ ሳልቀበል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ በንስሐ ፡ ሳልመለስ ፡ የሞትኩ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ የሰማይ ፡ ቤቱን ፡ ሥቃይና ፡ ኵነኔ ፡ እንዴት ፡ እችለው ፡ ይሆን ።

744 ከሥጋው ፡ ሳልበላ ፡ ከደሙ ፡ ሳልጠጣ ፡
—በፊት ፡ ተቀድሞ ፡ ያሞት ፡ እንዴት ፡ ይምጣ ።

ሠ ፡ የሚበላው ፡ ሥጋ ፡ ሳይቀርብ ፡ ማጣፈጫው ፡ ሐሞት ፡ ለምን ፡ መጣ ።

ወ ፡ ሥጋ ፡ ወደሙን ፡ ሳልቀበል ፡ ዕለተ ፡ ሞት ፡ ቢደርስብኝ ፡ ምን ፡ እሆን ፡ ይሆን ።

745 ከሰል ፡ የሚሆኑ ፡ ብዙ ፡ ዕንጨቶች ፡ ሳሉ ፡
—ዝግባ ፡ ለምንድነው ፡ ይቈረጥ ፡ የሚሉ ። (ዮ ፡ ን)፡

ሠ ፡ ከሰል ፡ የሚሆን ፡ ሌላ ፡ ዕንጨት ፡ እያለ ፡ ለምንድነው ፡ ዝግባ ፡ እንዲቈረጥ ፡ የሚያዙት ።

ወ ፡ ሕዝብን ፡ ሳይበድል ፡ ሳያንገላታ ፡ በለስላሳ ፡ ሁናቴ ፡ አገር ፡ የሚያስተዳድረውን ፡ ለምን ፡ በበላዩ ፡ ቈራጭ ፡ የሆነ ፡ ሾሙበት ።

746 ከሰማይ ፡ ዝቅ ፡ አርጎ ፡ ከምድር ፡ ከፍ ፡ አርጎ ፡ አሠርቶ ፡ ቤቱን ፡
—በመስኮት ፡ አግብቶ ፡ ይሞቃል ፡ ጣይቱን ።

ሠ ፡ መስኮቱን ፡ ከፍቶ ፡ የጧት ፡ ፀሐይ ፡ ይቀበላል ፤ የቤቱ ፡ አሠራር ፡ ፀሐይ ፡ ለማግኘት ፡ የተመቸ ፡ ነው ።

ወ ፡ ብልኀና ፡ አስተዋይ ፡ የሆነችውን ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱን ፡ አግብቶ ፡ ቦታ ድላ ፡ በደስታ ፡ ይኖራል ።

747 ከሰማንያ ፡ ቀርቶ ፡ ዋስ ፡ ከማሳገት ፡
—ከዳኛው ፡ ጋር ፡ ነበር ፡ አብሮ ፡ መንሣት ። (ቀኛ ፡ ጎ ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ ቸኰሎ ፡ ከችሎት ፡ ሄደ ፤ ዋስ ፡ ከማሳገት ፡ ከዳኛውና ፡ ከወንበሩ ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ መንሣት ፡ ነበር ።

ወ ፡ ንጉሡ ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ውርደት ፡ ከመቀበል ፡ ከዳኛው ፡ ምኒልክ ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ መሞት ፡ የተሻለ ፡ ነበር ።

748 ከሴቶቹ ፡ ሁሉ ፡ ኰሩ ፡ ነበረች ፤
—ዘንድሮ ፡ ምን ፡ ሆነች ፡ ራሷን ፡ ጣለች ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ እንደሷ ፡ ሰውነትን ፡ የሚጠብቅ ፡ አልነበረም ፤ የሆነችውን ፡ አላውቅም ፤ ዘንድሮ ፡ ራሷን ፡ አጐሳቊላለች ፤ አይመስሉ ፡ መስላለች ።

ወ ፡ ዘንድሮ ፡ በጣም ፡ ተጐዳች ፤ ራስ ፡ ሞቱባት ፤ ደጋፊዋን ፡ አጣች ።

749 ከሸዋ ፡ ከትግሬ ፡ ቀለብ ፡ ብለምንህ ፡
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ ተከፉ ፡ ለምን ፡ ትለኛለህ ።

ሠ ፡ የእኽል ፡ አበል ፡ ከሸዋ ፡ ተትግሬ ፡ እንድትሰጠኝ ፡ ብጠይቅህ ፡ ከፋ ፡ ካለው ፡ መሬትህ ፡ ታዝልኛለህ ፤ አንዳንድ ፡ ጊዜ ፡ እንኳ ፡ ከቅርቡ ፡ ቦታ ፡ አትሰጠኝምን ።

ወ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እንድበደል ፡ እንድቀየም ፡ ሆድ ፡ እንዲብሰኝ ፡ ለምን ፡ ታደርጋለህ ፤ ለምን ፡ እንደዚህ ፡ አድርገህ ፡ ታስከፋኛለህ ።

750 ከበሩ ፡ ላይ ፡ ቆሜ ፡ እኔ ፡ አየሁ ፡ ያለውን ፤
—የክንፉ ፡ አዳም ፡ ፈረስ ፡ ያልፍ ፡ ይመስል ፡ አሁን ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ የክንፉ ፡ አዳም ፡ ፈረስ ፡ አሁን ፡ የሚያልፍ ፡ መስሎኝ ፡ ቆሜ ፡ እጠብቃለሁ ፤ እሱን ፡ ለመመልከት ፡ ተመኝቻለሁ ።

ወ ፡ የክንፉ ፡ አዳም ፡ ፈረስ ፡ አንዱ ፡ እልፍ ፡ መስሎ ፡ ሲሄድ ፡ ሲያልፍ ፡ አየሁት ።

751 ከበሮ ፡ መምታቱን ፡ ሰዉ ፡ ሲያሳምር ፡
—ንጉሡ ፡ ጽናጽል ፡ አያውቅም ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ከበሮ ፡ በሚገባ ፡ ቢመታ ፡ ንጉሡ ፡ ጸናጽል ፡ መጣሉን ፡ አያውቅበትም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ምንም ፡ ሰባቂ ፡ ቢያዋሽክ ፤ አሉባልተኛ ፡ ቢበዛ ፡ ንጉሡ ፡ የመረረ ፡ ጠብ ፡ አያደርጉም ፡ ነበር ።

752 ከባሕር ፡ ዳር ፡ ሆኜ ፡ ብጠቅሰው ፡ ብጠቅሰው ፡
—ወዲያው ፡ ዘቅጦ ፡ ቀረ ፡ ይወጣል ፡ ያልኩት ፡ ሰው ። (ሑ ፡ ጂ) ፡

ሠ ፡ ከባሕር ፡ ይወጣል ፡ ብዬ ፡ ስጠባበቀው ፡ ወዲያው ፡ ሰጥሞ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ያድጋል ፡ ሥልጣኑ ፡ ይስፋፋል ፡ ብዬ ፡ በተስፋ ፡ የምጠባበቀው ፡ ሰው ፡ ከንቱ ፡ ሆኖ ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ ሳይበቃ ፡ ቀረ ።

753 እቤተ ፡ ክሲያን ፡ (ቤተ ፡ ክርስቲያን) ፡ ሄደን ፡ ባውዳመቱ ፡ ቀን ፡
—ሰው ፡ ረግጠን ፡ መጣን ፡ መቋሚያ ፡ እንኳ ፡ አጥተን ።

ሠ ፡ መቆሚያ ፡ መተላለፊያ ፡ አጥተን ፡ ሰው ፡ እየረመረምን ፡ መጣን ።

ወ ፡ እቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ሄደን ፡ እሰው ፡ ዐፅም ፡ ላይ ፡ ቆመን ፡ የሙታንን ፡ ዐጥንት ፡ ረግጠን ፡ መጣን ።

754 ከቤተ ፡ ክሲያን ፡ ጓሮ ፡ አንድ ፡ ጥጥ ፡ ቢኖረኝ ፡
—ለልብስህ ፡ አታስብ ፡ አፈራለሁ ፡ አለኝ ።

ሠ ፡ በቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ያለኝ ፡ ጥጥ ፡ ለልብሴ ፡ አያሳስበኝም ፤ ሳይችለኝ ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ በመቃብር ፡ ዐፈር ፡ መሆን ፡ አለብኝ ፤ አንድ ፡ ቀን ፡ ወደ ፡ መሬትነት ፡ እለወጣለሁ ።

755 ከተማርነው ፡ ሁሉ ፡ ከጠቢብነት ፡
—ቢቀርም ፡ አይጐዳ ፡ ብር ፡ አፍሳሽነት ።　　　　(ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ብር ፡ ሠሪ ፡ መሆን ፡ አይጠቅምም ፤ እንዲያውም ፡ ይህ ፡ ሞያ ፡ ቢቀር፡ ጕዳት ፡ አያመጣም ።

ወ ፡ ለበቅሎ ፡ ለፈረስ ፡ ጌጥ ፡ ለሴቶች ፡ መሣሪያ ፡ እያሉ ፡ ብር ፡ እያቀለጡ ፡ ማባከኑ ፡ ቢቀር ፡ መልካም ፡ ነው ።

756 ከተራራው ፡ ቆሞ ፡ የሚጣራው ፡ ማነው ፤
—ወንድሜ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወይ ፡ በለው ፡ ወይ ፡ በለው ።

ሠ ፡ የሚጣራው ፡ ወንድሜ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አቤት ፡ በለው ፤ ድምፅ ፡ አሰማው ።

ወ ፡ ወዮ ፡ ወዮ ፤ ወንድሜ ፡ በለው ፡ ሞተ ፤ ተቀበረ ፤ ዐፈር ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ።

757 ከተወለድኩ ፡ ቈየሁ ፡ ካደግሁም ፡ ዘገየሁ ፤
—ከሰው ፡ ፊት ፡ በልቼ ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ አረጀሁ ።

ሠ ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ ተወልጄ ፡ በልቼ ፡ ጠጥቼ ፡ በዕድሜዬ ፡ ከሰው ፡ በፊት ፡ አረጀሁ ።

ወ ፡ ራሴን ፡ ሳልችል ፡ በመለመን ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ በማየት ፡ አረጀሁ ።

758 ከትንሣኤው ፡ ሳንደርስ ፡ ከሌት ፡ ምጽአት ፡
—አሁኑን ፡ አለቅን ፡ ገና ፡ በማማት ።

ሠ ፡ የሕማማት ፡ ጾም ፡ ጐዳን ፤ በጾም ፡ በጸሎት ፡ በስግደት ፡ ብዛት ፡ ሰውነታችን ፡ ይከሣ ።

ወ ፡ ሰውን ፡ ማማት ፡ መቦጨቅ ፡ ይጐዳል ፤ የሰውን ፡ ስም ፡ በከንቱ ፡ ማንሣት ፡ በእግዚአብሔር ፡ ዘንድ ፡ ያስፈርዳል ።

759 ከንጉሡ ፡ ግቢ ፡ ከበሩ ፡ ቆመሽ ፡
—በይ ፡ ያለቀሰውን ፡ ትነግሪኛለሽ ።

ሠ ፡ በንጉሡ ፡ አደባባይ ፡ ታዛቢ ፡ ሆነሽ ፡ ቁሚና ፡ በኋላ ፡ ያዘነውን ፡ የተበደለውን ፡ ትነግሪኛለሽ ።

ወ ፡ የበላ ፡ ሆድ ፡ አይችልምና ፡ በንጉሡ ፡ ሞት ፡ ያለቀሰውን ፡ ሐዘን ፡ የጸናበትን ፡ ለይተሽ ፡ ትነግሪኛለሽ ።

760 ከአቤል ፡ ዠምሮ ፡ ነበር ፡ የታመነ ፤
—አሁን ፡ ግን ፡ ብናየው ፡ ሞት ፡ ቀጣፊ ፡ ሆነ ።

ሠ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ ሞት ፡ አይዋሽም ፡ ነበር ፤ ባንደበቱ ፡ ሐሰት ፡ ገብቶ ፡ አያውቅም ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ ዋሾና ፡ ቀጣፊ ፡ አታላይ ፡ ሆኗል ።

ወ ፡ ዛሬስ ፡ አለ ፡ አለና ፡ ሞት ፡ ቡቃያውን ፡ ወጣቱን ፡ እየቀጠፈ ፡ ይወስድ ፡ ዠመረ ።

761 ከእንግዲህስ ፡ ወዲህ ፡ አልወጣም ፡ ከቤቴ ፤
—የሌላ ፡ አልፈልግም ፡ ይበቃኛል ፡ ሀብቴ ።

ሠ ፡ እንግዲህ ፡ ወዲህ ፡ የሌላ ፡ ሰው ፡ ገንዘብ ፡ አልመኝም ፤ የግል ፡ ሀብቴ ፡ ለፍቼ ፡ ያገኘሁት ፡ ደክሜ ፡ ያፈራሁት ፡ ቅርስ ፡ ይበቃኛል ።

ወ ፡ ሌላ ፡ አልመኝም ፤ እግዚአብሔር ፡ ቢያቈይልኝ ፡ ይኸው ፡ ባሌ ፡ «ሀብቴ» ፡ በቂዬ ፡ ነው ።

762 ከእንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ አይሆንም ፡ ጨለማ ፤
—እንይዘዋለን ፡ በር ፡ በሩን ፡ በሻማ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ በየደጃፉ ፡ በየበሩ ፡ ሻማ ፡ እያበራን ፡ እንቀመጣለን ፤ ከንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ በጨለማ ፡ ውስጥ ፡ አንኖርም ።

ወ ፡ እየተሽቀዳደምን ፡ ኬላውን ፡ እንይዘዋለን ፤ ማለፊያ ፡ እናሳጣዋለን ።

763 ከእንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ የልቤን ፡ ልናገር ፤
—ያባ ፡ መልአክ ፡ ተድላ ፡ ጠጁ ፡ ውሃ ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ከአባ ፡ መልአክ ፡ ተድላ ፡ ቤት ፡ ጠጅ ፡ ነው ፡ ተብሎ ፡ የሚሰጠው ፡ ጥሩ ፡ ውሃ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ጠጅ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ለሚያጠጣው ፡ ጌታ ፡ ላባ ፡ መልአክ ፡ ተድላ ፡ እንባ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ፈሰሰለት ፤ ሕዝቡ ፡ ካንዠት ፡ አለቀሰለት ።

764 ከከተማ ፡ ገብተን ፡ ከማኸሉ ፡ ላይ ፡
—ብዙ ፡ ሰው ፡ አገኘን ፡ ወተት ፡ ወተት ፡ ባይ ።

ሠ ፡ ከተማ ፡ ሄደን ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ ሥራ ፡ ፈቶ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ሲዞር ፡ ሲንከራተት ፡ ላይና ፡ ታች ፡ እያለ ፡ ሲዋትት ፡ አየን ።

ወ ፡ የከተማው ፡ ሰው ፡ ብዙው ፡ ወተት ፡ ፈላጊ ፡ ነው ።

765 ከወሰድሃትማ ፡ ከደረቴ ፡ ነጥቀህ ፡
—ባንተም ፡ ቀን ፡ ይኸው ፡ ነው ፡ ያዛት ፡ ተጠንቀቀህ ።

ሠ ፡ ራስህ ፡ በልጠብህ ፡ ከነጠቅኸኝ ፡ ባንተም ፡ ጊዜ ፡ ይኸው ፡ ነውና ፡ አ
ስብበት ፤ ተጠንቅቀህ ፡ ያዛት ።

ወ ፡ ዱሮውኑ ፡ ባልወሰድህብኝ ፤ ብሶብህ ፡ ከነጠቅኸኝ ፡ ተጠንቀቅ ፡ ጥቃ
ቴን ፡ እንደምወጣብህ ፡ ዕወቅ ።

766 ከወንድሞቼ ፡ ጋር ፡ ምንድን ፡ ያጣላኛል ፤
—ወይኔ ፡ የምበላው ፡ መሬት ፡ ይኖረኛል ።

ሠ ፡ ለመሬት ፡ ብዬ ፡ ከወንድሞቼ ፡ ጋራ ፡ ለምን ፡ እቀያየማለሁ ፤ ዕድሌ ፡
የሚሰጠኝን ፡ መሬት ፡ አላውቅም ።

ወ ፡ ኖሬ ፡ ኖሬ ፡ እግዚአብሔር ፡ ባዘጋጀልኝ ፡ በሦስት ፡ ክንድ ፡ መሬት ፡
መወሰኔ ፡ አይቀርም ፤ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ መሬት ፡ ይበላኛል ።

767 ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ጥበብ ፡ ከለበሰችው ፡
—እሷ ፡ መርገፉን ፡ ነው ፡ የመረጠችው ።

ሠ ፡ ርሷ ፡ የፈቀደችው ፡ ከጥበቡ ፡ ኩታ ፡ ይልቅ ፡ መርገፉን ፡ ነው ፤ በው
ኗም ፡ በሕልሟም ፡ የሚታያት ፡ እሱው ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ወ ፡ ያንን ፡ ሁሉ ፡ ዕውቀት ፡ ይዛ ፡ ዐፈር ፡ ሆነች ፤ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡
ረገፈች ።

768 ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ፍጥረት ፡ ዐይናችን ፡ ካየው ፡
—ይኸ ፡ የኛ ፡ ንጉሥ ፡ ድልድሉ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ንጉሣችን ፡ ያላጠረ ፡ ያልረዘመ ፡ ድልድል ፡ የሆነ ፡ መካከለኛ ፡ ቁ
መት ፡ ያለው ፡ ነው ።

ወ ፡ የኛ ፡ ንጉሥ ፡ ሥራው ፡ በየሄደበት ፡ ሁሉ ፡ በማናቸውም ፡ ነገር ፡
ድል ፡ ማድረግ ፡ ነው ፤ ከፊቱ ፡ ጦር ፡ አይቆምም ፤ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የድል ፡
ዕድል ፡ ይገጥመዋል ።

769 ከዚህ ፡ ተወልጄ ፡ ከዚህ ፡ አድጊያለሁ ፤
—መኪና ፡ ሰፊ ፡ ነኝ ፡ የሰው ፡ ልክ ፡ ዐውቃለሁ ። (ማ ፡ ወ ፡ አ) ፡

ሠ ፡ የሰውን ፡ መጠን ፡ በቀላሉ ፡ ለማወቅና ፡ ለመረዳት ፡ እችላለሁ ።

ወ ፡ ሰውን ፡ መገመት ፡ ይሆንልኛል ፤ ቅሌታሙንና ፡ ጨዋውን ፡ ሰው ፡
በፊቱ ፡ ዐውቀዋለሁ ።

770 ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ፍጥረት ፡ ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ዓለም ፡
—ደግሰው ፡ ደግሰው ፡ በይ ፡ አልተገኘም ።

ሠ ፡ ለፍተው ፡ ወጥተው ፡ ወርደው ፡ ያዘጋጁትን ፡ ድግስ ፡ የሚጋበዝላ
ቸው ፡ አጡ ፤ በላተኛ ፡ አላገኙም ፤ ድግሳቸው ፡ ባከነ ።

ወ ፡ ቅን ፡ አሳብ ፡ የነበረው ፡ ያ ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ እንግዲህ ፡ አልተገኘም ፤
ሞተ ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለየ ።

771 ከዚያችም ፡ እኅቷ ፡ ከሰከረችቱ ፡
—የምታሳዝነኝ ፡ ያልታደለችቱ ።

ሠ ፡ ሰክራ ፡ ከምትንዠባረረው ፡ ይልቅ ፡ መጠጥ ፡ ያላገኘችው ፡ እኅቷ ፡ ታሳዝነኛለች ።

ወ ፡ ከሞተችው ፡ ይልቅ ፡ ቋሚዋ ፡ ዕድለ ፡ ቢስ ፡ በመሆኗ ፡ ታሳዝነኛ ለች ፤ የሞተ ፡ ምን ፡ አለበት ፤ ዕዳውን ፡ ጠቀለለ ፤ ከተተ ።

772 ከደጅ ፡ ሲያባርረኝ ፡ ዘመዴ ፡ ወዳጄ ፡
—ከፉ ፡ ቀን ፡ አወጣኝ ፡ የወለድሁት ፡ ልጄ ።

ሠ ፡ ዘመድ ፡ ወዳጄ ፡ ፊት ፡ ሲነሣኝ ፡ ሥጋ ፡ ደግ ፡ ነው ፡ አይጨክንምና፡ ክፉውን ፡ ቀን ፡ ልጄ ፡ አወጣኝ ።

ወ ፡ የገዛ ፡ ልጄን ፡ በልቼ ፡ የረኃቡን ፡ ዘመን ፡ አለፍሁት ፤ የልጄን ፡ ሥጋ፡ እርሜን ፡ እየተመገብሁ ፡ ክፉውን ፡ ቀን ፡ ወጣሁ ፤ ሕይወቴን ፡ አተረፍኩ ።

773 ከደጋ ፡ ላይ ፡ ሆኜ ፡ ቈላን ፡ ተመለከትሁ ፤
—ከወራጅ ፡ በስተቀር ፡ አንድም ፡ ወጪ ፡ አላየሁ ።

ሠ ፡ አላፊ ፡ አግዳሚው ፡ ወደ ፡ ቈላ ፡ ወራጅ ፡ እንጂ ፡ ወደ ፡ ደጋው ፡ የ. ሚወጣ ፡ አንድም ፡ መንገደኛ ፡ የለም ።

ወ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የማየው ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ሲወርድ ፡ እንጂ ፡ ከ መቃብር ፡ ሲወጣ ፡ አይደለም ።

774 ከገበሬው ፡ ይሁን ፡ ከበሬው ፡ ብርታት ፡
—መተማ ፡ ተጠምዶ ፡ ጐንደር ፡ መፈታት ።

ሠ ፡ እመተማ ፡ ላይ ፡ የተፈለመ ፡ የርሻው ፡ ፊር ፡ ጐንደር ፡ ገታ ፤ የበሬ ውና ፡ የገበሬው ፡ ጽናት ፡ ይገርማል ።

ወ ፡ መተማ ፡ ላይ ፡ ንጉሡ ፡ ድል ፡ ስለ ፡ ሆኑ ፡ ጐንደር ፡ ተፈታ ፤ ተዘረፈ ፤ ተበዘበዘ ።

775 ከገንዘቤ ፡ ሁሉ ፡ አጣሁበት ፡ ትርፍ ፡
—ብሩ ፡ ላልቦ ፡ ሆነ ፡ ወርቁም ፡ ለመርገፍ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ብሩ ፡ ለግር ፡ አልቦ ፡ ለሴት ፡ ወይዘሮ ፡ ጌጥ ፡ ወርቁ ፡ ለፈረስ ፡ ለበ ቅሎ ፡ መሣሪያ ፡ ለመረሻትና ፡ ለመርገፍ ፡ በመሆን ፡ አለቀ ፤ ደኅና ፡ ነገር ፡ ላይ ፡ ሳይውል ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ሁለቱንም ፡ ልጆቼን ፡ ብሩንና ፡ ወርቁን ፡ ሞት ፡ ነጠቀኝ ፤ በመቃብር፡ ረግፈው ፡ ቀሩ ።

776 ከጥርጊያው ፡ ጐዳና ፡ ይቀርባል ፡ ብለው ፡
—በስርቆሽ ፡ በር ፡ ሄዱ ፡ ይሻላል ፡ ብለው ።

ሠ ፡ ያቋርጣል ፡ ብለው ፡ በጓሮ ፡ በር ፡ በኩል ፡ ተሹለክልከው ፡ ሄዱ ።

ወ ፡ ማታለሉንና ፡ ማጭበርበሩን ፡ ይጠቅማል ፡ ብለው ፡ ይዘውታል ።

777 ከጥንት ፡ የመጣ ፡ ነው ፡ ይኸ ፡ ልማዳችን ፤
—ኮሬ ፡ ብሎ ፡ መሄድ ፡ በልጅነታችን ።

ሠ ፡ ሰው ፡ በወጣትነት ፡ ዘመኑ ፡ ትዕቢት ፡ ይሰማዋል ፤ ሡራት ፡ ያጠቃዋል ።

ወ ፡ እግዚአብሔርን ፡ ለመለመን ፡ ኮራ ፡ ወደሚባለው ፡ ገዳም ፡ በልጅነት ፡ መንኖ ፡ መሄድ ፡ ካባት ፡ የመጣ ፡ ነው ።

778 ከፍ ፡ ያለ ፡ ሰራዊት ፡ ቀድሞ ፡ ነበረኝ ፤
—ዛሬም ፡ አልደኸየሁ ፡ ብዙ ፡ ዐጀብ ፡ አለኝ ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ጥንቱም ፡ ባይበዛ ፡ አሁንም ፡ በቂ ፡ ተከታይ ፡ አለኝ ፤ ብቻዬን ፡ አልቀረሁም ።

ወ ፡ ዛሬም ፡ የሚያስገርምና ፡ የሚያስደንቅ ፡ አንዳንድ ፡ ነገር ፡ ይገጥመኛል ፤ ዐጀብ ፡ የሚያሰኝ ፡ አይጠፉም ።

779 ሡሉን ፡ ተኳሡለን ፡ አልዋልን ፡ ከቤታችን ፡
—በምን ፡ አማራቸው ፡ ዐቧራው ፡ መልካችን ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ሳንታጠብ ፡ ሳንጸዳ ፡ ዐቧራ ፡ የለበሰው ፡ መልካችን ፡ ምኑ ፡ አማራቸው ።

ወ ፡ ዐቧራ ፡ መልካ ፡ ባለው ፡ እርሻችን ፡ ላይ ፡ በምን ፡ ዐይናቸው ፡ ዐረፈ ፤ ምን ፡ ቢያስቡ ፡ ሊወስዱ ፡ ተነሡብን ።

780 ካህን ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ በሩቁ ፡ ሳየው ፡
—ለካስ ፡ ጨዋው ፡ ኖሯል ፡ የጠመጠመው ።

ሠ ፡ ጠምጥሞ ፡ ሳየው ፡ ቄስ ፡ የመሰለኝ ፡ መሀይምን ፡ ኖሯል ፤ በስመ ፡ አብን ፡ እንኳ ፡ የማያውቅ ፡ ነው ።

ወ ፡ ለካ ፡ ነገሩን ፡ የጠመጠመውና ፡ የጐነጐነው ፡ በሰው ፡ ነገር ፡ አይደርስም ፡ የሚባለው ፡ ጨዋው ፡ ሰው ፡ ኖሯል ።

781 ካህን ፡ ሞተ ፡ ብሎ ፡ አይነግሩም ፡ ዐዋጅ ፡
—እንዲያው ፡ በየደብሩ ፡ መላክ ፡ ነበር ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ ከየቤተ ፡ ክርስቲያኑ ፡ መልክት ፡ ይላክ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፤ የካህን ፡ ሞት ፡ በነጋሪት ፡ አይነገርም ፡ ነበር ፤ ይህ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ነው ።

ወ ፡ በየደብሩ ፡ በየክብረ ፡ በዓሉ ፡ እየሄደ ፡ ሲያገለግልና ፡ ሲዘምር ፡ መልአክ ፡ ከሰማይ ፡ የወረደ ፡ ይመስል ፡ ነበር ።

782 ከአባይ ፡ እስከ ፡ አባይ ፤ በሙሉ ፡ ሲገዙ ፡
—ያገር ፡ ዋስ ፡ ሆኑና ፡ በዳሞት ፡ ተያዙ ።

ሠ ፡ ለድፍን ፡ ጐጃም ፡ ዋስ ፡ ሆነው ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ በዳሞት ፡ ነገር ፡ ታግተዋል ፡ ይባላል ።

ወ ፡ ሕዝብ ፡ አስተዳዳሪ ፡ አገር ፡ አዋይ ፡ የነበሩት ፡ ሰው ፡ የማይቀረውን ፡ ሞት ፡ ሞቱ ፡ ወደ ፡ እውነተኛው ፡ ዓለም ፡ ሄዱ ።

783 ካገሩም ፡ እንዳይኖር ፡ ከሰው ፡ አይስማማ ፡
—ተሰብሮ ፡ አሁን ፡ መጥቶ ፡ ተቀምጧል ፡ ከተማ ።

ሠ ፡ ሰብሮ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ መጥቶ ፡ እከተማ ፡ ተቀምጧል ።
ወ ፡ አቶ ፡ ከተማ ፡ ከሄደበት ፡ አገር ፡ ተደብድቦ ፡ ተሰብሮ ፡ መጥቶ ፡ ተኝቷል ።

784 ካጣቢውም ፡ እንደሁ ፡ ከእንዶዱ ፡ ማነስ ፡
—ዐፈር ፡ መስሎ ፡ ታየኝ ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡ ልብስ ።

ሠ ፡ የማጠቢያ ፡ ሳሙና ፡ ወይም ፡ እንዶድ ፡ በማጣት ፡ ነው ፤ ወይስ ፡ ያጣቢ ፡ እጦት ፤ በሙሉ ፡ የሰዉ ፡ ልብስ ፡ አድሮ ፡ ይታየኛል ።
ወ ፡ ያዳም ፡ ልጅ ፡ የለበሰው ፡ ሥጋ ፡ ዐፈር ፡ ኋኝ ፡ ነው ፤ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ትቢያ ፡ ይሆናል ።

785 ክብርዎ ፡ ትልቅ ፡ ነው ፡ ሀብትዎም ፡ ብዙ ፡ ነው ፡ ችግር ፡ የለብዎ ፤
—ማዘን ፡ መነገድን ፡ ማን ፡ አስተማረዎ ።

ሠ ፡ ክብርዎ ፡ ትልቅ ፡ ሲሆን ፡ ችግር ፡ ሳይኖርብዎ ፡ በምን ፡ ምክንያት ፡ ለማንስ ፡ ይድላው ፡ ብለው ፡ ማእዘን ፡ ይነግዳሉ ።
ወ ፡ እንደ ፡ ተመቻቸውና ፡ እንደ ፡ ደላቸው ፡ ሰዎች ፡ መደሰትን ፡ አይሹም ፤ ማዘን ፡ መጸለይን ፡ ይወዳሉ ፤ እግዚአብሔር ፡ መረጠዎት ።

786 ክብር ፡ ለመኰንን ፡ ሽመታ ፡ ረከሰ ፡
—ከዳጕሳው ፡ ይልቅ ፡ ጥሩ ፡ እኽል ፡ ታፈሠ ።

ሠ ፡ እኽል ፡ ረከሰ ፤ ጥሩው ፡ እኽል ፡ ከመናኛው ፡ እኩል ፡ ይሸመታል ፤ ማፈሥ ፡ መዛቅ ፡ ሆነ ።
ወ ፡ በራስ ፡ መኰንን ፡ መሪነት ፡ እነቀኛዝማች ፡ ታፈሠ ፡ ዐድዋ ፡ ላይ ፡ ከፍ ፡ ያለ ፡ ክብር ፡ የሚያስገኝ ፡ ጀግንነት ፡ ፈጸሙ ።

787 ከፈቱልኝ ፡ ሳይል ፡ የገባው ፡ ሰው ፡ ማነው ፤
—የኔ ፡ እንኳን ፡ የድኻው ፡ ቤቴ ፡ ተፈሪ ፡ ነው ።

ሠ ፡ የኔ ፡ እንኳ ፡ የምስኪኑ ፡ ቤት ፡ የታፈረ ፡ የተከበረ ፡ ነው ፤ ማንም ፡ አይደፍረውም ።
ወ ፡ ትዳሬ ፡ ንብረቴ ፡ ጃንሆይ ፡ ናቸው ፤ ወግ ፡ ማዕርግ ፡ ያገኘሁት ፡ በተፈሪ ፡ ዘመነ ፡ መንግሥት ፡ ነው ።

788 ኮላሽና ፡ ታሞ ፡ አፍቀራ ፡ ጭምር ፡ ባንድነት ፡ ያማሉ ፡
—መቅደላን ፡ የንጉሥ ፡ ደም ፡ አለበት ፡ እያሉ ።

ሠ ፡ መቅደላ ፡ የንጉሥ ፡ ዘር ፡ ነው ፡ ይባላል ፤ ሰዎች ፡ የነጋሢ ፡ ደም ፡ አለው ፡ እያሉ ፡ ያወራሉ ።
ወ ፡ መቅደላ ፡ ታሪክ ፡ ያለው ፡ አገር ፡ ነው ፤ የንጉሥ ፡ ደም ፡ ፈሶበታል ፡ ጀግናው ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስን ፡ ያኽል ፡ ሰው ፡ ሞቶበታል ።

789 ኮሶ ፡ ለመጠጣት ፡ ብትሰደኝ ፡ እናቴ ፡
—ቀጨሞ ፡ ጋበዙኝ ፡ እናያ ፡ ጕለንቴ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 962 ፡ 1024) ፡
(አ ፡ በ) ፡

ሥ ፡ ኮሶ ፡ ለመጠጣት ፡ ብሄድ ፡ እንጕለንቴ ፡ የቀጨሞ ፡ ፍሬ ፡ አቅመው ፡ መለሱኝ ።

ወ ፡ ግብር ፡ ለመግባት ፡ ቤተ ፡ መንግሥት ፡ ብሄድ ፡ በቀጨሞ ፡ አርጩሚ፡ ተመትቼ ፡ መጣሁ ።

790　ወሌ ፡ የጣይቱን ፡ አይቶ ፡ ብርታቷን ፡
—ውሃም ፡ አልመረጠ ፡ ጠጣው ፡ ድፍርሱን ።　(አ ፡ እ) ፡

ሥ ፡ ወሌ ፡ የጠራና ፡ ያልጠራ ፡ መሆኑን ፡ ሳይለይ ፡ አንፎርሻውን ፡ ውሃ ፡ ለጋው ፤ ድፍርሱን ፡ ጠጣው ።

ወ ፡ የእቴጌ ፡ ጣይቱን ፡ ብርታት ፡ አየና ፡ ወሌ ፡ አባ ፡ ጠጣው ፡ ከተፋፋመው ፡ ጦር ፡ ውስጥ ፡ ገባ ፤ ከጠላቱ ፡ ጋራ ፡ በቈራጥነት ፡ ተዋጋ ።

791　ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ ነው ፡ የታመነ ፡ አሽከር ፡
—ከተላከ ፡ ወዲያ ፡ ቢሞትም ፡ አይቀር ።　(1) (ወ ፡ ጸ ፡ ጋ) ፡

ሥ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ አንዠት ፡ አርስ ፡ ነው ፤ ምንም ፡ እክል ፡ ቢገጥመው ፡ ችግር ፡ ቢያገኘው ፡ ይሞታታል ፡ እንጂ ፡ መልክቱን ፡ ሳያደርስና ፡ ሳይፈጽም ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ (ደጃዝማች) ፡ እተላከበት ፡ አገር ፡ ሞቶ ፡ ሬሳው ፡ መጣ ፤ በሄደበት ፡ ቦታ ፡ አልቀረም ፤ ላገሩ ፡ ዐፈር ፡ በቃ ።

792　ወርቀ ፡ ዘቦ ፡ ግምጃ ፡ የሚገባትን ፡
—በጨርቋ ፡ ቀበሯት ፡ ምንትዋብ ፡ ወሌን ።　(ዘለ ፡ ቍ ፡ 523) ፡

ሥ ፡ በወርቀ ፡ ዘቦ ፡ ግምጃ ፡ መከፈን ፡ የሚገባት ፡ ምንትዋብ ፡ ወሌን ፡ በመናኛ ፡ ጨርቅ ፡ ጠቅለው ፡ ቀበሯት ።

ወ ፡ ምንትዋብ ፡ ወሌ ፡ በወጣትነቷ ፡ ሞተች ፤ አሳዛኝ ፡ ሞት ፡ ደረሰባት ።

793　ወርቄን ፡ ቀብሪያለሁ ፡ ችግርም ፡ የለብኝ ፤
—ኮራ ፡ ብዬም ፡ ብሄድ ፡ አይነወርብኝ ።

ሥ ፡ ብዙ ፡ ወርቅ ፡ ቀብሪያለሁ ፤ ችግር ፡ የለብኝምና ፡ እንደ ፡ ልቤ ፡ ለመሆን ፡ ለመዝናናት ፡ እችላለሁ ።

ወ ፡ አለኝታዬና ፡ ተስፋዬ ፡ የነበረውን ፡ ልጄን ፡ ወርቄን ፡ ተቀብርኩ ፡ ከዚህ ፡ ምን ፡ አደርጋለሁ ፤ መንኜ ፡ ኮራ ፡ ከሚባለው ፡ ገዳም ፡ ብሄድ ፡ አይሻልምን ።

794　ወርውረው ፡ ቢጥሉት ፡ ሸክላ ፡ መች ፡ ይድናል ፤
—ይሰበራል ፡ እንጂ ፡ ገል ፡ ዐፈር ፡ ይሆናል ።

ሥ ፡ ሸክላ ፡ ወርውረው ፡ ከጣሉት ፡ አይተርፍም ፤ ይደቃል ፤ ዐፈር ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ የሰው ፡ አካል ፡ ዐፈር ፡ ኋኝ ፡ ነው ፤ የለበሰው ፡ ሥጋ ፡ በመቃብር ፡ ትቢያ ፡ ይሆናል ።

(1) ደጃዝማች ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ ወልደ ፡ ሚካኤል ፡ ከነደጃዝማች ፡ ዐምደ ፡ ሚካኤል ፡ ጋራ ፡ ባይሮፕላን ፡ ወደ ፡ ደሴ ፡ ተልከው ፡ በማረፍ ፡ ላይ ፡ ባደጋ ፡ ምክንያት ፡ ስለ ፡ ሞቱ ፡ የቀሩት ፡ በመኪና ፡ በመንገድ ፡ ሲመለሱ ፡ የርሳቸው ፡ አስከሬን ፡ በዚያው ፡ አይሮፕላን ፡ ሆኖ ፡ ወደ ፡ አዲስ ፡ አበባ ፡ በመጣ ፡ ጊዜ ፡ የተገጠመ ።

795 ወርዳ ፡ ነበር ፡ ቈላ ፡ ሥራ ፡ ልታሠራ ፡
—ወደቀች ፡ ይላሉ ፡ በዚያው ፡ አገርግራ ።

ሠ ፡ ቈላ ፡ ወርዳ ፡ ፀሐይ ፡ አድክሟት ፡ ወደቀች ።
ወ ፡ አገርግራ ፡ ከሚባል ፡ አገር ፡ ጥራ ፡ ግራ ፡ ሞተች ።

796 ወስታ ፡ ከሜዳው ፡ ላይ ፡ ምንድነው ፡ ጅባቱ ፡
—ባይነግሩን ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የንጉሥ ፡ እናት ፡ ሞቱ ።

ሠ ፡ የንጉሡ ፡ እናት ፡ ሞተው ፡ በወስታ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ይለቀሳል ፤ ይረገዳል ፤ ሕዝቡ ፡ እንባ ፡ በንባ ፡ ይራጫል ።
ወ ፡ እንደ ፡ እናት ፡ ለሕዝባቸው ፡ ያዝኑና ፡ ይራሩለት ፡ የነበሩት ፡ ንጉሥ ፡ ሞቱ ፤ እናት ፡ የሆኑ ፡ ነጋሢ ፡ ዐረፉ ።

797 —ወተቱን ፡ ብንጠው ፡ ሸፍታ ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ፡
ወትሮም ፡ ካለማረፍ ፡ ከመርጋት ፡ የቀረ ።

ሠ ፡ ወተቱን ፡ ብንገፋ ፡ ብንገፋው ፡ ቅቤ ፡ ሳይወጣው ፡ ቀረ ፤ እየተዡረ ፈረፈ ፡ እንቢ ፡ አለ ፤ ቅባት ፡ ሊወጣው ፡ አልቻለም ።
ወ ፡ ገር ፡ ጭምት ፡ የነበረው ፡ ሰው ፡ መንገላታት ፡ መታሰር ፡ መፈታት ፡ ቢበዛበት ፡ ሸፈተ ፤ እበረሓ ፡ ገባ ፤ ፋኖ ፡ ሆነ ።

798 ወተት ፡ በጨለማ ፡ እያበላሻችሁ ፡
—ቀን ፡ እንዲህ ፡ ይገፋል ፡ እዩት ፡ ላሳያችሁ ። (ዘለ ፡ ቊ ፡ 18) ፡

ሠ ፡ እናንተ ፡ በጨለማ ፡ ወተት ፡ እየናጣችሁ ፡ ታባክናላችሁ ፤ እንደኔ ፡ በብርሃን ፡ ቀን ፡ ብትንጡት ፡ አይበላሽም ፡ ነበር ።
ወ ፡ ዕድሜ ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ያልቃል ፤ ዘመን ፡ በችግርም ፡ ውስጥ ፡ ሆኖ ፡ ይገፋል ፤ ጊዜ ፡ እንደማያልፍ ፡ የለም ።

799 ወታደር ፡ አይደለም ፡ ለመንግሥት ፡ ያደረው ፤
—እኔን ፡ ያከሰረኝ ፡ ያቡን ፡ ነው ፡ ያቡን ፡ ነው ።

ሠ ፡ እኔን ፡ ከችግር ፡ ላይ ፡ የጣለኝ ፡ ያለ ፡ ቅርሴን ፡ ያሳጣኝ ፡ አቡኑ ፡ ነው ፤ የዘረፈኝ ፡ ወታደር ፡ አይደለም ፤ ጳጳስ ፡ ነው ።
ወ ፡ ገንዘቤን ፡ ሀብቴን ፡ የጨረሰው ፡ ቡና ፡ ነው ።

800 ወትሮም ፡ ጠቢብ ፡ ነበር ፡ ሰሎሞን ፡ አባቱ ፤
—ምኒልክ ፡ በለጠ ፡ ሰው ፡ ይዞ ፡ መብላቱ ።

ሠ ፡ አባቱም ፡ ጠይብ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ ልጁ ፡ የበለጠ ፡ ሆነ ።
ወ ፡ እንደ ፡ ምኒልክ ፡ ከሕዝብ ፡ ጋራ ፡ መብላት ፡ የሚወድ ፡ ከቶ ፡ አልተገኘም ።

801 ወንበሩን ፡ አይደለሁ ፡ አልበይንልሽ ፤
ጌታውን ፡ አይደለሁ ፡ አልበይንልሽ ፤
—ግቢ ፡ ተመሬቱ ፡ ተፈረደብሽ ።

ሠ ፡ ዳኛው ፡ አድልቶ ፡ ፍትሕን ፡ አጓድሎ ፡ ከፈረደብሽ ፡ ወዳገርሽ ፡ ግቢ ።
ወ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርጃ ፡ ሆኖ ፡ የማይቀረውን ፡ ሞት ፡ ሞትሽ ፤ ወደ ፡ መሬትሽ ፡ ገባሽ ፤ ጥርኝ ፡ ዐፈር ፡ ሆንሽ ።

802 ወንዱም ፡ ይመጣና ፡ እምዬ ፡ ይልሻል ፤
ሴቱም ፡ ይመጣና ፡ እምዬ ፡ ይልሻል ፤
—አንቺውስ ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ ቤት ፡ አጥፊ ፡ ኖረሻል ።

ሠ ፡ ቤቱን ፡ ዐይኑ ፡ ተኰላውን ፡ ያጠፉሽው ፡ ለካ ፡ አንቺ ፡ ኖረሻል ፤ ወንዱም ፡ ሴቱም ፡ እሷ ፡ ናት ፡ እያለ ፡ ባንቺ ፡ ያመካኛል ።

ወ ፡ የመጣው ፡ ሁሉ ፡ እምዬ ፡ እናቴ ፡ እያለ ፡ ያለቅስልሻል ፤ ለካ ፡ በቤትሽ ፡ ያለውን ፡ ተካፍለሽ ፡ የምትኖሪ ፡ ቸር ፡ ሴት ፡ ኖረሻል ።

803 ወንድሜ ፡ ቤት ፡ ሠርቶ ፡ ሳይመርገው ፡ እስካሁን ፡
—አንተ ፡ ዐፈር ፡ ተሸከም ፡ እኔ ፡ ውሃ ፡ ልሁን ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ዐፈር ፡ አግዝ ፤ እኔ ፡ ውሃ ፡ ልቅዳና ፡ የወንድሜን ፡ ቤት ፡ እንምረግለት ፤ እንለስንለት ።

ወ ፡ አንተ ፡ ከሞትህና ፡ ዐፈር ፡ ሆነህ ፡ ከቀረህ ፤ ሳለቅስ ፡ እንባዬን ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ሳፈስ ፡ እኖራለሁ ፤ ደስታ ፡ አላገኝም ።

804 ወንድሜ ፡ ብቻውን ፡ ሲሄድ ፡ አለት ፡ ላለት ፡
—እሠይ ፡ የምሥራች ፡ ደመና ፡ ሆነለት ። (መዲ ፡ ቍ ፡ 6 ፤ ዘለ ፡ ቍ ፡ 156 ፡ 1127 ) ፡

ሠ ፡ ወንድሜ ፡ ጣይ ፡ እንዳይመታው ፡ ዋዕየ ፡ ሐሩር ፡ እንዳያቃጥለው ፡ ሰማዩ ፡ ዳመነለት ፤ ቀኑ ፡ ቀዝቃዛ ፡ ሆነለት ።

ወ ፡ እግዚአብሔር ፡ አላጋለጠውም ፤ ወንድሜ ፡ ያፈሰበው ፡ ደም ፡ ሳይታወቅ ፡ ተሸፍኖ ፡ ቀረ ።

805 ወንድሜን ፡ አጣሁት ፡ ብሻው ፡ ባስጠይቀው ፡
—ከተማሰው ፡ ገብቶ ፡ እንዳይገኝ ፡ ሳውቀው ።

ሠ ፡ እንደማይገኝ ፡ ሆዴ ፡ ሲያውቀው ፡ አድራሻ ፡ የሌለውን ፡ እከተማ ፡ የገባውን ፡ ወንድሜን ፡ በመላ ፡ እፈልገዋለሁ ።

ወ ፡ ሞቶ ፡ እመቃብር ፡ ውስጥ ፡ የገባውን ፡ ወንድሜን ፡ ሁለተኛ ፡ የማላገኘው ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ያንገበግበኛል ።

806 ወንድሜ ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ስፈልግ ፡ ሌሊት ፡
—አይብ ፡ በንቅብ ፡ አድሮ ፡ አገኘሁት ፡ ጧት ።

ሠ ፡ ማታ ፡ የጠፋው ፡ ወንድሜ ፡ አይብ ፡ በንቅብ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ አድሮ ፡ አገኘሁት ።

ወ አይብ ፡ በንቅብ ፡ ተቀምጦ ፡ አድሮ ፡ ኖሮ ፡ ጧት ፡ አገኘሁት ።

807 ወንድሜ ፡ ፈረስህን ፡ እንዳወጣ ፡ ሸጠው ፤
—ባስበው ፡ ከበደኝ ፡ እንኳን ፡ ልቀመጠው ።

ሠ ፡ እንኳን ፡ ልቀመጠው ፡ ይቅርና ፡ ያንተን ፡ ፈረስ ፡ አሽከር ፡ እየሳበው ፡ ቢከተለኝ ፡ አልፈቅድም ፤ ያለክብሬ ፡ ይህን ፡ ማድረጉ ፡ ይከብደኛል ፤ ይቀፈኛል ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ አንተ ፡ ሞተህ ፡ እኔ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ልኖር ፡ አልመኝም ፤ ባስበው ፡ ባወጣው ፡ ባወርደውም ፡ የማይሆንልኝ ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ።

808 ወንድሞቻችንስ ፡ በጣም ፡ በርትተዋል ፤
—አልበቀለም ፡ እንጂ ፡ ብዙ ፡ ዘር ፡ ዘርተዋል ።

ሠ ፡ ወንድሞቻችን ፡ በየቦታው ፡ ዘርተዋል ፤ በያለበት ፡ አዝምረዋል ፤ ሆኖም ፡ አልበቀለላቸውም ፤ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀርቷል ።

ወ ፡ ወንድሞቻችን ፡ ምንም ፡ ብዙ ፡ ልጆች ፡ ቢኖሯቸው ፡ አያሌዎቹ ፡ ሞተዋል ፤ ቤት ፡ ዘመዳሞቹን ፡ ሞት ፡ ያጠቃቸዋል ።

809 ወንድሞቼ ፡ ሁሉ ፡ አትኩራ ፡ ይሉኛል ።
—ኮራ ፡ ብዬ ፡ ሄጄ ፡ ብሞት ፡ ይሻለኛል ።

ሠ ፡ እየተክለፈለፍሁ ፡ ከምሄድ ፡ ረጋ ፡ ብዬ ፡ በመንጓደድ ፡ ብራመድ ፡ ይሻለኛል ።

ወ ፡ ኮራ ፡ ከሚባለው ፡ ገዳም ፡ ገብቼ ፡ ለእግዚአብሔር ፡ አገልግዬ ፡ ብሞት ፡ ድኅነተ ፡ ነፍስ ፡ ይኖረኛል ፡ ብዬ ፡ አምናለሁ ።

810 ወንዶች ፡ ተማሮችን ፡ ሳትድር ፡ እናት ፡ ሆና ፤
—ያለምራት ፡ ቀረች ፡ አወይ ፡ አወይ ፡ ዝና ።

ሠ ፡ ወንዶች ፡ ልጆቿን ፡ ሳትድርና ፡ ምራቶች ፡ ሳይኖሯት ፡ ቀረች ።

ወ ፡ የዓለሙ ፡ ሁሉ ፡ (የመላ ፡ ኢትዮጵያ) ፡ እራት ፡ የኑሮ ፡ ድጋፍ ፡ የነበረች ፡ ዝናዋ ፡ ያማረ ፡ እቴጌ ፡ መነን ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ በሞት ፡ ተለየች ።

811 ወንጌል ፡ ተምሯል ፡ ወይ ፡ ያባት ፡ ፈረስ ፤
—ይትረፍ ፡ ለነገ ፡ አይል ፡ ምንም ፡ ቢደግስ ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ምንም ፡ ብዙ ፡ ቢደገስ ፡ መቈጠብና ፡ ለነገዬ ፡ ማለት ፡ አያውቅም ፤ የተገኘውን ፡ አብሮ ፡ መካፈልና ፡ መጨረስ ፡ ይወዳል ።

ወ ፡ አባ ፡ ይትረፍ ፡ (ራስ ፡ አባተ ፡ ቧለው) ፡ ለጠላት ፡ ጊዜ ፡ አይሰጥም ፤ ባለጋራውን ፡ ሳይውል ፡ ሳያድር ፡ ሥር ፡ ሳይሰድ ፡ ዕለቱን ፡ ማጥፋት ፡ ይወዳል ።

812 ወየው ፡ ዳኛ ፡ አግኝቶ ፡ ዦማን ፡ የከሰሰው ፤
—ደሞሳ ፡ መድረቁ ፡ እንዳልወሰደ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ እንዳልሰረቀና ፡ እንዳልወሰደ ፡ ሰው ፡ ደርሶ ፡ ጨዋ ፡ ይሆናል ፤ አላየሁም ፡ ብሎ ፡ ይክዳል ፤ ዐይኑ ፡ ደረቅ ፡ ነው ።

ወ ፡ የዦማ ፡ ወንዝ ፡ ሰው ፡ እንዳልወሰደ ፡ ነፍስ ፡ እንዳላጠፋ ፡ ሁሉ ፡ በጋ ፡ ሲመጣ ፡ ይደርቃል ፤ ውሃ ፡ አይገኝበትም ።

—ወይኔን ፡ ተሸክሜ ፡ እዞራለሁኝ ፤
813 አንድም ፡ የሚገዛኝ ፡ አላገኘሁኝ ።

ሠ ፡ የወይን ፡ እሸቴን ፡ ይዤ ፡ እንከራተታለሁ ፤ እዞራለሁ ።

ወ ፡ ወዮታን ፡ አተረፍኩ ፤ እዬዬን ፡ ይዤ ፡ ቀረሁ ፤ ሐዘንና ፡ ትካዜ ፡ የማይለየኝ ፡ ሆን ፤ የሚያጽናናኝ ፡ አጣሁ ።

814 ወይስ ፡ ሞኝ ፡ አትባል ፡ አይደለህ ፡ ሕፃን ፤
—ምን ፡ ጊዜ ፡ ረሳኸው ፡ ነግሬህ ፡ ስሜን ።

ሠ ፡ አሁን ፡ ነግሬህ ፡ ስሜን ፡ ከምን ፡ ጊዜው ፡ ዘነጋኸው ፤ ልበ ፡ ቢስ ፡ ዝንጉ ፡ ነህ ፤ የማስታወስ ፡ ኀይል ፡ የለህም ።

ወ ፡ ያገሬ ፡ የስሜን ፡ ሕዝብ ፡ ከምን ፡ ጊዜ ፡ ረሳኸውና ፡ ጥንቃቄ ፡ ጐደለህ ።

815 ወይ ፡ አላሳጨደው ፡ ወይ ፡ ከብት ፡ አልበላው ፤
—ከቶ ፡ መቼ ፡ ይሆን ፡ ያ ፡ ሣር ፡ ማለቂያው ።

ሠ ፡ በክልሉ ፡ ውስጥ ፡ ያለው ፡ ሣር ፡ ለመቼም ፡ አያልቅ ፤ አይታጨድ ፤ ወይም ፡ ከብት ፡ አይግጠው ፤ እንዲያው ፡ ተቀምጧል ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ የምንሣቀየው ፡ እስከ ፡ መቼ ፡ ድረስ ፡ ነው ፤ ምነው ፡ መከራችን ፡ በዛ ፤ አሳራችን ፡ አላልቅ ፡ አለ ።

816 ወይ ፡ አልሆነ ፡ ሙሴ ፡ ወይ ፡ አልሆነ ፡ ኢያሱ ፤
—ርብን ፡ ከፈለው ፡ ከግር ፡ እስከ ፡ ራሱ ። (1)

ሠ ፡ ከላይ ፡ እስከ ፡ ታች ፡ የርብን ፡ ወንዝ ፡ ከፈለው ፤ ሠንጥቆት ፡ ተሻገረ ።

ወ ፡ የርብ ፡ ወንዝ ፡ በፈሰሰ ፡ አገር ፡ ግዛት ፡ አገኘ ።

817 ወይ ፡ አልተቀደሰ ፡ የባረኩት ፡ ሰው ፤
—ንጉሥ ፡ መስቀልዎን ፡ ቢተዉት ፡ ምነው ። (2)

ሠ ፡ ክህነት ፡ የለዎ ፤ ሥልጣነ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አልተቀበሉ ፤ መስቀል ፡ ምን ፡ ያደርግልዎታል ፤ ላይባርኩበት ፡ ለምን ፡ ያዙት ።

ወ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ እጅግ ፡ አይጨክኑ ፤ ሕዝብ ፡ መስቀልዎን ፡ እባክዎ ፡ ይተዉት ።

818 ወይ ፡ አንተ ፡ አትታጣ ፡ እኔ ፡ አልሞትልህ ፤
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ ገድ ፡ ሆነህ ፡ ትቈየኛለህ ።

---

(1) የራስ ፡ ወልደ ፡ ሥላሴ ፡ ልጅ ፡ ደጃች ፡ ነጋሽ ፡ ስለ ፡ ሸፈተና ፡ አልገዛም ፡ ስላለ ፡ በዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ ትእዛዝ ፡ ራስ ፡ አዳል ፡ ለጦርነት ፡ ወደ ፡ በጌምድር ፡ ሲሄዱ ፡ ሞልቶ ፡ የነበረውን ፡ «ርብ» ፡ የሚባለውን ፡ ወንዝ ፡ ስለ ፡ ተሻገሩ ፡ የተገጠመ ።

(2) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ደብረ ፡ ታቦር ፡ ላይ ፡ አንዱን ፡ ባለጠጋ ፡ ትልቅ ፡ ቤት ፡ ስለ ፡ ነበረው ፡ ለሕዝብ ፡ ማቃጠያ ፡ ስጠኝ ፡ ቢሉት ፡ እንኳን ፡ ቤቱ ፡ እኔስ ፡ የራስዎ ፡ አይደለሁምን ፡ ቢላቸው ፤ ነጣቂ ፡ ንጉሥ ፡ ማድረጉ ፡ ነውን ፡ ብለው ፡ እንዲሰቀል ፡ ስላደረጉ ፡ ሚስቱ ፡ ያለቀሰችው ።

ሠ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ተፊቴ ፡ አትጠፋም ፤ በየሄድኩበት ፡ መዠመሪያ ፡ የማ
ገኝህ ፡ አንተን ፡ ነው ።
ወ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ መቃብርህን ፡ አየዋለሁ ፤ ሳልፍ ፡ ሳገድም ፡ እመለከት
ሃለሁ ፤ ከሐሳቤ ፡ አትጠፋም ።

819 ወይ ፡ ወር ፡ ተራ ፡ የለኝ ፡ ዕረፍት ፡ አላገኝ ፤
—ዘወትር ፡ በጭቃ ፡ እለፋለሁኝ ።

ሠ ፡ የሚተካልኝ ፡ ሳይኖር ፡ ዕረፍት ፡ ሳላገኝ ፡ ጭቃ ፡ በመርገጥ ፡ እለፋ
ለሁ ።
ወ ፡ በጭቃ ፡ ሹም ፡ እንገላታለሁ ፤ እታሰራለሁ ፤ እፈታለሁ ፤ እወጣለሁ ፤
እወርዳለሁ ።

820 ወይ ፡ ዕድሌ ፡ ሀብቴ ፡ ምን ፡ ያለሁ ፡ ሰው ፡ ነኝ ፤
—ከልፍኙ ፡ ወጥቼ ፡ እዳስ ፡ ገባሁኝ ።

ሠ ፡ ከእልፍኝ ፡ መግባቴ ፡ አዳራሽ ፡ መቀመጤ ፡ ቀረና ፡ ወደ ፡ ዳስ ፡ ገባ
ሁ ፤ እያደር ፡ እዋረድ ፡ ዠመር ።
ወ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ክብርና ፡ ማዕርግ ፡ ቀረና ፡ ዕዳ ፡ ገባሁ ።

821 ወይዘሮ ፡ ወሰኔን ፡ ወሊድ ፡ ተዋቸው ፤
—በቃቸው ፡ ዐረፉ ፡ ሚሊዮን ፡ ወልደው ። (1) (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ብዙ ፡ ልጅ ፡ ካገኙ ፡ በኋላ ፡ መውለድ ፡ አቆሙ ፤ ወሊድ ፡ ተዋቸው ።
ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ወሰኔ ፡ ሚሊዮንን ፡ ወልደው ፡ ዐረፉ ።

822 ወደ ፡ ፊት ፡ መጥቼ ፡ እንዳልጠይቅህ ፡
—እኔም ፡ ጊዜ ፡ የለኝ ፡ አንተም ፡ በድን ፡ ነህ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 91) ፡

ሠ ፡ እኔ ፡ መጥቼ ፡ እንዳልጠይቅህ ፡ ጊዜ ፡ የለኝም ፤ አንተም ፡ “ ጽን ” ከሚባ
ለው ፡ ሩቅ ፡ አገር ፡ ነህ ።
ወ ፡ መጥቼ ፡ እንዳልጠይቅህ ፡ አንተም ፡ ዐፈር ፡ ሆንክ ፤ እንግዲህ ፡ አን
ገናኝም ።

823 ወዴት ፡ ሄዱ ፡ ብዬ ፡ ጌቶችን ፡ ጠየቅሁኝ ፤
—ዐፈር ፡ ባይኔ ፡ ብለው ፡ ትላንት ፡ አለፉ ፡ አሉኝ ።

ሠ ፡ ዐፈር ፡ ባይኔ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ እሄዳለሁ ፡ ብለው ፡ ትላንት ፡
በዚህ ፡ በኩል ፡ አለፉ ፡ አሉኝ ።
ወ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ ተለይተው ፡ ተቀበሩ ፤ በዐይናቸው ፡ ዐፈር ፡
ተሞላበት ።

824 ወድቆ ፡ ቢፈራርስ ፡ ዘሞ ፡ ቤታችን ፡
—በምን ፡ ይጠገናል ፡ ይህ ፡ አለማዘን ።

ሠ ፡ ማእዘን ፡ ከሌለ ፡ መሎጊያ ፡ ከታጣ ፡ የሚዘመው ፡ ቤት ፡ በምን ፡
ይቃናል ።
ወ ፡ ማዘን ፡ መተከዝ ፡ ከሌለ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ በምን ፡ ይታለፋል ፤
እንደ ፡ ምን ፡ ይቻላል ።

---

(1) ወይዘሮ ፡ ወሰኔ ፡ ወልደ ፡ ገብርኤል ፡ ሚሊዮን ፡ ወልደ ፡ መስቀልን ፡ እንደ ፡ ተገላ
ገሉ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ በሞት ፡ መለየታቸውን ፡ ለመናገር ፡ ነው ።

825 ወገራ ፡ አሳላፊ ፡ ደንቢያ ፡ እንጀራ ፡ ጣይ ፡
—ተበላህ ፡ ጐንደሬ ፡ አትነሣም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ምግብ ፡ ከተመገብህ ፡ በኋላ ፡ መነሣት ፡ አትችልምን ።

ወ ፡ የጐንደር ፡ ሕዝብ ፡ ጠላት ፡ ሊይዝህ ፡ ነው ፡ እኮ ፤ ተነሥተህ ፡ እጅ
ህን ፡ አውጣ ፤ አምረህ ፡ ሽሽ ።

826 ወገራ ፡ አታመንታ ፡ በለሳም ፡ አትባክን ፤
—አስታውቅሃለሁ ፡ በቅርብ ፡ ቀን ፡ ስሜን ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 299) ፡

ሠ ፡ ሳይውል ፡ ሳያድር ፡ ስሜን ፡ እነግርሃለሁ ።

ወ ፡ ወገራም ፡ በለሳም ፡ በሙሉ ፡ እንድትከት ፤ ስሜንም ፡ ወደ ፡ ፊት ፡
አስታውቅሃለሁና ፡ ተጠንቀቀህ ፡ ቈይ ።

827 ወጌሻ ፡ ተገኝቷል ፡ እቴ ፡ ቶሎ ፡ ነይ ፤
—እንዲህ ፡ ተነካክተሽ ፡ ትቀሪያለሽ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ አንካሳ ፡ ሆነሽ ፡ እንዳትቀሪ ፡ የተሰበርሽውን ፡ በትኩሱ ፡ ተጠገኚው ፤
ወጌሻ ፡ ይይሽ ።

ወ ፡ ከእስላም ፡ ጋራ ፡ ኖረሽ ፡ ክርስትናሽን ፡ አጕድፈሽ ፡ ትቀሪ ፡ ነወይ ፤
ወደ ፡ አገርሽ ፡ ተመልሰሽ ፡ ከዘመድ ፡ አትቀላቀይም ፡ ወይ ።

828 ወጥመድ ፡ መጠመዱን ፡ ያ ፡ ቆቅ ፡ አላየው ፤
—ያልጠረጠረ ፡ እንደሁ ፡ መያዙ ፡ እንጂ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ያ ፡ ቆቅ ፡ ካልገነገነ ፡ ካልበረገገና ፡ ካልበረረ ፡ መያዝ ፡ ላይቀርለት ፡
ነው ።

ወ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ጠላቱን ፡ ሠግቶ ፡ ካልጠበቀ ፡ ከባለጋራው ፡ እጅ ፡ መ
ውደቁ ፡ የማይቀር ፡ ነው ፤ (ያልጠረጠረ ፡ ተመነጠረ) ።

829 ዋቄ ፡ ዲቦ ፡ ቤቱን ፡ አኵርቶ ፡ ቢሠራ ፡
—ኀይሉ ፡ ቢወጣበት ፡ ተለመጠ ፡ ደራ ።

ሠ ፡ ኵርቶ ፡ ተሠርቶ ፡ የነበረው ፡ የዋቄ ፡ ዲቦ ፡ ቤት ፡ ኀይሉ ፡ ቢወጣ
በት ፡ ዘበጠ ፤ ደሳሳ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ያ ፡ ይታበይና ፡ ይኰራ ፡ የነበረው ፡ ዋቄ ፡ ዲቦ ፡ የያዘውን ፡ አገር ፡
ደራን ፡ ኀይሉ ፡ (ንጉሥ ፡ ኀይለ ፡ መለኮት) ፡ ረግጦ ፡ ገዛው ፤ ሕግን ፡
አስተማረው ፤ አስገበረው ።

830 ዋናውስ ፡ በሽታ ፡ ምንም ፡ አልጐዳቸው ፤
—ካገገሙ ፡ ወዲያ ፡ ግርሻ ፡ ገደላቸው ።

ሠ ፡ ጤናቸውን ፡ ካገኙ ፡ በኋላ ፡ ያው ፡ በሽታቸው ፡ ተመልሶ ፡ ገደላቸው ።

ወ ፡ አባ ፡ ግርሻ ፡ (ራስ ፡ ዳርጌ) ፡ ድል ፡ አደረጓቸው ፤ ድምጥማጣቸውን ፡
አጠፉቸው ።

831 ዋየለሽ ፡ ተማሪ ፡ አሳብ ፡ የሌለው ፡
—ያንን ፡ መሳይ ፡ ቀለም ፡ ካፊር ፡ ቀየጠው ።

ሠ ፡ ቀለሙን ፡ ወስዶ ፡ ካፊር ፡ ደባለቀው ፤ አፈሰሰው ።

ወ ፡ ወዳያልኝ ፡ ወዲያ ፡ ያን ፡ መሳይ ፡ መልክና ፡ ዕውቀት ፡ ይዞት ፡ ተቀበረ ፤ አሳዛኝ ፡ ሞት ፡ ሞተ ።

832 ዋድላና ፡ ደላንታ ፡ ሁሉም ፡ አገር ፡ ነው ፤
—እንዴት ፡ የጁን ፡ ለቆ ፡ ይባክናል ፡ ሰው ።

ሠ ፡ አገሩን ፡ የጁን ፡ ትቶ ፡ ሄዶ ፡ ለምን ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ይንከራተታል ፤ በያለበት ፡ ይዞራል ።

ወ ፡ በጁ ፡ የያዘውን ፡ ትቶ ፡ ሌላ ፡ ለማግኘት ፡ ይጣጣራል ፤ በቃኝን ፡ አያውቅም ፡ ወይ ፤ ለምን ፡ የሰውን ፡ ገንዘብ ፡ አይጠግብም ።

833 ውሃ ፡ አጠጪ ፡ ጠፍቶ ፡ ከምንጃር ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፤
—ያች ፡ የኔ ፡ አበባ ፡ ረገፈች ፡ አሉ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ውሃ ፡ የሚያጠጣት ፡ ጠፍቶ ፡ ተክሉ ፡ ደረቀች ፤ አበባዬም ፡ ረገፈች ።

ወ ፡ አበባ ፡ እያልኩ ፡ የምጠራት ፡ እኅቴ ፡ ሞተች ፤ ለመዳን ፡ ተስፋ ፡ ሲኖራት ፡ ባስታማሚ ፡ ጥፋት ፡ ዐረፈች ።

834 ውሃው ፡ ጥሩ ፡ ሆኖ ፡ ልብስ ፡ ስላነጣ ፡
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ ከዚህ ፡ ወንዝ ፡ አጣቢ ፡ አይታጣ ።

ሠ ፡ ውሃው ፡ ጥሩ ፡ ስለ ፡ ሆነ ፡ ከዚህ ፡ ወንዝ ፡ ልብስ ፡ የሚያጥብ ፡ አይጠፋም ።

ወ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ከዚህ ፡ ወንዝ ፡ ውስጥ ፡ ልብስ ፡ የሚሰርቅ ፡ አይጠፋም ።

835 ውሃ ፡ ጠማህ ፡ አሉ ፡ ከመንገድ ፡ ገብተህ ፤
—ደረቀ ፡ መሰለኝ ፡ አያሌው ፡ ጠጅህ ።

ሠ ፡ የጠጅ ፡ ጌታ ፡ የነበርከው ፡ አያሌው ፡ ከመንገድ ፡ ገብተህ ፡ ውሃ ፡ እንኳን ፡ አጣህና ፡ ቸገረህ ፡ ወይ ?

ወ ፡ ጠጅ ፡ የምታጠጣን ፡ ጌታችን ፡ አያሌው ፡ በሞት ፡ ተለየኸን ፡ ቤትህ ፡ ተፈታ ፡ ጌትነትህ ፡ በቃ ፡ ተከተተ ።

836 ውቢቷ ፡ ሙሽራ ፡ ከሰፋችልን ፡
መሶብና ፡ አገልግል ፡ እናቀርባለን ፤
ሙሽራችን ፡ ምረጥ ፡ የምትወደውን ፤
—ሁለቱን ፡ አገልግል ፡ ትገዛ ፡ እንደሆን ።

ሠ ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ብለህ ፡ እኚህን ፡ ሁለቱን ፡ አገልግሎች ፡ አንተ ፡ ግዛቸው ፤ ሥንቅ ፡ መያዣ ፡ ይሆኑሃል ፤ በርትተህ ፡ አስቀራቸው ።

ወ ፡ መሾም ፡ አገር ፡ መግዛት ፡ በማዕርግ ፡ ማደግ ፡ ቢያምርህ ፡ ለሁለቱ ፡ ባለሥልጣኖች ፡ በቅንነት ፡ ታዘዝ ፤ ከልብ ፡ አገልግል ።

837 ውዲቱ ፡ ኢትዮጵያ ፡ አክርማ ፡ ይዛለች ፤
—ለልጆቿ ፡ መብሊያ ፡ ገና ፡ ትሰፋለች ።

ሠ ፡ ለልጆቿ ፡ ምግብ ፡ ማቅረቢያ ፡ መሶብ ፡ ትሰፋለች ፤ ማዕድ ፡ መሥሪያ ፡ ታዘጋጃለች ።

ወ ፡ ኢትዮጵያ ፡ መንግሥቷን ፡ ታስፋፋለች ፤ የተወሰዱባትን ፡ አገሮች ፡ ለልጆቿ ፡ ታስመልሳለች ።

838 ውድማው ፡ ይለቅለቅ ፡ ይሰጣበት ፡ ነዶ ፤
—የኛ ፡ ተራ ፡ ቀርቷል ፡ ያ ፡ ሂዶ ፡ ያ ፡ ሂዶ ።

ሠ ፡ ዐውድማው ፡ ተለቅልቋል ፤ የአኺዶው ፡ ተራ ፡ ደርሷል ፤ ክምሩን ፡ እንጣልና ፡ ውቂያ ፡ እንዠምር ።

ወ ፡ ሁሉም ፡ ሂዶ ፡ ብቻችንን ፡ ቀርተናል ፤ እንግዲህ ፡ እኛም ፡ ጊዜ ፡ ሞታችንን ፡ እንጠብቅ ።

839 ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ባተ ፡ መልካም ፡ ናቸው ፤
—እኋላ ፡ ቀርቼ ፡ ሲሄዱ ፡ አየኋቸው ።

ሠ ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስን ፡ በስተኋላቸው ፡ ስመለከታቸው ፡ ባታቸው ፡ ያምራል ፤ የተሞናደለ ፡ ነው ።

ወ ፡ በዕድሜ ፡ ሰንብቼ ፡ ያፄ ፡ ቴዎድሮስን ፡ ሞት ፡ በማየቴ ፡ እደነቃለሁ ።

840 ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ እጅግ ፡ ተዋረዱ ፤
—የሸዋን ፡ መኳንንት ፡ እጅ ፡ ነሥተውት ፡ ሄዱ ። (1)

ሠ ፡ ለበታቾቻቸው ፡ አጐንበሰው ፡ ሰላምታ ፡ ሰጡ ፤ እኩዮቻቸው ፡ ላልሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ሲወድቁ ፡ ሲነሡ ፡ ሰንብተው ፡ ሄዱ ።

ወ ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ የሸዋን ፡ መኳንንት ፡ እጅ ፡ እጁን ፡ ቈርጠውት ፡ ሄዱ ፤ ግፍ ፡ ዋሉበት ፤ አይቀጡ ፡ ቅጣት ፡ ቀጡት ።

841 ዐድዋ ፡ ገበያ ፡ ላይ ፡ አይቼህ ፡ ነበርሁ ፤
—እኔም ፡ እኮ ፡ እናትህ ፡ መልካም ፡ ገበየሁ ። (አ ፡ አ) ፡

ሠ ፡ በዐድዋው ፡ ገበያ ፡ እኔም ፡ ዐወቅሁበት ፤ ብዙ ፡ ነገር ፡ ገበየሁ ፤ አልተታለልሁም ።

ወ ፡ ፊታውራሪ ፡ ገበየሁ ፡ መልካም ፡ ዠብዱ ፡ ሠራህ ፤ ጥሩ ፡ ስምን ፡ አተረፍህ ፤ ላገርህ ፡ ታላቅ ፡ ሞያን ፡ ዋልክ ።

842 ዐሊ ፡ ዐሊን ፡ ገሎት ፡ ደስ ፡ ብሎት ፡ አደረ ፤
—መልሱ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሆን ፡ ሰርጉ ፡ እንዲህ ፡ ያማረ ።

ሠ ፡ ሰርጉ ፡ ተዋጥቶ ፡ ነበር ፤ እንዲህ ፡ አልነበረም ፤ መልሱን ፡ ደግሞ ፡ ለማየት ፡ ያብቃን ።

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ሸዋ ፡ መጥተው ፡ ከአቤቶ ፡ ሰይፉ ፡ ጋራ ፡ ተዋግተው ፡ ድል ፡ ካደረጉ ፡ በኋላ ፡ ምርኮኛውን ፡ እጅና ፡ እግሩን ፡ ስላስቈረጡት ፡ ባሏ ፡ የሞተባት ፡ የሸዋ ፡ ሴት ፡ ያለቀሰችው ።

ወ ፡ ዐሊ ፡ ዐሊን ፡ በመግደሉ ፡ ተደስቷል ፤ የኋላውን ፡ ቂም ፡ በቀል ፡ አላ ስታወሰም ፤ ደሙን ፡ የሚወጣ ፡ ብድሩን ፡ የሚመልስ ፡ ዘመድ ፡ የመ ጣበት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ወዮለት ።

843 ዐርብ ፡ ረቡን ፡ በጧት ፡ እንግደፍ ፡ ያላችሁ ፤
—ጊዜ ፡ እንዲህ ፡ ይደርሳል ፡ ስሙኝ ፡ ልንገራችሁ ።

ሠ ፡ እዩት ፡ ሰዓት ፡ እንዲህ ፡ ሲደርስ ፡ ዐርብ ፡ ረቡን ፡ ልትገድፉ ፡ ነበር ፤ ለጥቂት ፡ ልትሳሳቱ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ጭቈና ፡ መከራ ፡ አለፈና ፡ እንደዚህ ፡ ካለው ፡ መልካም ፡ ጊዜ ፡ ላይ ፡ ደረስን ፤ አያችሁ ፡ ወንድሞቼ ፤ ትዕግሥት ፡ ደስታን ፡ ይወልዳል ።

844 ዐርብ ፡ ረቡን ፡ ገደፍሁ ፡ እንጀራ ፡ ባዋዜ ፤
—እንዲህ ፡ ለማይቈየው ፡ ለሚደርሰው ፡ ጊዜ ።

ሠ ፡ ሰዓቱ ፡ እንዲህ ፡ ሲደርስ ፡ ወጥ ፡ እስኪሠራ ፡ ዐርብ ፡ ረቡን ፡ መታ ገሥ ፡ አቃተኝ ፤ ለጥቂት ፡ በአዋዜ ፡ ገደፍሁ ፤ መታገሥ ፡ ተስኖኝ ፡ በማ ይረባ ፡ ነገር ፡ ተሳሳትሁ ።

ወ ፡ ብዙ ፡ ዘመን ፡ ለማልቈይበት ፡ ዓለም ፤ እንደ ፡ ጥላ ፡ ለሚያልፈው ፡ ዕድ ሜዬን ፡ ሙሉ ፡ ስዋትት ፡ የነፍሴን ፡ ነገር ፡ ረስቼው ፡ ኖርሁ ፤ ፈጣ ሪዬን ፡ በደልሁ ።

845 ዐባይ ፡ በጣና ፡ ላይ ፡ ሲሻገር ፡ አየና ፤
—ልጄ ፡ ጣና ፡ ገባ ፡ እንደ ፡ ዐባይ ፡ ሆነና ።

ሠ ፡ የዐባይን ፡ ውሃ ፡ ይመስል ፡ ልጄ ፡ በጣና ፡ ባሕር ፡ ላይ ፡ አለፈ ።

ወ ፡ ልጄ ፡ ከጣና ፡ ገባ ፤ ከባሕሩ ፡ ጋራ ፡ ተደባለቀ ።

846 ዐባይ ፡ ወዲያ ፡ ማዶ ፡ የበቀለች ፡ ዕንጨት ፡
—አስተውሎ ፡ ላያት ፡ ወይን ፡ ናት ፡ ወይን ፡ ናት ።

ሠ ፡ ዐባይ ፡ ማዶ ፡ የምትታየው ፡ ተክል ፡ ወይን ፡ ትመስላለች ፤ ልብ ፡ አድርጎ ፡ ሲመለከቷት ፡ የወይን ፡ ተክልነቷ ፡ ይታወቃል ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ የእናትን ፡ ነገር ፡ ምን ፡ ያደርጓል ፤ ምትክ ፡ አይገኝ ላት ፤ መሰል ፡ የላት ፤ አሁን ፡ እንደ ፡ እናት ፡ የሚያስብና ፡ የሚያዝን ፡ የት ፡ ይገኛል ።

847 ዐባይ ፡ ዋና ፡ ገብተህ ፡ የማታውቀውን ፡
—ተጣና ፡ አብዬ ፡ እንድትወጣ ፡ ሁን ።

ሠ ፡ ጣናን ፡ ዋኝተህ ፡ ነፍስህን ፡ ለማዳን ፡ በርታ ፤ ሕይወትህን ፡ ለማዳን ፡ ተጣጣር ።

ወ ፡ አብዬ ፡ ከጣና ፡ ደሴት ፡ ላይ ፡ ታስረህ ፡ እንዳትቀር ፡ እጅህን ፡ ለማ ውጣት ፡ ሞክር ፤ ተስፋ ፡ አትቍረጥ ።

848 ዐባይ ፡ ውሃ ፡ ሞልቶት ፡ ይታያል ፡ ራሱ ፤
—በፍቅር ፡ ጠብ ፡ አለ ፡ እስቲ ፡ ዋና ፡ አትርሱ ።

ሠ ፡ ዋናን ፡ ማወቅ ፡ ይገባል ፤ መዋኘትንም ፡ መርሳት ፡ አያስፈልግም ።

ወ ፡ በፍቅር ፡ መኻል ፡ ጠብ ፡ አለና ፡ የማጥቃትን ፡ ዘዴ ፡ አለመርሳት ፡ ነው ።

849 ዐውደ ፡ ዓመቱን ፡ ሁሉ ፡ ከወገኖቹ ፡ ጋር ፡ አክብሮ ፡ አስከበረ፡
—መስቀል ፡ ዕንቍጣጣሽ ፡ ገናንም ፡ ነበረ ። (መ ፡ አ) ፡

ሠ ፡ ለመስቀል ፡ ለዕንቍጣጣሽና ፡ ለገና ፡ በዓል ፡ ከዘመዶቹ ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ ውሎ ፡ ነበር ፤ ዐውደ ፡ ዓመቱን ፡ ያከበረው ፡ ከወገኖቹ ፡ ጋራ ፡ ነው ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ መስቀል ፡ ገናና ፡ ዕንቍጣጣሽ ፡ እንደሚያስደስቱ፡ ሁሉ ፡ ሕዝቡን ፡ ያስደስቱ ፡ ነበር ፤ የትፍሥሕትና ፡ የሐሤት ፡ መገኛ ፡ ገናና ፡ ጌታ ፡ ነበሩ ።

850 ዐይኔ ፡ መቼ ፡ በራ ፡ መቼ ፡ ዳነልኝ ፤
—የሰው ፡ ፊት ፡ ማየቴ ፡ በጣም ፡ ደነቀኝ ።

ሠ ፡ ዐይኔ ፡ ድኖ ፡ ሰው ፡ ለማየት ፡ መቻሌ ፡ በጣም ፡ ገረመኝ ፤ እንደዚህ ፡ በቶሎ ፡ የሚሻለኝ ፡ አልመሰለኝም ፡ ነበር ።

ወ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ አዱኛዬ ፡ ጠፍቶ ፡ ተቸግሬ ፡ አጥቼ ፡ ነጥቼ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ ማየቴ ፡ መገጠጤ ፡ በጣም ፡ ያስገርመኛል ።

851 ዐይኔ ፡ ዐፈር ፡ ገባበት ፡ ወይኔ ፡ ወየው ፤
—ቀጸላዬን ፡ ጥዬ ፡ ባለቅስ ፡ ምነው ።

ሠ ፡ የራሴ ፡ ቀጸላ ፡ የፊቴ ፡ መከለያ ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ምነው ፡ አላለቅስ ፤ በዐ ይኔ ፡ ዐፈር ፡ ይገባበት ፡ የለም ፡ ወይ ።

ወ ፡ ሲነጠልብኝ ፡ ማልቀስ ፡ ይነሰኝን ፤ ቀጸላ ፡ ሲሞት ፡ እኔ ፡ ያላዘንኩ ፡ ማን ፡ ይዘንልኝ ።

852 ዐይንህ ፡ ብርሃን ፡ አይችል ፡ አንተ ፡ ገመምተኛ ፤ (1)
—ይቈረቍርሃል ፡ ና ፡ ተመለስ ፡ ተኛ ። (አ ፡ መ) ፡

ሠ ፡ ዐይንህን ፡ ያምሃል ፤ ዐርፈህ ፡ ተኛ ፤ ከፀሓይ ፡ አትውጣ ።

ወ ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ይቈጭሃል ፤ ውሎ ፡ አድሮ ፡ ያሳዝንሃል ፤ ወደኛ ፡ ብትመ ለስ ፡ ከኛ ፡ ብትቀላቀል ፡ ይሻልሃል ።

853 ዓለም ፡ አድንቆታል ፡ ጠበቃችንን ፤
—ጠቅል ፡ አንሣ ፡ ብሎ ፡ ቢያስፈጥምልን ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ጠበቃችን ፡ ባለጋራችንን ፡ ረታልን ፤ ውርርዱን ፡ አስነሣው ።

ወ ፡ ጠቅል ፡ ጠላትን ፡ አስጨረሰው ፤ አስጨፈጨፈው ፤ ከኢትዮጵያ ፡ አስወጥቶ ፡ አበረረው ፤ ማንነቱን ፡ አሳወቀው ።

854 ዓሣ ፡ ምን ፡ ቸግሮ ፡ ተርፎል ፡ በየወንዙ ፤
—ገና ፡ ያበሉናል ፡ መረቡን ፡ ከያዙ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

(1) ደጃች ፡ ኃይለ ፡ ሥላሴ ፡ ጉግሳ ፡ ባ፲፱፻፳፰ ፡ ዓ ፡ ም ፡ ከድተው ፡ ወደ ፡ ጠላት ፡ ጦር ፡ በተቀላቀሉ ፡ ጊዜ ፡ ትንቢታዊ ፡ ምክርን ፡ በያዘ ፡ ግጥም ፡ ተግሣጽ ፡ የተሰጠበት ።

ሠ ፡ ዓሣ ፡ ማጥመጃውን ፡ መረቡን ፡ ከያዙ ፡ የምንበላው ፡ አንቸገርም ፤ ዓሣ ፡ እንይዛለን ፤ እናጠምዳለን ።

ወ ፡ ጠላትን ፡ ማጥቃት ፡ ከዠመሩ ፡ የመረብን ፡ ወንዝ ፡ ከያዙ ፡ አንጠቃም ፤ ድል ፡ የኛ ፡ ነው ።

855 ዕቃ ፡ ተሸክሜ ፡ ያለመጠን ፡ ከብዶኝ ፡
—እኔን ፡ ካንተ ፡ በቀር ፡ የለም ፡ ያዋረደኝ ።

ሠ ፡ ሸክሜን ፡ ያቃለልክልኝ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ነህ ፤ ደክሞኝ ፡ ሳለ ፡ ከጫንቃዬ ፡ ያወረደልኝ ፡ ካንተ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ የለም ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ እኔን ፡ ያዋረድከኝ ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ነህ ፤ በሰው ፡ አላዝንም ።

856 ዕቃ ፡ እንግዛ ፡ ብለን ፡ ከተማ ፡ ገብተን ፡
—በማዘን ፡ ገበያ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ አየን ።

ሠ ፡ በማእዘን ፡ ተራ ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ አየን ፤ ቋሚና ፡ አግዳሚ ፡ ገዥው ፡ ለካ ፡ ብዙ ፡ ነው ።

ወ ፡ በማዘን ፡ በመተከዝ ፡ የሚኖረው ፡ ሰው ፡ ብዙ ፡ ነው ።

857 ዕቃ ፡ የሚያመጣ ፡ የሚላክ ፡ ሳይጠፋ ፡
—የዋሁ ፡ ዱባለ ፡ በገዛ ፡ እጁ ፡ ለፋ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ሳይጠፋ ፡ ተላላኪ ፡ ሳይታጣ ፡ የሚሸከም ፡ ሳይቸግር ፡ የዋሁ ፡ ዱባለ ፡ ዕቃ ፡ በማመላለስ ፡ ደከመ ፤ ለፋ ።

ወ ፡ ዱባለ ፡ አላርፍ ፡ ብሎ ፡ እንደበቱን ፡ ባለመጠበቁ ፡ መመታት ፡ መደብደብ ፡ ደረሰበት ።

858 ዕድሜውን ፡ ብንቈጥረው ፡ ተኝተን ፡ ሌሊት ፡
—አርባ ፡ ፊሪ ፡ ሆነው ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ። (1)

ሠ ፡ የንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ዕድሜ ፡ ብናስበው ፡ ለአርባ ፡ አንድ ፡ የጐደለው ፡ ሠላሳ ፡ ዘጠኝ ፡ ዓመት ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ዐርብ ፡ ቀን ፡ ሞተው ፡ ዐፈር ፡ ቀመሱ ፤ በዕለተ ፡ ዐርብ ፡ ተቀበሩ ።

859 ዕድሜው ፡ አጫጭሩ ፡ እየተዳረገኝ ፤
—ሴቲቱን ፡ እንደ ፡ ወንድ ፡ ገዳይ ፡ አደረገኝ ።

ሠ ፡ ወንድ ፡ ይመስል ፡ እኔን ፡ ሴቲቱን ፡ እንደ ፡ ገዳይ ፡ ቈጠሩኝ ፤ ታላቅ ፡ ጀብዱ ፡ የሠራሁ ፡ አስመሰሉኝ ።

ወ ፡ ዕድሜያቸው ፡ አጫጭር ፡ የሆነ ፡ ባሎች ፡ እያገባሁ ፡ ትገድላለች ፡ ባል ፡ አይኖርላትም ፡ እያሉ ፡ ያሙኛል ።

---

(1) ጐዠም ፡ ብዙ ፡ ጊዜ ፡ በመሳፍንት ፡ ሲገዛ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ በመጨረሻው ፡ ራስ ፡ አዳል ፡ ንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ተብለው ፡ ነገሡ ። ነገር ፡ ግን ፡ እምብዛም ፡ ሳይቈዩ ፡ ዐርብ ፡ ቀን ፡ በ፴፱ ፡ ዓመት ፡ ዕድሜያቸው ፡ ስለ ፡ ሞቱ ፡ ሕዝቡ ፡ ይወዳቸው ፡ ነበርና ፡ በቀብሩ ፡ ሰዓት ፡ አልቃሽ ፡ የገጠመችው ።

860 ዝሓው ፡ ለሰለሰ ፡ ሽማኔው ፡ ተቈጣ ፤
—እስከ ፡ ወዲያው ፡ ድረስ ፡ መጠቅለያው ፡ ታጣ ። (1)

ሠ ፡ ፈትሉ ፡ እጅግ ፡ ቀጠነ ፤ ሽማኔው ፡ ለመጠቅለል ፡ ተቸገረ ።

ወ ፡ እስከ ፡ መቼውም ፡ ይቅርታ ፡ የማይደረግበት ፡ ነው ፤ ፍጻሜውም ፡ እጅግ ፡ አሳዛኝ ፡ ሆነ ።

861 ዘመንህ ፡ አለቀ ፡ ይለኛል ፡ ሰው ፤
—ለካስ ፡ ኖሬ ፡ ኖሯል ፡ እኔ ፡ ሳላውቀው ።

ሠ ፡ ሳይታወቀኝ ፡ ሳይሰማኝ ፡ ለካስ ፡ ብዙ ፡ ዓመት ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላይ ፡ ኖሬያለሁ ፤ እያሌ ፡ ዘመን ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ቈይቻለሁ ።

ወ ፡ እኔ ፡ ሳልሰማ ፡ ቀርቼ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ እሱስ ፡ የሚቀመጠው ፡ «ኖሬ» ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ኖሯል ፤ የዚያ ፡ አገር ፡ ሰው ፡ ነው ።

862 ዘመድ ፡ ሂድ ፡ ይለኛል ፡ ሐኪም ፡ ወዳለበት ፤
—ምን ፡ ቸግሯችኋል ፡ እንዳገኘሁ ፡ ብሞት ።

ሠ ፡ ችግር ፡ ሳይደርስብኝ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ ሳላይ ፡ ሀብቴ ፡ እያለ ፡ አሁን ፡ ብሞት ፡ ምን ፡ ቸግሯችኋል ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ አገኘሁ ፡ የሞተውን ፡ ሞት ፡ ባገኝ ፡ ምን ፡ ነበር ፤ ከሱ ፡ ተለይቼ ፡ የምኖረው ፡ ሕይወት ፡ ምን ፡ ያኽል ፡ ያስደስተኛል ።

863 ዘመድ ፡ ወዳጅ ፡ የለኝ ፡ በደጁ ፡ የሚያልፍ ፤
—በል ፡ እንደዚህ ፡ ዝጋው ፡ ቤቴ ፡ ይቈለፍ ።

ሠ ፡ ዘመድ ፡ ወዳጅ ፡ ከጠፋ ፡ የሚገባበት ፡ ከታጣ ፡ ቤቴን ፡ ዝጋውና ፡ ቈልፈው ፤ ባዶውን ፡ ያለሰው ፡ ይኑር ።

ወ ፡ የሚጠይቀኝ ፡ ዘመድ ፡ ወዳጅ ፡ አሳጣኸኝ ፤ ባንተ ፡ ምክንያት ፡ ንብረቴ ፡ ተፈታ ፤ ትዳሬ ፡ ፈረሰ ።

864 ዘመዶቼ ፡ ሁሉ ፡ በጣም ፡ ተጫኑኝ ፤
—አይኑር ፡ ይጣ ፡ ብለው ፡ አስፈረዱብኝ ።

ሠ ፡ መላ ፡ ንብረቴን ፡ ለቅቄ ፡ ካገር ፡ እንድወጣ ፡ የገዛ ፡ ዘመዶቼ ፡ አስፈረዱብኝ ፤ ሰባራ ፡ ሥንጥር ፡ ሳሊዝ ፡ ባዶ ፡ እጄን ፡ እንድሰደድ ፡ አደረጉኝ ።

ወ ፡ ይጣ ፡ እሚባለው ፡ አገር ፡ አይኑር ፡ ብለው ፡ እንዳልቀመጥ ፡ አደረጉኝ፤ ከተወለድኩበት ፡ አገር ፡ እንዳልኖር ፡ በፍርድ ፡ ዘመዶቼ ፡ አስወጡኝ ።

865 ዘመዶቼ ፡ ሁሉ ፡ ውድማ ፡ የገባችሁ ፡
—ይድከመው ፡ ይታክተው ፡ ይጣሰው ፡ ብላችሁ ።

(1) ደጃች ፡ ብሩ ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ድል ፡ አድርገዋቸው ፡ «ጭልጋ» ፡ በሚባል ፡ ቦታ ፡ ታስረው ፡ ሳሉ ፤ ሚስታቸው ፡ ወይዘሮ ፡ የውብዳር ፡ ከልፍኝ ፡ አሽከራቸው ፡ ጋራ ፡ መዝናናታቸውን ፡ ሰምተው ፡ በበገና ፡ ስልት ፡ የገጠሙት ።

ሠ ፡ ዘመዶቼ ፡ ጥላችሁኝ ፡ ከውድማ ፡ የገባችሁ ፡ እናንተን ፡ በመፈለግ ፡ ውድማ ፡ በመጣስ ፡ ይድከመው ፡ ይታክተው ፡ ብላችሁ ፡ ነውን ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ ዘመዶቼ ፡ በሞት ፡ አለቃችሁ ፤ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ብቻዬን ፡ ያለዘር ፡ አስቀራችሁኝ ።

866 ዘመዶቼ ፡ እንሂድ ፡ እንግባ ፡ አገራችን ፤
—ምኒልክ ፡ ከሞተ ፡ እንጀራ ፡ አባታችን ።

ሠ ፡ የናታችን ፡ ባል ፡ ያሳደገን ፡ አባታችን ፡ ከሞተ ፡ ወደ ፡ አገራችን ፡ እንመለስ ፤ ከዘመድ ፡ እንቀላቀል ።

ወ ፡ ለክብር ፡ ለማዕርግ ፡ ያበቃን ፡ ኑሯችንን ፡ ንብረታችንን ፡ ያሻሻለልን ፡ ምኒልክ ፡ ከሞተ ፡ ከተማውን ፡ ለቀን ፡ ወደየትውልድ ፡ አገራችን ፡ እንግባ ።

867 ዘረፍረፍ ፡ ጐነፍነፍ ፡ ያለው ፡ ዙፋንህ ።
—አገር ፡ ምድር ፡ ሞልቷል ፡ ጠቅለው ፡ በጅህ ።

ሠ ፡ የዙፋን ፡ ልብስህ ፡ ተዝረፍርፏል ፤ ሰብስብ ፡ አድርገህ ፡ ያዘው ።

ወ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ (ቀ ፡ ኃ ፡ ሥ) ፡ መንግሥትህ ፡ ተስፋፍቷል ፤ በዙፋንህ ፡ ሥር ፡ ብዙ ፡ አገሮች ፡ ይተዳደራሉ ፤ መላ ፡ ኢትዮጵያን ፡ ጠቅለህ ፡ ይዘሃል ።

868 ዘምቶ ፡ የሞተ ፡ ሰው ፡ ያዝንለት ፡ አያጣ ፤
—አሞራ ፡ እንኳ ፡ ወርዶ ፡ ፊቱን ፡ ነጭቶ ፡ ወጣ ።

ሠ ፡ አሞራ ፡ እንኳ ፡ በወንድሜ ፡ ሞት ፡ እጅግ ፡ አዝኖ ፡ ፊቱን ፡ እየነጨ፡ ሲያለቅስ ፡ ውሎ ፡ ሄደ ፤ ሐዘኔን ፡ ተካፈለኝ ።

ወ ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ወድቆ ፡ የቀረውን ፡ ወንድሜን ፡ አሞራ ፡ ፊቱን ፡ እየነጨ ፡ ሥጋውን ፡ እየተቧጨቀ ፡ በላው ።

869 ዘቢቡን ፡ ገዝቼ ፡ ይገዬ ፡ ስጠብቀው ፡
—ቄሱ ፡ ዕጣኑን ፡ ወስዶ ፡ ካፈር ፡ ደባለቀው ።

ሠ ፡ ለብፅዐት ፡ የመጣውን ፡ ዕጣን ፡ ቄሱ ፡ ዐፈር ፡ ላይ ፡ በተነው ፤ ከመሬት ፡ ደባለቀው ።

ወ ፡ ቄሱ ፡ ለሞተው ፡ ሕፃን ፡ የግባተ ፡ መሬት ፡ ጸሎት ፡ አደረሰለት ፤ ቆሞ፡ አስቀበረው ።

870 ዘንድሮ ፡ በረዶ ፡ መንገዱን ፡ አገደኝ ፤
—ውሃ ፡ ሆኖ ፡ ባይቀር ፡ እንዴት ፡ በነደደኝ ። (አ ፡ መ) ፡

ሠ ፡ ተቈልሎ ፡ አላሳልፍ ፡ ያለኝ ፡ በረዶ ፡ ሻምቶ ፡ ውሃ ፡ የማይሆን ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ እንዴት ፡ በቈጨኝ ፡ ነበር ።

ወ ፡ እንዲያ ፡ ተጅመልምሎ ፡ በብዛት ፡ የመጣው ፡ የፋሽስት ፡ ጦር ፡ ድል፡ ሆኖ ፡ እንደ ፡ በረዶ ፡ ቀልጦ ፡ እንደ ፡ ጉም ፡ በኖ ፡ የማይጠፋ ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ እንዴት ፡ ባዘንሁ ፡ ነበር ።

871 ዘንድሮ ፡ አገራችን ፡ ዞራት ፡ ተለመደ ፤
—አንተ ፡ ማለት ፡ ቀርቶ ፡ ሁሉ ፡ አንቱን ፡ ወደደ ።

ሠ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ ከበሬታን ፡ ፈለገ ፤ አንቱ ፡ ለመባል ፡ ፈቀደ ፤ ራሱን ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ አደረገ ።

ወ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ ርስዎን ፡ ወደደ ፤ ሕፃኑ ፡ ሽማግሌው ፡ ያፈቅርዎት ፡ ዠመር ።

872 ዘንድሮ ፡ ፋሲካን ፡ ሰው ፡ እጋብዛለሁ ፤
—አንተ ፡ ሰንጋ ፡ ስጠኝ ፤ እኔ ፡ በግ ፡ አርዳለሁ ።  (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አንተ ፡ ለቍርጥ ፡ የሚሆነውን ፡ ሰንጋ ፡ ብትሰጠኝ ፡ እኔ ፡ ለድስት ፡ ወጥ ፡ የሚሆነውን ፡ በግ ፡ ገዝቼ ፡ አርዳለሁ ።

ወ ፡ እኔ ፡ በዘብ ፡ ታግጃለሁ ፤ «በጋርድ» ፡ ተከልክያለሁ ፤ ወደ ፡ ውስጥ ፡ ልገባ ፡ አልቻልኩም ።

873 —ዘንግ ፡ አላሉምና ፡ ለመያዝ ፡ በጅዎ ፡
—ከዘራ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ በትረ ፡ መንግሥትዎ ።

1 ሠ ፡ ዘንግ ፡ ለመያዝ ፡ አልፈቀዱም ፤ ለድጋፍ ፡ የሚያገለግል ፡ ከዘራ ፡ ነው ፡ እንጂ ።

ወ ፡ ወደ ፡ አባትዎ ፡ ዙፋን ፡ ለመውጣት ፡ መንግሥቱን ፡ ለመያዝ ፡ ችላ ፡ አላሉም ፤ በእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ በጅዎ ፡ ሆነ ።

2 ሠ ፡ በጅዎ ፡ የያዙት ፡ በትረ ፡ መንግሥት ፡ ከዘራ ፡ አይደለምን ።

ወ ፡ መንግሥትዎ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ ፈሳሽ ፡ እንደ ፡ እንግዳ ፡ ደራሽ ፡ አይደ ለም ፤ ከላይ ፡ ሲወርድ ፡ ሲዋረድ ፡ ተያይዞ ፡ የመጣ ፡ ነው ፤ ዙፋንዎ ፡ ጥንታዊ ፡ ነው ።

874 ዘውዴ ፡ ለጎዣሞች ፡ ሲደግስላቸው ፡
—ከቤትም ፡ አይደለ ፡ ከሜዳ ፡ ሰጣቸው ።

ሠ ፡ ዘውዴ ፡ ለጎዣሞች ፡ ያዘጋጀውን ፡ ግብዣ ፡ ከሜዳ ፡ ላይ ፡ አበላቸው ፤ እዱር ፡ ጋበዛቸው ።

ወ ፡ ዘውዴ ፡ ጎዣሞችን ፡ ጨፍጭፏቸው ፡ ረብርቧቸው ፡ አመለጠ ፤ ገድሎ ፡ ከሜዳ ፡ ላይ ፡ አንጥፏቸው ፡ ሄደ ።

875 ዘውዴ ፡ ያንን ፡ ገንቦ ፡ ተራድተን ፡ እንያዘው ፤
—አንተስ ፡ ማንገቻ ፡ አለህ ፡ እኔ ፡ እንዴት ፡ ላጉዘው ።  (1)

ሠ ፡ ያንተ ፡ ገንቦ ፡ መያዣ ፡ አለው ፤ ገመር ፡ ተሠርቶለታል ፤ ለማንገት ፡ ይመቻል ፤ የኔን ፡ የሌለውን ፡ እንዴት ፡ ላድርገው ፤ እባክህ ፡ እንረዳ ዳና ፡ እንያዘው ።

ወ ፡ ዘውዴ ፡ አንተ ፡ የጦር ፡ ግንባር ፡ አለህ ፤ ካንተ ፡ ፊት ፡ የሚቆም ፡ ሰራ ዊት ፡ የለም ፤ ገቶ ፡ መክቶ ፡ የሚመልስህ ፡ አይገኝም ።

---

(1) ራስ ፡ ጎይሉና ፡ ራስ ፡ ወልደ ፡ ገብርኤል ፡ ሲዋጉ ፡ የዳሞቱ ፡ ገዥ ፡ ደጃች ፡ አክሎግ ፡ ከድቶ ፡ ከራስ ፡ ወልደ ፡ ገብርኤል ፡ ሆኖ ፡ ሲዋጋ ፡ ጀግናው ፡ ደጃች ፡ ዘውዴ ፡ ስለ ፡ ማ ረኩት ፡ በቀረርቶ ፡ የተገጠመ ።

876 ዘግቼ ፡ ቈልፌ ፡ የተውሁትን ፡ እልፍኝ ፡
—ከፍተሽ ፡ መቈየትሽ ፡ በጣም ፡ አሳዘነኝ ።

ሠ ፡ የዘጋሁትን ፡ ቤት ፡ ክፍቱን ፡ አድርገሽ ፡ ለሌባ ፡ ጥለሽው ፡ መሄድሽ ፡ በጣም ፡ አሳዘነኝ ፤ አስተከዘኝ ።

ወ ፡ እንደዚያ ፡ ገር ፡ የዋህ ፡ የነበርሽው ፡ ሴት ፡ እንደዚህ ፡ ተለውጠሽ ፡ ክፉ ፡ ሁነሽ ፡ ስላገኘሁሽ ፡ ሐዘን ፡ ተሰማኝ ፤ የሰው ፡ ተፈጥሮ ፡ አስገረመኝ ።

877 ዘግይተህ ፡ ብትሄድ ፡ ገና ፡ ነው ፡ ጊዜህ ፤
—የፀሐይን ፡ መንገድ ፡ ምን ፡ አስወደደህ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ጥቂት ፡ ቈይተህ ፡ ጥላ ፡ ሲበርድልህ ፡ ለምን ፡ አትሄድም ፤ በዚህ ፡ ሐሩር ፡ እንዴት ፡ መራመድ ፡ ትችላለህ ።

ወ ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡ ሆይ ፡ እኅትኽ ፡ ልዕልት ፡ ፀሐይ ፡ የሞተችውን ፡ ሞት ፡ ሞትህ ፤ ተመሳሳይና ፡ አሳዛኝ ፡ የሆነ ፡ ሐዘንን ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ አተረፍክ ።

878 ዛሬስ ፡ አምኃየስ ፡ አረጀ ፡ ደቀቀ ፤
—ምድር ፡ ይይዝ ፡ ዝመር ፡ እየተንፏቀቀ ። (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ አምኃየስ ፡ በውነት ፡ አረጀ ፤ መግደርደር ፡ አልሆነለትም ፤ መሬት ፡ ለመሬት ፡ እየዳኸ ፡ ይሄድ ፡ ዝመር ።

ወ ፡ ግዛት ፡ ለማስፋፋት ፡ አገር ፡ ለማቅናት ፡ ይጣጣር ፡ ዝመር ፤ ታጥቆ ፡ ተነሣ ።

879 ዛሬ ፡ ብቻ ፡ ሳይሆን ፡ ጥንቱንም ፡ ባያት ፡
—እናት ፡ ኢትዮጵያ ፡ ባለሞያ ፡ ናት ።

ሠ ፡ ከጥንት ፡ ዠምሮ ፡ እናት ፡ ኢትዮጵያ ፡ እጅግ ፡ ሞያ ፡ ዐዋቂ ፡ ናት ፤ የባልትና ፡ ዕውቀት ፡ ቤት ፡ አያያዝ ፡ ለማንም ፡ የለም ፤ የተመሰገነች ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ናት ።

ወ ፡ ኢትዮጵያ ፡ ጥንትም ፡ ቢሆን ፡ ሥነ ፡ ጥበብና ፡ ሥልጣኔ ፡ የነበረባት ፡ አገር ፡ ናት ፤ በእጅ ፡ ሥራ ፡ ዕውቀትና ፡ በማናቸውም ፡ ሞያ ፡ የታወቀች ፡ ነበረች ።

880 ዛሬ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ሞተ ፡ ብሎ ፡ ያለ ፡ ማነው ፤
—ባያውቀው ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አዳራሽ ፡ ሙሉ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ዛሬ ፡ የሞተው ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ብቻ ፡ አይደለም ፤ ቤት ፡ ሙሉ ፡ ነው ።

ወ ፡ አዳራሽ ፡ ገብቶ ፡ ሙሉ ፡ ግብር ፡ ያበላ ፡ የነበረው ፡ ነው ፡ የሞተው ።

881 ዛሬ ፡ ጢት ፡ ገሥግሠን ፡ ገበያ ፡ ወጥተን ፡
—ፈልገን ፡ ፈልገን ፡ ጨው ፡ አጥተን ፡ መጣን ።

ሠ ፡ ጨው ፡ ፍለጋ ፡ ገበያ ፡ ወጥተን ፡ ብንዞር ፡ ብንንከራተት ፡ ሳናገኝ ፡ ቀርተን ፡ መጣን ፤ ጨው ፡ ተወደ፡ል ።

ወ ፡ በአሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ረጋ ፡ ያለ ፡ ጭምት ፡ ሰው ፡ አይገኝም ፤ የተጣላ ፡ የሚያስታርቅ ፡ የተበደለ ፡ የሚያስክስ ፡ ጨዋ ፡ የለም ።

882 ዝኆኒቱ ፡ ንቃኝ ፡ አለፈች ፡ በደጄ ፤
—ዐይኗን ፡ ጥርሷን ፡ ብሎ ፡ ያመጣታል ፡ ልጄ ።

ሠ ፡ ንቃኝ ፡ አቃላኝ ፡ በደጄ ፡ ያለፈችውን ፡ ዝኆን ፡ ልጄ ፡ ባይንሽ ፡ በጥርስሽ ፡ ብሎ ፡ ለምኖ ፡ ያመጣታል ።

ወ ፡ አሁን ፡ በደጄ ፡ ያለፈችውን ፡ ዝኆን ፡ ለጥርሷ ፡ ሲል ፡ ልጄ ፡ ዐይኗን ፡ መቶ ፡ ይገድላታል ።

883 ዝም ፡ ብለህ ፡ ተቀመጥ ፡ ይኸን ፡ ሰው ፡ አይስማ ፤
—አትታገሥም ፡ ወይ ፡ ከመታህ ፡ ወዲያማ ።

ሠ ፡ የልብህን ፡ ካደረስህና ፡ ከተደባደብክ ፡ ወዲያ ፡ እንኳ ፡ አትታገሥም ፤ ከዚህ ፡ የበለጠ ፡ ምን ፡ ለማድረግ ፡ ነው ፡ የምትጋበዘው ።

ወ ፡ ከተሸነፍክ ፡ ከተደበደብክ ፡ በኋላ ፡ የምትፍጨረጨረው ፡ ምን ፡ ልትሆን ፡ ነው ፤ ይልቅስ ፡ ሰው ፡ አይስማህ ፤ ዐርፈህ ፡ ተቀመጥ ።

884 ዝም ፡ ብለውኝ ፡ ሄዱ ፡ ጥለውኝ ፡ ካውድማ ፡
—ምን ፡ አረጋለሁኝ ፡ ትጣሰው ፡ ካሉማ ።

ሠ ፡ ጫካውን ፡ መንጥራ ፡ ውድማውን ፡ ጥሳ ፡ ትምጣ ፡ ብለው ፡ ከደን ፡ ውስጥ ፡ ጥለውኝ ፡ ሄዱን ።

ወ ፡ የሚረዳት ፡ ሰው ፡ ትጣ ፡ የምታደርገው ፡ መላ ፡ ቅጡ ፡ ይጥፋት ፡ ብለው ፡ ብቻዬን ፡ ያለሰው ፡ ያለረዳት ፡ ጥለውኝ ፡ በሞት ፡ ሄዱ ፤ ያሳዝናል ።

885 ዝም ፡ ብላችሁ ፡ ብሉ ፡ እንደ ፡ ተቻላችሁ ፤
—የለሁበት ፡ እኔ ፡ በዚህ ፡ አልጫችሁ ።

ሠ ፡ እናንተ ፡ የቻላችሁትን ፡ ያኽል ፡ ተመገቡ ፤ አልጫችሁን ፡ አልነካባችሁም ፤ በሱ ፡ መብላት ፡ አልፈቅድም ።

ወ ፡ ዐርፋችሁ ፡ ተቀመጡ ፤ እኔ ፡ በዚህ ፡ ነገር ፡ ለክፋም ፡ ሆነ ፡ ለደግ ፡ እግምት ፡ ላይ ፡ አላውላችሁም ፤ አላጫችሁም ።

886 ዝባድ ፡ ለመነገድ ፡ ከመውረድ ፡ መተማ ፡
—ዕጣኑ ፡ ይሻላል ፡ ለለት ፡ እራትማ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 772) ፡

ሠ ፡ ከመተማ ፡ ዝባድ ፡ እያመጡ ፡ ከመነገድ ፡ እዚሁ ፡ ሆኖ ፡ ዕጣን ፡ እየሸጡ ፡ የዕለት ፡ ጕርሥን ፡ ማግኘት ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ ነፍስን ፡ ለማዳን ፡ ክፉ ፡ ቀንን ፡ ለመውጣት ፡ ሲጨንቅ ፡ ሲጠብ ፡ ረኃብ ፡ የገዛ ፡ ልጅን ፡ ሥጋ ፡ ያስበላል ።

887 ዝናቡ ፡ ዘነበ ፡ ይሞላል ፡ ውሃው ፤
—አወይ ፡ ይህን ፡ ጊዜ ፡ ለተሻገረው ።

ሠ ፡ ደራሽ ፡ ውሃ ፡ ሳይመጣ ፡ ወንዙ ፡ ሳይሞላ ፡ ዥረቱን ፡ ይህን ፡ ጊዜ ፡ መሻገር ፡ ነበር ።

ወ ፡ ይህን ፡ መጥፎ ፡ ዘመን ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ታግሦ ፡ ከመልካም ፡ ጊዜ ፡ ከደኅና ፡ ሰዓት ፡ መድረስ ፡ ይበጃል ።

888 ዝናብ ፡ ዘነበ ፡ አሉ ፡ ያውም ፡ ማት ፡ በረዶ ፤
—ተሻገር ፡ ጐዣሜ ፡ ተሸጥ ፡ ወዲያ ፡ ማዶ ።

ሠ ፡ አንተ ፡ የጐዣም ፡ ሰው ፡ ብዙ ፡ ዝናብ ፡ ጥሏል ፤ ውሃ ፡ ሳይሞላብህ ፡ ሸጡን ፡ (ፈፋውን) ፡ አልፈህ ፡ ከማዶ ፡ ተሻገር ።

ወ ፡ ጐዣሜ ፡ ወደ ፡ ማዶ ፡ እየተወሰድህ ፡ መሸጥ ፡ አልቀረልህም ፤ የባርነት ፡ ቀንበር ፡ አልወረደልህም ።

889 ዝናቡ ፡ ዘነበ ፡ ደጁ ፡ ረሰረሰ ፤
—ቤት ፡ ያላችሁ ፡ ግቡ ፡ የኔ ፡ ቤት ፡ ፈረሰ ።

ሠ ፡ ታላቅ ፡ ዝናብ ፡ መጣ ፤ ቤት ፡ ያላችሁ ፡ ገብታችሁ ፡ ተጠለሉ ፤ ዝናብ፡ አይንካችሁ ፤ እኔ ፡ ቤቴ ፡ የፈረሰው ፡ መግቢያ ፡ ያጣሁት ፡ ዶፍ ፡ ቢወርድብኝም ፡ ግድ ፡ የለም ።

ወ ፡ ቤት ፡ ትዳር ፡ ያላችሁ ፡ ወደ ፡ አገራችሁ ፡ ግቡ ፤ እኔ ፡ ንብረቴ ፡ ፈርሷል ፤ ትዳሬ ፡ ቀርቷል ፤ አልመለስም ፤ እንደ ፡ ወጣሁ ፡ እቀራለሁ ።

890 የሐበሻን ፡ ጥቃት ፡ ውርደቱን ፡ ቢሰማ ፤
—በጣም ፡ ተቃጠለ ፡ ተናደደ ፡ ዲማ ።

ሠ ፡ የወገኑን ፡ የሐበሻን ፡ መጠቃት ፡ ቢሰማ ፡ ዲማ ፡ ደሙ ፡ ፈላ ፤ ትዕግሥቱ ፡ አለቀ ፤ እንደ ፡ እሳት ፡ ነደደ ፤ ጨሰ ፡ ተቃጠለ ።

ወ ፡ ዲማ ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ በእሳት ፡ ነደደ ፤ ተመዘበረ ፤ ጠፋ ፤ ከጠላት ፡ እጅ ፡ ወደቀ ።

891 የሑዳዴውስ ፡ ጦም ፡ ምንም ፡ አላለው ፤
—ሰው ፡ ሁሉ ፡ ያለቀው ፡ በማማቱ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በጾም ፡ በጣም ፡ የሚጐዳው ፡ በሕማማት ፡ ሰሞን ፡ ነው።

ወ ፡ የአዳም ፡ ልጅ ፡ ፈጣሪውን ፡ የሚበድለው ፡ ከነፍሱ ፡ የሚሳሳተው ፡ በሐሜት ፡ ነው ፤ የተፈጥሮ ፡ ወንድሙን ፡ የሚያሳዝነው ፡ አንደበቱ ፡ ስለማያርፍ ፡ ነው ።

892 የሆዴ ፡ መድኀኒት ፡ ለኔ ፡ እናቴ ፡ ነች ፤
—መድኀኒቱን ፡ ምሳ ፡ ታበላኛለች ።

ሠ ፡ ሆዴን ፡ ሲያመኝ ፡ ቍርጠት ፡ ሲነሣብኝ ፡ መድኀኒት ፡ የምትሰጠኝና ፡ የምትፈውሰኝ ፡ የገዛ ፡ እናቴ ፡ ነች ።

ወ ፡ ሲርበኝ ፡ ወስፋቴ ፡ እኽል ፡ ሲያሰኘው ፡ የምትመግበኝ ፡ ምሳዬን ፡ በጊዜ ፡ የምትሰጠኝ ፡ እምዬ ፡ ናት ።

893 የልጄን ፡ ገዳይ ፡ ትናንት ፡ አገኘሁት ፤
—አይቶኝ ፡ ቢደነግጥ ፡ ውሃ ፡ ቢሆን ፡ ተውኩት ።

ሠ ፡ ደመኛዬን ፡ አገኘሁትና ፡ ሲያየኝ ፡ ቢብረከረክና ፡ ቢርበደበድ ፡ ተውኩት ፤ ሳላሲዘው ፡ ቀረሁ ።

ወ ፡ የልጄ ፡ ገዳይ ፡ የማይከሰስ ፡ የማይወቀሥ ፡ ግዕዛን ፡ የሌለው ፡ ውሃ ፡ ሙላት ፡ ቢሆን ፡ የማደርገውን ፡ ባጣ ፡ እዬዬዬን ፡ ይገፎ ፡ ቀረሁ ፤ ሁሉንም ፡ ነገር ፡ ተውኩት ።

894 የሚያውቅበት ፡ ታጥቶ ፡ በደጋኑ ፡ ዐመል ፡
—አንተ ፡ ሠራህበት ፡ ደግነህ ፡ ጠቅል ።

ሠ ፡ በሴቶቹም ፡ ሞያ ፡ አለሁ ፡ ትላለህ ፤ የደጋኑን ፡ ዐመል ፡ አንተ ፡ ዐወቅ ህበት ፤ መንደፊያውን ፡ አቀናበርከው ።

ወ ፡ ግርማዊ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ አንተ ፡ ቸር ፡ ለጋስ ፡ ነህ ፤ ስንኳን ፡ ለወዳ ጅህ ፡ ለጠላትህ ፡ ደግ ፡ ነህ ፤ እግዚአብሔር ፡ በሰጠህ ፡ ሥልጣን ፡ ሠራህበት ፤ ሕዝብን ፡ አስተዳደርክበት ።

895 የሚጓዘው ፡ ሰንጋ ፡ የሚነዳው ፡ ሽሕር ፡ ለልደት ፡ ባይደርስ ፡
—እሱ ፡ ላም ፡ አርዶ ፡ ዋለ ፡ የሸዋው ፡ ንጉሥ ።　(እ ፡ ጣ) ፡

ሠ ፡ ሰንጋውና ፡ ሽሕሩ ፡ ስላልደረሰ ፡ ንጉሡ ፡ ላም ፡ አርዶ ፡ ልደትን ፡ አከበረ ።

ወ ፡ የሸዋው ፡ ንጉሥ ፡ የልደት ፡ ለት ፡ እስላሞችን ፡ ድል ፡ አድርጎ ፡ አስ ገበራቸው ፤ ሐረርን ፡ ያዘ ።

896 የማታውስ ፡ ዝናም ፡ ምንም ፡ አልጐዳኝ ፤
—ቀን ፡ ጥሎ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የደበደበኝ ።

ሠ ፡ የማታው ፡ ዝናም ፡ አላገኘኝም ፤ የደበደበኝ ፡ ቀን ፡ የጣለው ፡ ነው ።

ወ ፡ የተደበደብኩትና ፡ የተንጓጠጥኩት ፡ ጊዜ ፡ ቢጥለኝና ፡ ዘመን ፡ ቢያ ዋርደኝ ፡ ነው ።

897 የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ የኋላው ፡ ኵነኔ ፡
—ኮራ ፡ ብዬ ፡ ሄጄ ፡ እሞታለሁ ፡ እኔ ።

ሠ ፡ መሞቴ ፡ ካልቀረ ፡ ተንቀባርሬ ፡ የልቤን ፡ ሠርቼ ፡ እሞታለሁ ፤ ባለኝ ፡ ገንዘብ ፡ እደሰትበታለሁ ።

ወ ፡ ሞት ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ ኮራ ፡ ገዳም ፡ ገብቼ ፡ ፈጣሪ ዬን ፡ አገልግዬ ፡ ለነፍሴ ፡ የሚበጃትን ፡ ሠርቼ ፡ እሞታለሁ ።

898 የምትገዙ ፡ ሰዎች ፡ ያውና ፡ ቦታችን ፤
—ማዘን ፡ በያይነቱ ፡ ሞልቷል ፡ በቤታችን ።

ሠ ፡ በኛ ፡ ቤት ፡ ለቋሚ ፡ ለአግዳሚ ፡ የሚሆን ፡ ማእዘን ፡ በያይነቱ ፡ ይገ ኛል ፤ ለጣራ ፡ ለግድግዳ ፡ የሚሆን ፡ ዕንጨት ፡ አለ ።

ወ ፡ በቤታችን ፡ ማዘን ፡ መተከዝ ፡ የተለመደ ፡ ነው ።

899 የምትጠብቀኝ ፡ ገረዴ ፡ ነበረች ፤
—ምንም ፡ ሰው ፡ አልሆንም ፡ ቀን ፡ ጥላኝ ፡ ከሄደች ።

ሠ ፡ የምትረዳኝና ፡ ዐመሌን ፡ የምታውቅልኝ ፡ ገረዴ ፡ ቀን ፡ በቀን ፡ ጥላኝ ፡ ኰበለለች ፤ ምን ፡ ይበጀኛል ።

ወ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ በቤቴ ፡ የነበረው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ቀረ ፤ አዱኛ ፡ ብላሽ ፡ ሆነ ፤ ከዚያ ፡ ሁሉ ፡ ገንዘብ ፡ ባዶ ፡ እጄን ፡ ቀረሁ ።

900 የምትጠጡት ፡ ማኅበር ፡ ታቦቱ ፡ ማነው ፤
—ሙሴ ፡ ሙሴ ፡ ነወይ ፡ በወንበር ፡ ያለው ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡ የተቀመጡት ፡ የማኅበሩ ፡ አስተናባሪዎች ፡ ናቸው ፡ ወይ ።

ወ ፡ በወንበር ፡ ላይ ፡ የተቀመጡት ፡ ፈረንጅ ፡ ፈረንጆቹ ፡ ናቸው ፡ ወይ ።

901 የምን ፡ ዝምታ ፡ ነው ፡ አልልም ፡ ዝም ፡ ዝም ፡
—እሱም ፡ አለት ፡ ቀረ ፡ እኔም ፡ አለወንድም ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 353 ፡ 423) ፡

ሠ ፡ እሱ ፡ እኅቱን ፡ እኔም ፡ ወንድሜን ፡ አጣሁ ፤ ተለያይተን ፡ ቀረን ፤ ሁለተኛ ፡ ለመገናኘት ፡ ተስፋ ፡ የለንም ።

ወ ፡ እሱ ፡ ከአለት ፡ ድንጋይ ፡ ላይ ፡ ወድቆ ፡ የገደለው ፡ ሳይታወቅ ፡ ሞቶ ፡ ቀረ ፤ እኔም ፡ አንድ ፡ ወንድሜን ፡ በሞት ፡ አጣሁት ።

902 የሞት ፡ ሌብነቱን ፡ ማነው ፡ የማያውቅ ፤
—አይተነው ፡ የለም ፡ ወይ ፡ በፀሐይ ፡ ሲሰርቅ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ዐይን ፡ ባይን ፡ በቀን ፡ የሚሰርቅ ፡ ጭሉፋት ፡ ነው ፤ ለሌብነቱ ፡ አንድና ፡ ሁለት ፡ የለውም ፤ አገር ፡ ያወቀው ፡ ነው ።

ወ ፡ እንደ ፡ ሌባ ፡ ሳይታሰብ ፡ የሚመጣው ፡ ሞት ፡ በልዕልት ፡ ፀሐይ ፡ ላይ ፡ አደጋ ፡ መጣሉ ፡ ታወቀ ።

903 የሞትን ፡ ክፍታ ፡ ሁላችሁ ፡ ዕወቁ ፡
—ከሱ ፡ ቤት ፡ ይገኛል ፡ ብሩም ፡ ሆነ ፡ ወርቁ ።

ሠ ፡ ሰውየው ፡ እጅግ ፡ ሀብታም ፡ ነው ፤ ብሩ ፡ ወርቁ ፡ የሚገኘው ፡ ከሱ ፡ ቤት ፡ ነው ።

ወ ፡ «ብሩንና ፡ ወርቁን» ፡ ሞት ፡ ነጠቀኝ ፤ ብቻዬን ፡ ቀረሁ ።

904 የሠራሁት ፡ ቤቱ ፡ በጣም ፡ ሲስማማኝ ፤
—አሻቅቤ ፡ ባየው ፡ ጣሪያው ፡ በዛብኝ ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ቀና ፡ ብዬ ፡ ብመለከተው ፡ ባጡ ፡ ኰርቶ ፡ ጣራው ፡ ደርቶ ፡ አየሁት ።

ወ ፡ በሰጠኸኝ ፡ ጸጋ ፡ ሁሉ ፡ ተደስቼ ፡ ሳለሁ ፡ ተስፋ ፡ በማደርገው ፡ ልጄ ፡ ላይ ፡ ባደረው ፡ ጽኑ ፡ ሕመም ፡ (ጣር) ፡ የሚሰማኝ ፡ ጭንቅ ፡ ከባድ ፡ ሆነብኝ ።

905 የረኀብን ፡ ጊዜ ፡ መቻል ፡ ነው ፡ መክቶ ፡
—የጥም ፡ ጊዜ ፡ ብቻ ፡ አይቻልም ፡ ከቶ ።

ሠ ፡ የውሃን ፡ ጥም ፡ መታገሥ ፡ አይቻልም ፤ ሰውነትን ፡ እጅግ ፡ ያዝላል ፤ አንደበትን ፡ ያስራል ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሲጠም ፡ ተንኰል ፡ ሲያስብ ፡ ነገር ፡ ለማቃናት ፡ አስቸጋሪ ፡ ነው ።

906 የሩኤል ፡ ከተማ ፡ አንድ ፡ ብላ ፡ ታድሳ ፤
—ግቢ ፡ የትም ፡ የለ ፡ እንደነራስ ፡ ጉግሳ ። (1)

ሠ ፡ የራስ ፡ ጉግሳ ፡ አጥር ፡ ግቢ ፡ እጅግ ፡ ያምራል ፤ ቀያቸው ፡ ያለ ታል ።

ወ ፡ የራስ ፡ ጉግሳና ፡ የንግሥት ፡ ዘውዲቱ ፡ ጋብቻ ፡ እጅግ ፡ አማረ ፤ አስ ደሳች ፡ ሆነ ።

907 —የራስ ፡ ዐሊማ ፡ ጣት ፡ እጅግ ፡ ረዘመ ፤
ላየውም ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ በጣም ፡ አስገረመ ።

ሠ ፡ የራስ ፡ ዐሊ ፡ ጣት ፡ እጅግ ፡ ረዥም ፡ ነው ፤ አለንጋ ፡ ይመስላል ።

ወ ፡ ራስ ፡ ዐሊ ፡ እጅግ ፡ የሚያበሉት ፡ የሚያጠጡት ፡ እስከ ፡ ማጣት ፡ መድረሳቸው ፡ በጣም ፡ አስገረመ ።

908 የራስ ፡ ዐሊ ፡ አዳራሽ ፡ ያምር ፡ የነበረው ፡
—እልፍኙ ፡ ተከፍቶ ፡ ግቢው ፡ ፈርሶ ፡ አየነው ።

ሠ ፡ የራስ ፡ ዐሊ ፡ ቤት ፡ ቅጥረ ፡ ግቢው ፡ ፈርሶ ፡ ዐይነ ፡ ተኵላው ፡ ጠ ፍቶ ፡ አየነው ።

ወ ፡ ራስ ፡ ዐሊን ፡ ያኽል ፡ ሰው ፡ ቀን ፡ ቢጥላቸው ፡ አማቻቸው ፡ ከዷ ቸው ።

909 የራበው ፡ ካልበላ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይሆናል ፤
—ከዚያ ፡ ወዲያ ፡ ጦም ፡ ነው ፡ ማማት ፡ ይዠመራል ።

ሠ ፡ የአክፍለት ፡ ጊዜ ፡ ተቃርቧል ፤ ሰሙነ ፡ ሕማማት ፡ ይዠመራል ።

ወ ፡ እንግዲህ ፡ ማብላት ፡ ማጠጣት ፡ ከቀረ፤ ሰው፡ ማማትን፡ ይዠምራል።

910 የርብን ፡ ማዕበል ፡ ከሄደ ፡ አይመልሰው ፤
—ድርቅናው ፡ ምንድነው ፡ እንዳልወሰደ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ «ርብ» ፡ ዐይነ ፡ ደረቅ ፡ ነው ፤ ሰርቆ ፡ እንዳልሰረቀ ፡ ወስዶ ፡ እንዳል ወሰደ ፡ አላየሁም ፡ ይላል ፤ ያስተባብላል ።

ወ ፡ የርብ ፡ ወንዝ ፡ ሰው ፡ እንዳልወሰደ ፡ በሕዝብ ፡ ላይ ፡ ጕዳት ፡ እንዳላ ደረገ ፡ ሁሉ ፡ በጋ ፡ ሲመጣ ፡ ድርቅ ፡ ይላል ፤ ጥርኝ ፡ ውሃ ፡ አይገኝበ ትም ።

911 የሰው ፡ ልጅነትህ ፡ ከቀረ ፡ የሎዛው ፤
—መቼ ፡ ማግኘትህ ፡ ነው ፡ ልቤን ፡ የሚገዛው ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 666) ፡ (ወ ፡ ት ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ የምወድህና ፡ የማከብርህ ፡ ለጨዋ ፡ ልጅነት ህና ፡ ለደጉ ፡ ባሕርይህ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ለሀብትህ ፡ አይደለም ።

ወ ፡ ገንዘብና ፡ ማዕርግ ፡ በማግኘትህ ፡ ተታልዬ ፡ የበለጠ ፡ የምወድህ ፡ አይምሰልህ ።

---

(1) ራስ ፡ ጉግሳ ፡ ወሌ ፡ ወይዘሮ ፡ ዘውዲቱ ፡ ምኒልክን ፡ (በኋላ ፡ ንግሥት ፡ ነገሥታት ፡ ዘውዲቱን) ፡ ባገቡ ፡ ጊዜ ፡ ጋብቻው ፡ ታላቅና ፡ ተገቢ ፡ መሆኑ ፡ የተገለጠበት ።

912 የሰው ፡ ሁሉ ፡ አካል ፡ አድጎ ፡ አድጎ ፡ ያበቃል ፤
—የኔማ ፡ ጣት ፡ ጉድ ፡ ነው ፤ እንደ ፡ ገና ፡ ያድጋል ።

ሠ ፡ የኔ ፡ ጣት ፡ የሰው ፡ ሁሉ ፡ አድጎ ፡ ሲያበቃ ፡ እያደር ፡ እየረዘመ ፡ ይሄዳል ።

ወ ፡ የኔ ፡ ማጣት ፡ እያደር ፡ እየባሰ ፡ ይሄዳል ፤ ያልፍልኛል ፡ ስል ፡ በላይ ፡ በላዩ ፡ ይጨምራል ።

913 የሰው ፡ ሁሉ ፡ ጣቱ ፡ በልክ ፡ በልክ ፡ ያድጋል ፤
—የኔማ ፡ ጣት ፡ አድጎ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ በልጧል ።

ሠ ፡ የኔ ፡ ጣት ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ የበለጠ ፡ እጅግ ፡ የረዘመ ፡ ነው ፤ አለንጋ ፡ ይመስላል ።

ወ ፡ ችግሬ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ የበለጠ ፡ ሆነ ፤ ማጣቴ ፡ እየገፋ ፡ ሄደ ።

914 —የሰው ፡ መጨረሻ ፡ አቶሚክ ፡ ደጉ ፡ ሰው ፡
—ሁሉን ፡ አሳላፊ ፡ ነገር ፡ የማይከብደው ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፤

1 ሠ ፡ አቶሚክ ፡ በጣም ፡ ደግ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ እንደሱ ፡ ያለ ፡ ቸር ፡ ለጋስ ፡ የለም ፤ የሰው ፡ መጨረሻ ፡ ነው ።

ወ ፡ አቶሚክ ፡ ብዙ ፡ ሕዝብ ፡ የሚፈጅ ፡ ዓለምን ፡ የሚያጠፋ ፡ ከባድ ፡ መሣሪያ ፡ ነው ።

2 ሠ ፡ አቶሚክ ፡ እጅግ ፡ ታጋሽ ፡ ሆደ ፡ ሰፊ ፡ ነው ፤ ቢሰድቡት ፡ ክፉ ፡ ቢናገሩት ፡ አይከፋውም ።

ወ ፡ አቶሚክ ፡ የአዳምን ፡ ልጅ ፡ ከገጸ ፡ ምድር ፡ ለመደምሰስ ፡ የሚችል ፡ ጠንቀኛ ፡ መሣሪያ ፡ ነው ።

915 የሰውን ፡ ቤት ፡ ሁሉ ፡ ጨርሼ ፡ አየሁት ፤
—ግን ፡ እንደኛ ፡ የለም ፡ የተጣራ ፡ ቤት ።

ሠ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ የዘንድሮው ፡ ችግር ፡ ያገር ፡ ቢሆን ፡ እንደኛ ፡ የሚላስ ፡ የሚቀመስ ፡ የታጣበት ፡ ቤት ፡ አይገኝም ።

ወ ፡ ሞት ፡ በሁሉም ፡ ቤት ፡ ይገባል ፤ ግን ፡ እንደኛ ፡ ያጠቃው ፡ ዘር ፡ ያሳጣው ፡ የለም ።

916 የሰጡትን ፡ ዕቃ ፡ ቈጥሮ ፡ ካላኖረ ፡
—ታጣ ፡ ወዳጅነት ፡ ዘመድ ፡ መሆን ፡ ቀረ ።

ሠ ፡ ታማኝነት ፡ ከጠፋ ፡ አደራ ፡ ያስቀመጡትን ፡ ማጥፋትና ፡ መካድ ፡ ከመጣ ፡ ምን ፡ ዝምድና ፡ ተገኘ ፤ ወዳጅነትስ ፡ የት ፡ አለ ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሀብት ፡ ከሌለው ፡ ካጣ ፡ ከነጣ ፡ ወዳጅ ፡ ዘመድ ፡ የለውም ።

የሰጡኝን ፡ ጠላ ፡ አለ ፡ አኑሬዋለሁ ፤
የሰጡኝንም ፡ ጠጅ ፡ አለ ፡ አኑሬዋለሁ ፤
—በራሴ ፡ አዘንብዬ ፡ ባይኔ ፡ እቀዳዋለሁ ።

ሠ ፡ በጋን ፡ የሰጡኝን ፡ ጠጅ ፡ አዘንብዬ ፡ እየቀዳሁ ፡ እጠጣዋለሁ ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ የማለቅሰውና ፡ የማዝነው ፡ ለራሴ ፡ ስል ፡ ነው ፤ ወሮ ታዎ ውለታዎ ፡ ያንሰቀስቀኛል ፤ ያበሉኝ ፡ ጮማ ፡ አንገሮቴን ፡ ይበላ ቀል፡ ያጠጡኝ ፡ ጠጅ ፡ እንባ ፡ ሆኖ ፡ በዐይኔ ፡ ይኸው ፡ ይፈሳል ።

918 የሴቶች ፡ ሞያ ፡ ነው ፡ በልብህ ፡ ሳትል ፡
—ሰፍተህ ፡ እንድትኖር ፡ ለንጉሥ ፡ አገልግል ።　(በ ፡ ማ) ፡

ሠ ፡ ምንም ፡ የሴት ፡ ሞያ ፡ ቢሆን ፡ አንድ ፡ አገልግል ፡ ሰፍተህ ፡ ለንጉሡ ፡ ገጸ ፡ በረከት ፡ አቅርብ ፤ ማስታወሻ ፡ ብለህ ፡ ስጥ ።

ወ ፡ ከብረህ ፡ ገነህ ፡ ወግ ፡ ማዕርግ ፡ ደርሶህ ፡ ሥልጣን ፡ አግኝተህ ፡ እንድ ትኖር ፡ ተግተህ ፡ ለንጉሥ ፡ አገልግል ፤ በቅንነት ፡ በታዛዥነት ፡ ላገ ርህ ፡ ሥራ ።

919 የሸዋ ፡ መኳንንት ፡ እንግዲህ ፡ አትልፉ ፡
—ተመዞ ፡ የነበር ፡ ተከተተ ፡ ሰይፉ ።　(1)

ሠ ፡ ከአፎቱ ፡ ተመዞ ፡ የነበረው ፡ ሰይፍ ፡ ወደ ፡ ሰገባው ፡ ተመለሰ ፡ ከቦ ታው ፡ ገባ ።

ወ ፡ በሥልጣኑና ፡ በኀይሉ ፡ ከፍ ፡ ከፍ ፡ ብሎ ፡ አገሩን ፡ ሸዋን ፡ ይገዛ ፡ የነበረው ፡ ሰይፉ ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ ሞተ ፤ ተከተተ ፤ (ተቀበረ) ።

920 የሸዋ ፡ የጐዣም ፡ ተበትኖ ፡ ከብቱ ፡
የወሎ ፡ የትግሬ ፡ ተበትኖ ፡ ከብቱ ፡
—ገዛው ፡ አባ ፡ ታጠቅ ፡ ሰብስቦ ፡ በሀብቱ ።

ሠ ፡ አባ ፡ ታጠቅ ፡ የሕዝቡን ፡ ከብት ፡ በሙሉ ፡ ገዛው ፤ ላሙ ፡ በሬው ፡ የሚገኘው ፡ እሱ ፡ ቤት ፡ ብቻ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ አገሩን ፡ ጠቅሎ ፡ ገዛው ፡ ከዳር ፡ እስከ ፡ ዳር ፡ አስገበረው ።

921 የሽማግሌን ፡ ዕርቅ ፡ እሱ ፡ ከጠላው ፡
—በካሳ ፡ አስፈጥመህ ፡ ሥዩም ፡ አሽኘው ።　(ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ካሳ ፡ እንዲከፍል ፡ አስፈጥመህ ፡ ሸኘው ፤ አታውለው ፤ አታሳድረው ፤ ቶሎ ፡ አሰናብተው ።

ወ ፡ በራስ ፡ ካሳ ፡ ጭፍራ ፡ ጠላትን ፡ አስጨፍጭፈህ ፡ አስጨርሰው ፡ ድ ምጥማጡን ፡ አጥፍተህ ፡ አባረው ።

922 የቀድሞ ፡ ሌባዬ ፡ አመለጠኝ ፡ ደግሞ ፤
—ያውና ፡ እዚያ ፡ ማዶ ፡ ጋኔን ፡ ተሸክሞ ።

ሠ ፡ ከዚህ ፡ ቀደም ፡ ዕቃዬን ፡ የዘረፈ ፡ ሌባ ፡ ዛሬ ፡ ደግሞ ፡ ጋኔን ፡ ሰረቀ ፤ ያውና ፡ ተሸክሞት ፡ እዚያ ፡ ማዶ ፡ ይሮጣል ።

ወ ፡ የቀድሞ ፡ ጠላቴ ፡ ረድኤተ ፡ እግዚአብሔር ፡ ተለይቶታል ፤ የዛር ፡ ፈረስ ፡ ሆኖ ፡ ይኸው ፡ ይኖራል ፤ ጋኔን ፡ አድሮበት ፡ ይሟቀያል ።

---

(1) አቶ ፡ ሰይፉ ፡ የሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ ንጉሠ ፡ ሸዋ ፡ ልጅ ፡ አለሁ ፡ አለሁ ፡ ማለት ፡ ሲዠምሩ፡ ስለ ፡ ተገደሉ ፡ የርሳቸው ፡ ወገኖች ፡ የተናገሩት ፡ ቃል ፡ ነው ።

923 የቀረበው ፡ ጮማ ፡ ምንም ፡ ጣሙ ፡ ቢጥም ፡
—ያገራችን ፡ ጀግና ፡ ያላዋዜ ፡ አይቈርጥም ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ለቍርጥ ፡ የቀረበው ፡ ሥጋ ፡ ምንም ፡ ቢጣፍጥና ፡ ጮማ ፡ ቢሆን ፡ ያገሬ ፡ ጀግኖች ፡ ያለድቍስ ፡ አይበሉትም ፤ ያለአፍርንጅ ፡ አይቀምሱትም ፤ ያለአዋዜ ፡ አይመገቡም ።

ወ ፡ ምንም ፡ የጠላት ፡ ጦር ፡ አገራችንን ፡ ለመያዝ ፡ ቢመጣ ፡ አፈ ፡ ጉባኤ ያቸው ፡ የሆነውን ፡ አልዋዜን ፡ ለመቍረጥ ፡ ነው ፡ የሚጓጓው ።

924 የበለውን ፡ አባት ፡ የጐዠሙን ፡ ጥላ ፡
—በሽክም ፡ ወሰዱት ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ልበላ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ምን ፡ ላድርግ ፤ ምን ፡ ዐቅም ፡ አለኝ ፤ የበለውን ፡ አባት ፡ እንጠልጥለውት ፡ ሄዱ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ የጐዠሙ ፡ ባላባት ፡ ሞቶ ፡ ሬሳውን ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወሰዱት ፤ እንግዲህ ፡ ማን ፡ ያበላኝ ፡ ያጠጣኝ ፡ ይሆን ።

925 የባቡሩ ፡ መንገድ ፡ ጐዳናው ፡ ካለልህ ፡
—በሥርጥ ፡ ና ፡ ብሎ ፡ ማነው ፡ የመከረህ ።

ሠ ፡ አውራ ፡ ጐዳናውን ፡ ትተህ ፡ በስላች ፡ በግር ፡ መንገድ ፡ ና ፡ ያለህ ፡ ማነው ።

ወ ፡ በእስረኛ ፡ ላይ ፡ ልብህ ፡ ለምን ፡ አይራራም ፤ ማን ፡ ጨክን ፡ አለህ ። ፡

926 የቤተ ፡ክሲያን ፡ ሥራ ፡ ቀጠሮ ፡ አለብኝ ፤
—ዐፈር ፡ ለመሸከም ፡ እሄዳለሁኝ ።

ሠ ፡ ዐፈር ፡ ለማጋዝና ፡ ለቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ግንብ ፡ የሚሆን ፡ ጭቃ ፡ ለመርገጥ እሄዳለሁ ።

ወ ፡ በመቃብር ፡ ውስጥ ፡ ዐፈር ፡ በላዩ ፡ ላይ ፡ ሊመለስበት ፡ አስከሬኑ ፡ ወደ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተወሰደ ።

927 የተተካከለው ፡ ፍርድህ ፡ እንደ ፡ ሚዛን ፡
—ፈቅዳ ፡ ሰጥታሃለች ፡ በዘውዲቱ ፡ ግዛን ።

ሠ ፡ ፍርድህ ፡ የማይዛባው ፡ ንጉሥ ፡ ተፈሪ ፡ በዘውዲቱ ፡ ሞት ፡ ግዛን ፡ ጠብቀን።

ወ ፡ መርቃ ፡ ፈቅዳ ፡ በሰጠችህ ፡ በንጉሥነትህ ፡ ሥልጣን ፡ በመንግሥት ፡ ዘውዲቱ ፡ ስም ፡ አስተዳድረን ።

928 የተወራው ፡ ወሬ ፡ እውነት ፡ ሆኖ ፡ እንደሆን ፡
—ቤቴ ፡ ከመንገድ ፡ ዳር ፡ አለወንድም ፡ አይሆን ።

ሠ ፡ የምኖረው ፡ ከመንገድ ፡ ዳር ፡ ነው ፤ ይህ ፡ የሚሰማው ፡ ወሬ ፡ ርግጥ ፡ ከሆነ ፡ ወንድ ፡ ከሌለበት ፡ ቤቴ ፡ ያስፈራል ።

ወ ፡ ጥቃቴን ፡ የሚወጣልኝ ፡ ማስፈራሪያ ፡ የሚሆነኝ ፡ ወንድሜን ፡ ካጣሁ ፡ ቤቴ ፡ ንብረቴ ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

929 የተጠበሰ ፡ ዓሣ ፡ ይሸታል ፡ እጃችሁ ፡
—እረ ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ዓሣማበላችሁ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 700) ፡

ሠ ፡ እናንተ ፡ ሰዎች ፡ ዓሣ ፡ ዓሣ ፡ ትሸታላችሁ ፤ ለመሆኑ ፡ ማነው ፡ የተጠበሰ ፡ ዓሣ ፡ ያበላችሁ ።

ወ ካባታችሁ ፡ ልምድ ፡ ያልቈየላችሁን ፡ ዐሣማ ፡ ትበሉ ፡ ዠመርን ፤ ያገራችሁን ፡ ሥርዐትና ፡ ልምድ ፡ ለምን ፡ ተዋችሁት ።

930 የታጠቅ ፡ ጐራዴ ፡ ብረት ፡ የነበረ ፡
—እየቀላ ፡ ሄደ ፡ ደም ፡ እየመሰለ ።

ሠ ፡ ነጭ ፡ የነበረው ፡ የታጠቅ ፡ ጐራዴ ፡ ፍላት ፡ የገባ ፡ ይመስል ፡ ይቀላ ፡ ዠመር ፤ ደም ፡ እየመሰለ ፡ ሄደ ።

ወ ፡ የታጠቅ ፡ ሰይፍ ፡ በደም ፡ ተለወሰ ፤ የጠላቱን ፡ አንገት ፡ እየቀነጠሰና ፡ እየቀላ ፡ ጣለው ።

931 የትም ፡ ልሂድ ፡ ተዉኝ ፡ እያለ ፡ ቢያስቸግር ፡
—በቀላድ ፡ ታሰረ ፡ ያ ፡ ብርቱ ፡ ወታደር ።

ሠ ፡ ልብረር ፡ እያለ ፡ ቢያስቸግር ፡ ወታደሩን ፡ በገመድ ፡ አስረው ፡ አስቀመጡት ።

ወ ፡ ወታደሩን ፡ ቀላድ ፡ መሬት ፡ ሰጥተው ፡ አስቀመጡት ፤ ትዳር ፡ አስያዙት ።

932 የትናንቱ ፡ ችሎት ፡ ምንም ፡ አላማረ ፤
—ሕዝቡ ፡ ተበድሎ ፡ ያለ ፡ ካሳ ፡ ዋለ ። (ስለ ፡ ልዑል ፡ ራስ ፡ ካሳ) ፡

ሠ ፡ ሕዝቡ ፡ ተጠቅቶና ፡ ተደብድቦ ፡ ካሳ ፡ ሳይቀበል ፡ ቀረ ፤ የደም ፡ ዋጋ ፡ ሳያገኝ ፡ ወደ ፡ ቤቱ ፡ ገባ ።

ወ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ በራስ ፡ ካሳ ፡ መሞት ፡ አዘነ ፤ አማላጅ ፡ የነበሩትን ፡ መስፍን ፡ አጣ ።

933 የት ፡ አኑሮት ፡ ኖሯል ፡ ያንን ፡ ቊናውን ፤
—ሰፍሮ ፡ ተቀበለው ፡ ጋላ ፡ ብድሩን ። (1)

ሠ ፡ ጋላ ፡ ያበደረውን ፡ እኽል ፡ በሰፈረበት ፡ ቊና ፡ ሰፍሮ ፡ ለክቶ ፡ ተቀበለ ፤ የሰጠውን ፡ እኽል ፡ ተከፈለ ።

ወ ፡ የጋላ ፡ ወገን ፡ ቂሙን ፡ ተወጣ ፤ ብድሩን ፡ መለሰ ።

934 የችኩል ፡ ቤት ፡ ሠሪ ፡ መፍረሱን ፡ እያየው ፡
—በማገር ፡ ላይ ፡ ቆሞ ፡ እንዴት ፡ ይወጣል ፡ ሰው ።

ሠ ፡ እንዴት ፡ አእምሮ ፡ ያለው ፡ ሰው ፡ ማገር ፡ እየረገጠና ፡ እየያዘ ፡ ወደ ፡ ጣራ ፡ ይወጣል ፤ ይፈርሳል ፡ ብሎ ፡ አያስብምን ።

ወ ፡ ማን ፡ በሚገዛው ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ተቀምጦ ፡ ይኰራል ፤ ንጉሥ ፡ ሲጠራው ፡ ያልመጣው ፡ በምን ፡ ተመክቶ ፡ ኰሪቶ ፡ ነው ።

---

(1) የንጉሥ ፡ ተክለ ፡ ሃይማኖት ፡ ሰው ፡ ድል ፡ ሆኖ ፡ ከእምባቦ ፡ ዘመቻ ፡ ወዳገሩ ፡ ሲመለስ ፡ ጋላ ፡ በየመንገዱ ፡ እያሸመቀ ፡ ስለ ፡ ፊጃቸው ፡ የጐዣም ፡ አልቃሽ ፡ የገጠመችው ።

935 የነበርሁበቱ ፡ ትዝ ፡ ትዝ ፡ አለኝ ፤
—አኳኋኔ ፡ ጠፋኝ ፤ እረ ፡ ማን ፡ አሉኝ ። (ራስ ፡ ዐ) ፡

ሠ ፡ ችግር ፡ ነበርን ፡ አስረሳኝ ፤ ራሴን ፡ አስዘነጋኝ ።

ወ ፡ እኔ ፡ መሆኔን ፡ አጣሁት ፤ የነበረኝን ፡ ክብርና ፡ ማዕርግ ፡ አስቦ ፡ መረዳት ፡ ተሳነኝ ፤ መላ ፡ ቅጡ ፡ ጠፋኝ ፤ ለመሆኑ ፡ ሰዎች ፡ ማን ፡ ይሉኝ ፡ ነበር ፤ ስሜ ፡ ይታወሳችኋልን ።

936 የናት ፡ አገር ፡ ቀሚስ ፡ ያባት ፡ አገር ፡ ሸማ ፡
—ነጠላ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ የሰው ፡ አገርማ ።

ሠ ፡ በሰው ፡ አገር ፡ የሚለበሰው ፡ ለሰውነት ፡ የማይሞቅ ፡ ለትከሻ ፡ የማይደምቅ ፡ ነጠላ ፡ ነው ፤ በሚወለዱበት ፡ አገር ፡ የሚለበሰው ፡ ዕጥፍ ፡ የሆነ ፡ ጋቢና ፡ ቀሚስ ፡ ነው ።

ወ ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ተዝናንቶ ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ ለመኖር ፡ አይቻልም ፤ ሊተማመኑበትና ፡ ሊመኩበት ፡ አይገባም ፤ በሰው ፡ አገር ፡ መኖር ፡ ያስጠቃል ፤ ያዋርዳል ፤ አንገትን ፡ ደፍቶ ፡ ተሸቈጥቍጦ ፡ እንዲኖሩ ፡ ያስፈልጋል ።

937 የናቴ ፡ አገር ፡ ገረን ፡ እንሳሮ ፡ ያባቴ ፡ የኔ ፡ መርሐቤቴ ፡
—ዠማ ፡ ተጣጥቤ ፡ ልገባ ፡ ነው ፡ ቤቴ ።

ሠ ፡ በዠማ ፡ ውሃ ፡ ገላዬን ፡ ታጥቤ ፡ ሰውነቴን ፡ ተለቃልቄ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ መግባቴ ፡ ነው ።

ወ ፡ በተወለድኩበት ፡ አገር ፡ ባደግሁበት ፡ ወንዝ ፡ ያለ ፡ የሌለኝን ፡ ወንበዴ ፡ ነጥቆኝ ፡ ሸፍታ ፡ ዘርፎኝ ፡ ባዶ ፡ እጄን ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ መሄዴ ፡ ነው ።

938 የኔም ፡ እኅት ፡ አንቺ ፡ ያንቺም ፡ ወንድም ፡ እኔ ፤
—ምን ፡ መጠቅለያ ፡ አለው ፡ ይህ ፡ አለምናኔ ።

ሠ ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ ጥሎ ፡ ከመሄድና ፡ መንኖ ፡ ገዳም ፡ ከመግባት ፡ በቀር ፡ የሚበጅ ፡ የለም ፤ ቢለፉ ፡ ቢወጡ ፡ ቢወርዱ ፡ አይሞላም ።

ወ ፡ የዚህ ፡ ዓለምና ፡ የኔ ፡ ነገር ፡ ፍጻሜው ፡ ምን ፡ ይሆን ፤ ወየው ፡ መጨረሻችንን ፡ ላየው ፡ ሰው ።

939 የኔታ ፡ ደጃዝማች ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ደግነት ፡
—ዛሬ ፡ እንኳን ፡ ለሕዝቡ ፡ እንባ ፡ አተረፉለት ። (1)

ሠ ፡ ደጃዝማች ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ያው ፡ ናቸው ፤ የርሳቸው ፡ ደግነት ፡ ዘመን ፡ አይሽረውም ፤ ጊዜ ፡ አይለውጠውም ።

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ሕዝቡን ፡ ባስፈጁት ፡ ጊዜ ፡ ዘመድ ፡ ወዳጅ ፡ ለቅሶ ፡ እንዳያደርግ ፡ በብርቱ ፡ ተከልክሎ ፡ ነበር ፡ ይባላል ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ሞት ፡ የማይገባበት ፡ ቤት ፡ ስለሌለ ፡ የሚስታቸው ፡ አባት ፡ ደጃዝማች ፡ ውቤ ፡ ሞቱ ፤ በዚያ ፡ ጊዜ ፡ ሕዝቡ ፡ እንዲያለቅስላቸው ፡ አዘዙ ፤ ይህንንም ፡ ምክንያት ፡ በማድረግ ፡ ውጦት ፡ የነበረውን ፡ እንባ ፡ በየደጁ ፡ እየተሰበሰበ ፡ አፈሰሰ ፤ የደጃች ፡ ውቤ ፡ ገረድም ፡ ሁናቴውን ፡ አይታ ፡ ይህነን ፡ ግጥም ፡ ገጠመች ።

ወ ፡ ሞታቸው ፡ እንኳ ፡ ደግ ፡ ነገር ፡ ሠራ ፤ እንዳያለቅስ ፡ ተከልክሎ ፡ የነበረው ፡ ሕዝብ ፡ የርሳቸውን ፡ ዕረፍት ፡ ሰበብ ፡ በማድረግ ፡ እር ሙን ፡ አወጣ ፤ በዐይኑ ፡ ላይ ፡ አቅርሮ ፡ የነበረው ፡ እንባውን ፡ በም ክንያት ፡ አፈሰሰ ።

940 የኔንስ ፡ ባገሬ ፡ ሠራልኝ ፡ ባለጅ ፤
—ተጋላ ፡ የመጣች ፡ ያዳል ፡ ጦር ፡ ናት ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ የአዳል ፡ ጦር ፡ ከጋላ ፡ ተገዝታ ፡ የመጣች ፡ ናት ፤ እዚያው ፡ የተሠ ራች ፡ አይደለችም ።

ወ ፡ ሰው ፡ የፈጀች ፡ ሕዝብ ፡ የገደለች ፡ እየገፋች ፡ የመጣች ፡ የአዳል ፡ ጦር ፡ ናት ።

941 የንጉሥ ፡ አሽከር ፡ ጠፍቶ ፡ ሲፈለግ ፡ ሌሊት ፡
—ቀን ፡ ከተድላ ፡ ጋራ ፡ ሲሄድ ፡ አየሁት ። (1)

ሠ ፡ ንጉሡን ፡ ከድቶ ፡ ኰብሎ ፡ የጠፋው ፡ አሽከር ፡ ሳይፈራ ፡ ቀን ፡ በቀን ፡ ከተድላ ፡ ጋራ ፡ ሲሄድ ፡ አየሁት ።

ወ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ ማግኘት ፡ ዓለም ፡ ማየት ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ መደሰት ፡ ከደ ጃዝማች ፡ ተድላ ፡ ጋራ ፡ አብሮ ፡ ቀረ ፤ እሳቸው ፡ ሲሞቱ ፡ ሁሉም ፡ ነገር ፡ እንዳልነበረ ፡ ሆነ ።

942 የኛ ፡ ቤተ ፡ ሰቦች ፡ እዬዬ ፡ ብላችሁ ፡ ዋይ ፡ በሉና ፡ አልቅሱ ፤
አባባ ፡ ሄደዋል ፡ እንግዲህ ፡ ዕወቁት ፡ እንዳይመለሱ ።

ርኅሩኅ ፡ ሰው ፡ ወዳጅ ፡ አይጠና ፡ አንዠታቸው ፤
—አባባ ፡ በውነቱ ፡ ያባት ፡ አባት ፡ ናቸው ። (2) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 76) ፡
(ናርዶስ ፡ ማ ፡ ሥ) ፡

ሠ ፡ አባትነታቸው ፡ ርኅራኄና ፡ አዛኝነት ፡ የተመላበት ፡ ነበር ፤ ለልጆቻ ቸው ፡ እንደ ፡ እናት ፡ አንዠታቸው ፡ ወላላና ፡ ርግብግብ ፡ ነበር ።

ወ ፡ እኚህ ፡ ዛሬ ፡ የሞቱት ፡ ታላቅ ፡ ሰው ፡ ያባቴ ፡ አባት ፡ አያቴ ፡ ናቸው ።

943 የአዳ ፡ ገብረ ፡ ማርያም ፡ ልቅሶው ፡ የጠፋችሁ ፡
—የደጋን ፡ ሲፈታ ፡ ታገኙታላችሁ ።

ሠ ፡ የገብረ ፡ ማርያም ፡ የልቅሶው ፡ ውሎ ፡ የሚደረግበትን ፡ ቦታ ፡ የማታው ቁት ፡ ሰዎች ፡ የደጋን ፡ ከሚባለው ፡ ስፍራ ፡ ብትሄዱ ፡ ታገኙታላችሁ ።

ወ ፡ አገር ፡ አስተዳዳሪ ፡ ሕዝብ ፡ ሰብሳቢ ፡ የነበረው ፡ ገብረ ፡ ማርያም ፡ በመሞቱ ፡ የደጋን ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ጠፍቶ ፡ ሕዝቡ ፡ ተበትኖ ፡ ተወላጁ ፡ ተሰዶ ፡ ታዩታላችሁ ።

---

(1) በጐዣም ፡ ደብረ ፡ ወርቅ ፡ በሚባል ፡ ደብር ፡ ይኖር ፡ የነበረ ፡ ፩ ፡ ካህን ፡ ከመኳንንቶቻ ቸው ፡ እኩል ፡ አድርገው ፡ ያከብሩት ፡ የነበሩት ፡ ደጃዝማች ፡ ተድላ ፡ ከሞቱ ፡ በኋላ ፡ ኈስቍልናና ፡ ውርደት ፡ ስለ ፡ ደረሰበት ፡ በጸጸት ፡ የተናገረው ።

(2) ጸሓፌ ፡ ትእዛዝ ፡ ወልደ ፡ መስቀል ፡ ባረፉ ፡ ጊዜ ፡ የልጅ ፡ ልጃቸው ፡ ናርዶስ ፡ ማኅ ተመ ፡ ሥላሴ ፡ አያቷ ፡ ካባትም ፡ አባት ፡ ርኅሩኅ ፡ መሆናቸውን ፡ የገለጸችበት ።

944 የአገራችን ፡ ሰው ፡ እኽል ፡ ነበር ፡ ምግቡ ፤
—አሁን ፡ ባንተ ፡ ግብር ፡ ወተት ፡ አለ ፡ ሕዝቡ ።

ሠ ፡ ወተት ፡ ጠጥቶ ፡ የላም ፡ ልጅ ፡ አይቶ ፡ የማያውቅ ፡ ሁሉ ፡ አሁን ፡ ባንተ ፡ ድግስ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ ወተት ፡ አምጡ ፡ ባይ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ አንተ ፡ ባመጣኸው ፡ ጦስ ፡ ሕዝቡ ፡ ይንገላታ ፡ ይንከራተትና ፡ አገር ፡ ላገር ፡ ይዋትት ፡ ዠመር ፤ መቆሚያ ፡ መቀመጫ ፡ አጣ ።

945 የእግዚአብሔር ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የኔ ፡ አይደል ፡ ጉልበቱ ፤
—እንዲያው ፡ እንባ ፡ አነቀኝ ፡ ከተቀመጥኩቱ ።

ሠ ፡ የጠገበ ፡ ጉልበተኛ ፡ ሳልደርስበት ፡ ቢናገረኝ ፡ እልኽ ፡ ያዘኝና ፡ እንባ፡ አነቀኝ ፤ አለቀስኩ ።

ወ ፡ በኀይሉ ፡ ተመክቶ ፡ ምንም ፡ ሳልበድለው ፡ እተቀመጥኩበት ፡ መጥቶ ፡ አነቀኝ ፤ ጉልበቱን ፡ ፈተነብኝ ።

946 የካቲት ፡ ሚካኤል ፡ መቼ ፡ ተከበረ ፤
—ዶማ ፡ ይዞ ፡ ዋለ ፡ ሰው ፡ እየቈፈረ ። (መሸሻ ፡ ግዛው) ፡

ሠ ፡ የየካቲት ፡ ሚካኤል ፡ ሳይከበር ፡ ዋለ ፤ ሲታረስ ፡ ሲታጨድ ፡ ነበር ፤ ሰው ፡ እየቈፈረ ፡ በዓሉን ፡ ሻረው ።

ወ ፡ በየካቲት ፡ ሚካኤል ፡ አደጋ ፡ ሕዝቡ ፡ በአካፋ ፡ በዶማ ፡ ተጨፈጨፈ፤ ብርቱ ፡ ሥቃይ ፡ አየ ፤ አሰቃቂ ፡ የሆነ ፡ ውርደት ፡ ደረሰበት ፤ ታላቅ ፡ ግፍ ፡ ተዋለበት ።

947 የካቲት ፡ ዐርብ ፡ ቀን ፡ ሆኖ ፡ ሚካኤል ፡ (1) (መሸሻ ፡ ግዛው) ፡
—ምሣር ፡ ይዘው ፡ ዋሉ ፡ ሥራ ፡ ይመስል ።

ሠ ፡ የበዓሉን ፡ ቀን ፡ ሥራ ፡ አድርገው ፡ ዋሉ ፤ ሳያከብሩት ፡ ቀሩ ፤ ሲሠሩበት ፡ ታዩ ።

ወ ፡ የየካቲት ፡ ሚካኤል ፡ ለት ፡ ፋሽስት ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሕዝብ ፡ በምሣር ፡ እንደ ፡ ዕንጨት ፡ እየፈለጠ ፡ በሰይፍ ፡ በጐራዴ ፡ ፈጀው ።

948 የክንፉ ፡ አዳም ፡ ፈረስ ፡ ኀመሩ ፡ ግልገሉ ፡
—ገና ፡ ሁለት ፡ ሽረፍ ፡ አላደረሰ ፡ አሉ ።

ሠ ፡ የክንፉ ፡ ፈረስ ፡ ግልገል ፡ ነው ፤ ገና ፡ የመዠመሪያ ፡ ጥርሱ ፡ አልተሸረፈም ።

ወ ፡ ጀግናው ፡ ክንፉ ፡ አዳም ፡ በፈረስ ፡ ዘምቶ ፡ «አላ» ፡ ከሚባለው ፡ ስፍራ ፡ ደርሶ ፡ ወግቶ ፡ ድል ፡ አድርጎ ፡ ተምኾ ፡ መቶት ፡ ተመለሰ ።

949 የወትሮው ፡ ጉልበትህ ፡ ጋሻህ ፡ አለ ፡ ብዬ ፡
—እኔ ፡ አስደበደብኩህ ፡ ውብዬ ፡ ውብዬ ።

---

(1) ባ፲፱፻፳፱ ፡ ዓ ፡ ም ፡ የካቲት ፡ ፲፪ ፡ ቀን ፡ የሚካኤል ፡ ለት ፡ ግራዚያኒ ፡ በቦምብ ፡ በተመታ ፡ ጊዜ ፡ ፋሽስቶች ፡ የኢትዮጵያን ፡ ሕዝብ ፡ አሰቃቂ ፡ የሆነ ፡ ግፍ ፡ እንደ፡ ሠሩበት ፡ የሚገልጽ ።

ሠ ፡ ቍቋታዬን ፡ ሰምተህ ፡ እኔን ፡ ለመገላገልና ፡ ለማዳን ፡ መጥተህ ፡ ተደ
በደብህ ፤ በገዛ ፡ እጇ ፡ ወንድሜን ፡ አስጠቃሁህ ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ ውቤ ፡ የኔን ፡ ጥቃት ፡ ለመወጣት ፡ ስትል ፡ ሞተህ ፡ ቀረህ፤
ለኔ ፡ ስትል ፡ ሕይወትህን ፡ አሳለፍህ ።

950 የወንዱ ፡ መሣሪያ ፡ ተሸጠ ፡ መኔቻ ፡
—እንደ ፡ ምን ፡ ይቀራል ፡ የሴቱ ፡ ጕትቻ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የወንዱ ፡ መሣሪያ ፡ መኔቻ ፡ ሲሸጥ ፡ ሲለወጥ ፡ ለምን ፡ የሴቱ ፡ ጌጥ ፡
ድሪና ፡ ጕትቻው ፡ ይቀራል ።

ወ ፡ ከሴት ፡ መጓተቱ ፡ ከቶ ፡ እንዴት ፡ ይቀራል ።

951 የወደቀ ፡ ማንሣት ፡ ንጉሥ ፡ ያውቁ ፡ ነበር ፡
—ጕኑ ፡ ሳይወጋ ፡ ፊቱ ፡ ሳይሰበር ።

ሠ ፡ ከጦርነት ፡ ላይ ፡ ጐኑ ፡ ሳይደቅ ፡ ፊቱ ፡ ሳይሠረጕድ ፡ ጕዳት ፡ ሳይደ
ርስበት ፡ ንጉሡ ፡ ወታደሩን ፡ ያስነሡት ፡ ነበር ።

ወ ፡ የሰው ፡ ፊት ፡ ሳይገርፈው ፤ አደባባይ ፡ ሳያየው ፡ ንጉሡ ፡ ሕዝባቸ
ውን ፡ አስቀድመው ፡ ይደጕሙት ፡ ነበር ፤ ከችግር ፡ ላይ ፡ ሲወድቅም ፡
ያነሡት ፡ ነበር ።

952 የወዲያውን ፡ ቅጠል ፡ አናውቀውምና ፤
—ራስ ፡ ወሰን ፡ ሰገድ ፡ አሳየን ፡ ብሳና ።

ሠ ፡ እዚያ ፡ ማዶ ፡ ያለውን ፡ ቅጠል ፡ ምን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አናውቅምና ፡ ራስ ፡
ወሰን ፡ ሰገድ ፡ ብሳናው ፡ የቱ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ለይተህ ፡ አሳየን ።

ወ ፡ ራስ ፡ ወሰን ፡ ሰገድ ፡ ጦሩን ፡ ወግተህ ፤ ድል ፡ ነሥተህ ፡ ወሰኑን ፡ አል
ፈህ ፡ አሳየን ።

953 የዕድሌ ፡ ክፋቱ ፡ ፈተና ፡ አብዝቶብኝ ፡
—እዩት ፡ አየለና ፡ ኀይሌን ፡ ወሰደብኝ ። (1) (ወ ፡ ሠ ፡ ኀ)፡

ሠ ፡ ሰዎች ፡ እስቲ ፡ ፍረዱኝ ፤ የዕድሌ ፡ ክፋት ፡ ፈተና ፡ አብዝቶብኝ ፡
ኀይሌ ፡ ስለ ፡ ተቀነሰ ፡ ነጥቆ ፡ ወሰደብኝ ።

ወ ፡ ጨካኙ ፡ ሞት ፡ ወንድሜን ፡ አየለንና ፡ አባቴን ፡ ኀይሌን ፡ ወሰደብኝ ፤
አለኝታዎቼን ፡ ነጠቀኝ ፤ ያለአባትና ፡ ያለወንድም ፡ አስቀረኝ።

954 የዘመዶቼን ፡ ቤት ፡ ምነው ፡ አላድነው ፤
—ያክሥቴ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ የሚለበለበው ።

ሠ ፡ ያክሥቴን ፡ ቤት ፡ ሲያቃጥል ፡ እንዴት ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ አያለሁ ፤ ሄጄ፡
አላጠፋም ፤ ለምን ፡ ዝም ፡ ብዬ ፡ እመለከታለሁ ።

ወ ፡ ያ ፡ ጠላት ፡ በእሳት ፡ የሚያቃጥለው ፡ የሚዘርፈውና ፡ የሚበዘብዘው ፡
«ክስቴ» ፡ የሚባለው ፡ አይደለም ፡ ወይ ።

---

(1) ወይዘሮ ፡ ሠናይት ፡ ኀይሌ ፡ ወንድማቸው ፡ ልጅ ፡ አየለ ፡ ኀይሌና ፡ አባታቸው ፡ ጸሓፌ ፡
ትእዛዝ ፡ ኀይሌ ፡ ወልደ ፡ ሩፌ ፡ በሞት ፡ በመለየታቸው ፡ የተሰማቸውን ፡ ጥልቅ ፡ ሐ
ዘን ፡ የገለጹበት ።

955 የዚህ ፡ ዓለም ፡ ፍጥረት ፡ ሁሉ ፡ በሽተኛ ፤
—ተስቦ ፡ መጣና ፡ እንዲህ ፡ አረገኛ ።

ሠ ፡ እቤቴ ፡ ተስቦ ፡ ገብቶ ፡ ዘመዶቼን ፡ ፈጀብኝ ፤ ብቻዬን ፡ አስቀረኝ ፤ እንዲህ ፡ ድኻ ፡ አደረገኝ ።

ወ ፡ ሲሳብ ፡ ሲጐተት ፡ መጥቶ ፡ እንዲህ ፡ ጉድ ፡ አድርጎኝ ፡ ሄደ ፤ የዋህ ፡ መስሎ ፡ ገብቶ ፡ የማታለል ፡ ሥራ ፡ ሠርቶ ፡ ተመለሰ ።

956 የዚያ ፡ ማዶ ፡ ሰዎች ፡ አያምራቸው ፡ ምንጣፍ ፡ አያምራቸው ፡ ነት ፤
—ያማሴን ፡ የኛ ፡ ነው ፡ ፊት ፡ የወሰዱት ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ እነዚያ ፡ ሰዎች ፡ ምንጣፍ ፡ ቍርበት ፡ የላቸውም ፤ የወሰዱትም ፡ ማስ፡ የኛ ፡ ነው ።

ወ ፡ ጣሊያኖች ፡ አገራችንን ፡ የሚመለከቱት ፡ ከቀድሞ ፡ ዠምሮ ፡ ነው ፤ ያ ፡ የወሰዱት ፡ ሐማሴንም ፡ የኛ ፡ አገር ፡ ነው ።

957 የዛሬ ፡ ቤተ ፡ ክሲያን ፡ በጣም ፡ ረከሰ ፤
—አራሲቱ ፡ ገባች ፡ ደሟ ፡ እየፈሰሰ ።

ሠ ፡ እመጫቷ ፡ ደሟ ፡ ሳይነጥፍ ፡ እቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ገባች ፤ ቤተ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አጐደፈች ።

ወ ፡ ሴቲቱ ፡ በወሊድ ፡ ሞተች ፤ በደም ፡ እንደ ፡ ተጨበጠች ፡ ዐረፈች ፤ ባሳዛኝ ፡ ሁኔታ ፡ ሕይወቷ ፡ አለፈ ።

958 የዛሬ ፡ ዘመን ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ አትርሱኝ ፡ ባይ ፤
—ካዘንኩማ ፡ ራሴን ፡ አላድንም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ለሰው ፡ ከመጸለይ ፤ ትሩፋት ፡ ካለኝ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ሰው ፡ ከሆንኩ ፡ ለምን ፡ መዠመሪያ ፡ ራሴን ፡ አላድንም ፤ ነፍሴን ፡ አላተርፍም ።

ወ ፡ ጾም ፡ ጸሎት ፡ ሐዘን ፡ ትካዜ ፡ ሰውን ፡ ከሞት ፡ የሚያስቀር ፡ ቢሆን ፡ ኖሮ ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ድካሜ ፡ ጌታዬን ፡ ራስን ፡ ያድንልኝ ፡ ነበር ፤ ግን ፡ ሞት ፡ የማይቀር ፡ ሕግ ፡ በመሆኑ ፡ ሊተርፉ ፡ አልቻሉም ።

959 የዠጋ ፡ ወይዘሮ ፡ የስናን ፡ ወይዘሮ ፡ ያስቀምጧል ፡ እንጂ ፡ ቅልን ፡ ተጠንቅቆ ፤
—ደረቁን ፡ በላነው ፡ ያ ፡ ሁሉ ፡ ጨው ፡ አልቆ ።

ሠ ፡ መበያ ፡ ጠፍቶ ፡ ጨው ፡ በርበሬ ፡ ታጥቶ ፤ ደረቁን ፡ እንጀራ ፡ በልተን ፡ መጣን ።

ወ ፡ ደኅና ፡ ደኅናው ፡ ሰው ፡ በሞት ፡ አለቀና ፡ ባገራችን ፡ ሽማግሌ ፡ ጠፋ፤ ሰው ፡ የሚያስታርቅ ፡ ታጣ ።

960 የደጃዝማች ፡ ገንዘብ ፡ ምንም ፡ አልታወቀ ፤
—ወርቁም ፡ ሆነ ፡ ብሩ ፡ በሽጕጥ ፡ አለቀ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ያለ ፡ የሌለ ፡ ገንዘባቸው ፡ ብሩ ፡ ወርቁ ፡ በድብቅ ፡ እየተሰጠ ፡ አለቀ ፤ የገባበት ፡ ሳይታወቅ ፡ ቀረ ፤ ከንቱ ፡ መና ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ወርቁና ፡ ብሩ ፡ በሽጕጥ ፡ ተጋድለው ፡ ሞቱ ፤ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ተላለቁ ።

961 የደገኛ ፡ ነወይ ፡ ወይስ ፡ የቈለኛ ፤
—የምሥራች ፡ ሞተች ፡ የሚሉ ፡ አማርኛ ።

እኛም ፡ ብንመረምር ፡ ሰውም ፡ ብንጠይቅ ፤
—የምሥራች ፡ ሞተች ፡ ተብሎም ፡ አያውቅ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ የተጠላችና ፡ የተረገመች ፡ ብትሆን ፡ ሞቷ ፡ የምሥራች ፡ ሆኖ ፡ መነገር ፡ አልነበረበትም ፤ ይህ ፡ አዲስ ፡ ነገር ፡ ነው ፤ ከሰብአዊ ፡ ንግግር ፡ ውጭ ፡ ነው ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ የምሥራች ፡ ሞተች ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለየች ።

962 የዱሮ ፡ መድኀኒት ፡ ኮሶ ፡ ምን ፡ አላችሁ ፤
—ምንም ፡ አያስቀምጥ ፡ ይኸስ ፡ ቀጨሜቻችሁ ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡
(ዘለ ፡ ቍ ፡ 789 ፡ 1023) ፡

ሠ ፡ የቀጨሞ ፡ ፍሬ ፡ እንደ ፡ ኮሶ ፡ ሆድን ፡ አያጠራም ፤ ተቅማጥ ፡ የለውም ፤ ደስ ፡ አያሰኝም ።

ወ ፡ የቀጨሞው ፡ አርጩሜ ፡ ትዕግሥት ፡ ያስጨርሳል ፤ አያስቀምጥም ፤ እሱ ፡ እያለ ፡ ወደ ፡ ግብር ፡ መግባት ፡ አይቻልም ።

963 የዳኛው ፡ አሽከሮች ፡ ትግሬ ፡ የቀራችሁ ፡
—ከዳኛው ፡ የበለጥ ፡ ምን ፡ ጌታ ፡ አገኛችሁ ።

ሠ ፡ ከምኒልክ ፡ የበለጠ ፡ ለሕዝቡ ፡ የሚያዝንና ፡ የሚያስብ ፡ ንጉሢ ፡ ማንን ፡ አገኛችሁና ፡ የዳኛው ፡ አሽከሮች ፡ ትግሬ ፡ ቀራችሁ ፤ ያደራችሁለት ፡ ጌታስ ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ይሆን ።

ወ ፡ የዳኛው ፡ ምኒልክ ፡ አሽከሮች ፡ አገራችንን ፡ አናስጠቃም ፡ ንጉሠ ፡ ነገሥታችንን ፡ አናስደፍርም ፡ ብለው ፡ ከጠላታቸው ፡ ጋራ ፡ ተጨፋጭፈው ፡ ዐድዋ ፡ ላይ ፡ ቀሩ ።

964 —የጁን ፡ ጠጣው ፡ አትስጥ ፡ እያለችው ፡ እቱ ፡
—እኔ ፡ ከምን ፡ ብዬ ፡ ጠጁ ፡ መበርከቱ ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ የጨበጥከውን ፡ ጠጣው ፡ አትልቀቅ ፡ ለሰው ፡ አታሳልፍ ፡ እያለችው ፡ ኖሯል ፡ ለካ ፤ በእጁ ፡ ያለውን ፡ ጠጅ ፡ እስካሁን ፡ ያቈየው ፡ በሰጠችው ፡ ምክር ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ የጁ ፡ አገርህን ፡ አትልቀቅ ፤ አሳልፈህ ፡ ለሌላ ፡ አትስጥ ፡ እያለች ፡ እኅቱ ፡ ስለምትመክረው ፤ በግዛቱ ፡ ላይ ፡ ብዙ ፡ ቈየ ።

---

(1) እነኰለንቴ ፡ የተባሉ ፡ ጨካኝ ፡ ከልካዮች ፡ የቤተ ፡ መንግሥቱን ፡ በሮች ፡ ደፍሮ ፡ ተጋፍቶ ፡ የሚገባውን ፡ ሰው ፡ በቀጨሞ ፡ አርጩሜ ፡ እየሸነቈጡ ፡ ያበሩት ፡ እንደ ፡ ነበር ፡ ለመግለጥ ፡ የተነገረ ።

965 የጌታችን ፡ በሮች ፡ ስማቸው ፡ ማን ፡ ማነው ፤
—አንዱ ፡ ሰምቶ ፡ መቻል ፡ ትልቁም ፡ መተው ፡ ነው ።

ሠ ፡ የጌታችን ፡ በሮች ፡ ሰምቶ ፡ መቻልና ፡ መተው ፡ ይባላሉ ።

ወ ፡ ጌታችን ፡ ከጠባይህ ፡ ሁሉ ፡ ሁለት ፡ የማይለወጡ ፡ ባሕርዮች ፡ አሉኸ ፤ እኝህም ፡ ሰምቶ ፡ መቻልና ፡ ነገር ፡ አሳላፊነት ፡ ናቸው ።

966 የጐንደር ፡ ደብተራ ፡ ቄጥሮ ፡ እየተቀኘ ፡
—መማር ፡ እንደዚህ ፡ ነው ፡ ዘርፎ ፡ እንደ ፡ ተገኘ ።

ሠ ፡ ከተማሩ ፡ አይቀር ፡ ሳይጨነቁና ፡ ሳይቸገሩ ፡ ወዲያውኑ ፡ ከአንጐል ፡ አፍልቆ ፡ እንደ ፡ ተገኘ ፡ መቀኘት ፡ ነው ።

ወ ፡ እንደ ፡ ተገኘ ፡ ያላግባብ ፡ ሕዝብን ፡ መበደልና ፡ ገንዘቡን ፡ መዝረፍ ፡ ደፋርነትና ፡ ዐይን ፡ አውጣነት ፡ ያሰኛል ፤ (ውስጠ ፡ ዘለፋ) ።

967 —የጐዣሙ ፡ ዕዳዬስ ፡ ተከፈለልኝ ፤
—የዳሞቱ ፡ ግብር ፡ በጣም ፡ አሠጋኝ ።

ሠ ፡ የዳሞቱ ፡ መሬት ፡ ግብር ፡ እንዴት ፡ አድርጎ ፡ እንደሚከፈል ፡ አላውቅም ፤ በጣም ፡ ያሠጋኛል ።

ወ ፡ ዕለተ ፡ ሞትን ፡ ሳስታውሰው ፡ በጣም ፡ እሰቀቃለሁ ፤ ሥጋት ፡ ያድርብኛል ፤ የማይቀረው ፡ የሞት ፡ ፍዳ ፡ ያሠጋኛል ።

968 የጐዣም ፡ ባላልጋ ፡ ትናንት ፡ ተቀበረ ፤
—እግሬ ፡ ባይታሰር ፡ ለቅሶዬ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ ታስሬ ፡ ባልሆን ፡ እኔም ፡ እመቃብሩ ፡ መድረስ ፡ እለቅሰው ፡ መሄድ ፡ ነበረብኝ ፤ የማልቀርበት ፡ ለቅሶ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ባልያዝና ፡ ባልታሰር ፡ ኖሮ ፡ ከጌታዬ ፡ ቀብር ፡ ከለቅሷቸው ፡ አልለይም ፡ ነበር ።

969 የጐዣም ፡ የዳሞት ፡ ጥላው ፡ ተሰበረ ፤
—እግሬ ፡ ባይታሰር ፡ ለቅሶዬ ፡ ነበረ ።

ሠ ፡ ያ ፡ የዳሞቱ ፡ ትልቅ ፡ ጥላ ፡ መንገደኛውን ፡ ወጪ ፡ ወራጁን ፡ ፀሐይ ፡ እንዳይመታው ፡ ዋዕየ ፡ ሐሩር ፡ እንዳያቃጥለው ፡ ይከላከል ፡ ነበር ።

ወ ፡ የተበደለ ፡ የሚያስክስ ፡ የተጣላ ፡ የሚያስታርቅ ፡ አገር ፡ አዋይ ፡ ሽማግሌ ፡ ነበር ።

970 የጣቴን ፡ ቀለበት ፡ አንተ ፡ አድርገው ፡ ካሳ ፤
—በኔማጣት ፡ ገብቶ ፡ አስጨነቀኝሣ ። (1) (ራስ ፡ ዐ) ፡

ሠ ፡ ቀለበቴ ፡ ጠቦኛል ፤ አስጨንቆ ፡ ይዞኛል ፤ ከእንግዲህ ፡ ወዲያ ፡ ለኔ ፡ አይሆነኝምና ፡ ካሳ ፡ አንተ ፡ አድርገው ፤ ሰጥቼሃለሁ ፡ ውሰደው ።

ወ ፡ አግኝቶ ፡ ማጣት ፡ ተፈርቶ ፡ ተከብሮ ፡ በኖሩበት ፡ አገር ፡ ውርደትና ፡ እስራት ፡ ደርሶብኝ ፡ ተጨንቄ ፡ እኖራለሁ ።

---

(1) ራስ ፡ ዐሊ ፡ «አይሻል» ፡ ከሚባል ፡ ቦታ ፡ ከደጃች ፡ ካሳ ፡ (ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ) ፡ ጋራ ፡ ተዋግተው ፡ ድል ፡ በመሆናቸው ፡ ሸሽተው ፡ በራያ ፡ በረሓ ፡ እዋሻ ፡ ውስጥ ፡ ሳሉ ፡ ችግር ፡ ስለ ፡ ጸናባቸው ፡ በገና ፡ እየደረደሩ ፡ ያለቀሱት ።

971 የጠጣሁቱ ፡ ጠጅ ፡ ምንም ፡ ሳያሰክረኝ ፡
—እንጀራው ፡ አዞሮ ፡ በሰዎች ፡ ፊት ፡ ጣለኝ ።

ሠ ፡ የጠጣሁት ፡ ጠጅ ፡ ሳያሰክረኝ ፡ የበላሁት ፡ የእንክርዳድ ፡ እንጀ ያዞረኝ ፡ ያንኾልለኝ ፡ ዝመር ፤ ራሴን ፡ በጠበጠው ።

ወ ፡ እንጀራ ፡ ማጣት ፡ ራስን ፡ አለመቻል ፤ የሰው ፡ ፊት ፡ ያሳየኛል ፤ አገር ፡ ላገር ፡ ያዞረኛል ።

972 የጣላችሁት ፡ ጠጅ ፡ አንሶታለ ፡ ማሩ ፤
—እስኪ ፡ እናንተ ፡ ልጆች ፡ ተማሩ ፡ ጨምሩ ።

ሠ ፡ ጠጃችሁ ፡ ማር ፡ አንሶታል ፤ አልሱት ፤ ማር ፡ ጨምሩበት ፤ አክሉበት ።

ወ ፡ የኢትዮጵያ ፡ ልጆች ፡ በትምህርት ፡ ጠንክሩ ፤ በርቱ ፤ በዕውቀት ፡ ግፉ ።

973 ያ ፡ ሁሉ ፡ ማማሩ ፡ ዛሬ ፡ የት ፡ ተገኝቶ ፤
—የኔ ፡ ወንድም ፡ ጐንደር ፡ ስሙ ፡ ብቻ ፡ ቀርቶ ።

ሠ ፡ የዱሮ ፡ መልኩ ፡ ፍጹም ፡ ጠፍቷል ፤ ያ ፡ ሁሉ ፡ ውበቱና ፡ የልጅነቱ ፡ ደም ፡ ግባት ፡ በጭራሽ ፡ የለም ፤ አይመስሉ ፡ መስሏል ።

ወ ፡ ያ ፡ የታሪክ ፡ አገር ፡ የነበረው ፡ ጐንደር ፡ ጠፋ ፤ እንዳልሆነ ፡ ሆነ ፤ ያለሰው ፡ ቀረ ።

974 ያለሥጋ ፡ አትበላ ፡ ያለጠጅ ፡ አታድር ፡
—ያንተን ፡ እንግድነት ፡ እንዴት ፡ ቻለች ፡ ምድር ።

ሠ ፡ እንግድነትህ ፡ ያስቸግራል ፤ በቀላሉ ፡ በተገኘው ፡ ለመሸኘት ፡ አትችልም ፤ የሥጋና ፡ የጠጅ ፡ ጌታ ፡ አንተን ፡ በምን ፡ ታስተናግድሃለች ።

ወ ፡ ወዳያልኝ ፡ ወዲያ ፤ ያን ፡ ሁሉ ፡ ደግነት ፡ ለጋስነትና ፡ ቸርነት ፡ ይዘህ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ገባህን ፤ መጨረሻህ ፡ ይህ ፡ ሆኖ ፡ ቀረ ።

975 ያለበሳ ፡ ሥራ ፡ የማላውቀውን ፤
—ክፉ ፡ ባለጋራ ፡ አጠፋው ፡ ስሜን ።　　(ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ከሰው ፡ ነገር ፡ ሳልደርስ ፡ የሠራሁት ፡ ክፉ ፡ ሥራ ፡ ሳይኖር ፡ በከንቱ ፡ ስሜን ፡ አበላሹት ።

ወ ፡ ጨካኝ ፡ ጠላት ፡ ስሜን ፡ የሚባለውን ፡ አገር ፡ አጠፋው ፤ አቃጠለው ፤ ምድረ ፡ በዳ ፡ አደረገው ።

976 —ያለፍትሕ ፡ ያለርትዕ ፡ ተቀምቼ ፡ ከብቴን ፡
—ሳለቅስ ፡ እኖራለሁ ፡ ዕድሜ ፡ ልኬን ፡ ሳዝን ።

ሠ ፡ እዳኛ ፡ ሳልደርስ ፡ ፍርድ ፡ ሳላገኝ ፡ ከብቴን ፡ ተነጠቅሁ ፤ ሀብቴን ፡ ተዘረፍሁ ፤ ግፍ ፡ ተዋለብኝ ።

ወ ፡ ባሌ ፡ ከብቴ ፡ ተገድሎብኝ ፡ ባለጋሮቼ ፡ ሳይያዙ ፡ ፍርድ ፡ ሳይታይልኝ ፡ ቀረ ፤ ደሙ ፡ ፈሶ ፡ መና ፡ መቅረቱ ፡ ነው ።

977 ያ ፡ ልጅ ፡ ተራራውን ፡ ሊወጣ ፡ ያስባል ፤
—ዐዋቂ ፡ ሲያቅተው ፡ ድኾ ፡ እንዴት ፡ ይዘልቃል ። (ማ፡ወ፡እ)፡

ሠ ፡ የጠናው ፡ ሰው ፡ ዐቅም ፡ ያለው ፡ ጉልማሳው ፡ ሲያቅተው ፡ እንዴት ፡ ሕፃኑ ፡ ልጅ ፡ እየዳኸ ፡ ዐቀበቱን ፡ ለመውጣት ፡ የማይሆንለትን ፡ ይሞክራል ።

ወ ፡ ሀብት ፡ ያላቸው ፡ የተቻላቸው ፡ አይተው ፡ ሞክረውት ፡ አቅቷቸው ፡ የተዉትን ፤ የዕለት ፡ ጉርሥ ፡ የሌለው ፡ መናጢ ፡ ድኻው ፡ ለምን ፡ የማ ይሆንለትን ፡ ይለፋል ።

978 ያ ፡ ማለፊያው ፡ ጠጉርህ ፡ ያ ፡ ማለፊያው ፡ ዐይንህ ፡ እን ዴት ፡ አድሮ ፡ ይሆን ፤
—መጥቼ ፡ እንዳላይህ ፡ ካልተጠራሁ ፡ አይሆን ።

ሠ ፡ ዐይንህ ፡ ናፍቆኝ ፡ ላይህ ፡ እፈቅድ ፡ ነበር ፤ እኔ ፡ ካልተጠራሁ ፡ ለመ ምጣት ፡ አይሆንልኝም ።

ወ ፡ የሚቻል ፡ ቢሆን ፡ ዐይንህን ፡ ለማየት ፡ ጓጉቼ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ በሞት ፡ ካልተጠራሁ ፡ አንተ ፡ አለህበት ፡ ለመድረስ ፡ አልችልም ፤ አይሆንልኝም ።

779 ያ ፡ ማዶ ፡ ተራራ ፡ ረዥም ፡ ነው ፡ በጣም ፤
—በከብት ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ በግር ፡ አይወጣም ።

ሠ ፡ ያ ፡ ማዶ ፡ ተራራ ፡ በፈረስ ፡ በበቅሎ ፡ ካልሆነ ፡ በቀር ፡ በእግር ፡ አይ ዘለቅም ፤ ዐቀበቱ ፡ መጥፎ ፡ ነው ፤ ያታክታል ፤ ሰውነትን ፡ ያዝላል ።

ወ ፡ የዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ የሚቃናው ፡ በገንዘብ ፡ ነው ፤ እንዲያው ፡ በባ ዶ ፡ እጅ ፡ ቢጥሩ ፡ ቢግሩ ፡ አይሞላም ፤ አይሳካም ።

980 ያምናን ፡ ቀን ፡ አማሁት ፡ ላፌ ፡ ለከት ፡ የለው ፤
—መጣ ፡ የዘንድሮው ፡ እጅ ፡ እግር ፡ የሌለው ።

ሠ ፡ ያለፈውን ፡ ዓመት ፡ ሳማርር ፡ የዘንድሮው ፡ የባሰ ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ ሆነ ፤ ብርዱ ፡ ዝናሙ ፡ ከደጅ ፡ የማያስወጣ ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ይህ ፡ ዓመት ፡ ከመቼውም ፡ የበለጠ ፡ የረኃብ ፡ ዘመን ፡ ሆነ ፤ አባላ ሸኝ ፡ ጊዜ ፡ መጣ ፤ የሚላስ ፡ የሚቀመስ ፡ ጠፋ ።

981 ያ ፡ ሣሬ ፡ በዛና ፡ ታጭዶ ፡ አላልቅ ፡ አለኝ ፤
—ትንሽ ፡ የሚያግዘኝ ፡ ወይ ፡ ወንድም ፡ የለኝ ።

ሠ ፡ ብዙ ፡ ሣር ፡ አለኝ ፤ እኔ ፡ ሴቲቱ ፡ ባጭደው ፡ አላልቅ፡ አለ ፤ የሚያግ ዘኝ ፡ ወንድም ፡ በመጥፋቱ ፡ ግራ ፡ ገባኝ ።

ወ ፡ አሳሬ ፡ ብገፈግፈው ፡ የማያልቅ ፡ ሆነ ፤ መከራዬ ፡ በዛ ፤ ረዳት ፡ አጽ ናኝ ፡ ወንድም ፡ የለኝም ።

982 ያርባ ፡ አራቱ ፡ ደብር ፡ እያሉ ፡ ካህናቱ ፡
—ምነው ፡ በደርቡሽ ፡ እጅ ፡ ጐንደር ፡ መፈታቱ ። (1)

(1) አንዲት ፡ ስሜነኛ ፡ ሴት ፡ ጐንደር ፡ ቤት ፡ ነበራትና ፡ ደርቡሽ ፡ ከተማውን ፡ ካቃጠ ለው ፡ በኋላ ፡ ሄዳ ፡ በቤቷ ፡ አመድ ፡ ላይ ፡ ቆማ ፡ አገሩ ፡ ያለሰው ፡ መቅረቱን ፡ በመገን ዘብ ፡ የተሰማትን ፡ ሐዘን ፡ የገለጠችበት ።

ሠ ፡ ሊቃውንቱ ፡ ቀሳውስቱ ፡ ሞልተው ፤ ጐንደሬው ፡ በደርቡሽ ፡ ሥነ ፡ ሥርዐት ፡ ተፈታ ።

ወ ፡ ጐንደር ፡ በደርቡሽ ፡ እጅ ፡ ጠፋ ፤ አርባ ፡ አራቱ ፡ አብያተ ፡ ክርስቲያናት ፡ ተቃጠሉ ፤ ተመዘበሩ ።

983 ያርጎባ ፡ መኘታ ፡ ላንተም ፡ አይመችህ ፤
—እረ ፡ ባቡ ፡ ባቡ ፡ ራዱ ፡ ሰዎችህ ።

ሠ ፡ አርጎባ ፡ ላይ ፡ በመተኛትህ ፡ ሰዎች ፡ አልተደሰቱም ፤ እንዲያውም ፡ ሠግተውልህ ፡ ፈሩ ፤ ተንቀጠቀጡ ።

ወ ፡ የወረ ፡ ባቡ ፡ ጦር ፡ ምንም ፡ ሊመክትህ ፡ አልቻለም ፤ ሕዝቡ ፡ ፈራህ ፤ ተርበደበደልህ ።

984 ያችማ ፡ የኔ ፡ እት ፡ ቤት ፡ ሠርታ ፡ ነበረች ፤
—ሳትቀመጥበት ፡ ላፈርሰው ፡ ነው ፡ አለች ።

ሠ ፡ የሠራችውን ፡ ቤት ፡ ሳትቀመጥበት ፡ ልታፈርሰው ፡ ፈለገች ።

ወ ፡ እኅቱ ፡ ያንን ፡ መሳይ ፡ መልክ ፡ ይዛ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ዐፈር ፡ መሆን ፡ ስለማይቀር ፡ ሳትሰነብት ፡ መሞቷ ፡ ነው ።

985 ያቶ ፡ ሰይፉ ፡ ባሕርይ ፡ እጅግ ፡ ያስቸግራል ፤
—ጠላቱን ፡ እጅ ፡ ነሥቶ ፡ ለወዳጅ ፡ ይኰራል ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ያቶ ፡ ሰይፉ ፡ ጠባይ ፡ አይታወቅም ፤ ለባለጋራው ፡ ሰላምታ ፡ ይሰጣል ፤ ትሑት ፡ ነው ፤ ለወዳጁ ፡ ግን ፡ ይታበያል ፤ ለእግዚአብሔር ፡ ሰላምታ ፡ ይኰራል ።

ወ ፡ አቶ ፡ ሰይፉ ፡ የጠላውን ፡ ሰው ፡ እጁን ፡ ይቈርጠዋል ፤ ለሚወደውም ፡ ያኰራል ፤ መመኪያ ፡ ይሆናል ።

986 ያን ፡ ሁሉ ፡ ዕውቀትህን ፡ ያን ፡ ሁሉ ፡ ጥበብህን ፡ የት ፡ አደረሰከው ፤
—እረግ ፡ እንዱ ፡ ጠፋህ ፡ የምትመልሰው ።

ሠ ፡ የምትናገረው ፡ ጠፋህ ፤ ዐዋቂ ፡ የምትመስለው ፡ አንድ ፡ እንኳ ፡ ቃል ፡ መተንፈስ ፡ አቃተህ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ ያንን ፡ ሁሉ ፡ ዕውቀትና ፡ ጥበብ ፡ ይዘህ ፡ አንዱ ፡ ቅንጣት ፡ ልጁ ፡ ዐፈር ፡ ሆንህ ።

987 ያንበሳውን ፡ ጐፈር ፡ ቀሚስና ፡ ላንቃ ፡ አሰፍቶላቸው ፡
—አሽከሮቹን ፡ ይርጋ ፡ ወይ ፡ ባለበሳቸው ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ የተዘጋጀውን ፡ ያንበሳ ፡ ጐፈርና ፡ ካባ ፡ ላንቃ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ላሽከሮቹ ፡ አላለበሳቸውም ።

ወ ፡ ሞቱ ፡ አሽከሮቹን ፡ መሪር ፡ ሐዘን ፡ ጣለባቸው ፤ ከልና ፡ ወይባ ፡ አስመሰላቸው ።

988 ያንተ ፡ ቤት ፡ ፈረሰ ፡ የኔን ፡ ስታድስ ፤
—አጠገብህ ፡ ልሁን ፡ ገላዬ ፡ አትፍረስ ።

ሠ ፡ ሰውነቴ ፡ ገላዬ ፡ እየቈሰልክ ፡ እየፈራረስክ ፡ አትሂድ ።
ወ ፡ ገላዬ ፡ ወንድሜ ፡ አትለየኝ ፤ ሞትህን ፡ ልሙት ፤ እኔ ፡ ዐፈር ፡ ልሁን ።

989 ያንተ ፡ ያልሆነውን ፡ አትንካ ፡ ሲል ፡ መጽሐፍ ፡
—ያንዱን ፡ አትክልት ፡ እንዱ ፡ አይገባም ፡ መቀጠፍ ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ የሰው ፡ ተክል ፡ ማበላሸት ፡ አይገባም ፤ ያለፈቃድ ፡ መውሰድ ፡ እው ስጡ ፡ ገብቶ ፡ መረምረምና ፡ ማደባየት ፡ አያስፈልግም ።
ወ ፡ መዋሸትና ፡ ማበል ፡ የተናገሩትን ፡ መካድ ፡ አንደበትን ፡ ማጠፍ ፡ ለሰው ፡ ልጅ ፡ አይገባውም ።

990 ያንን ፡ ባሕር ፡ ዐረብ ፡ አጣጥፈህ ፡ አኑረው ፤
—ሁለተኛ ፡ ስፋ ፡ ደጕሳው ፡ ለተበለው ።

· ሁለተኛ ፡ ደጕስ ፡ አትደጕስ ፡ ብለህ ፡ ከሱ ፡ ጋራ ፡ አትጣላ ፤ ባሕር ፡ ዐረቡንም ፡ አጥፈህ ፡ አስቀምጠው ።
ወ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ዐረብን ፡ አትመን ፤ ከደግ ፡ ሰው ፡ አትቍጠረው ፤ አታቅርበው ።

991 ያንን ፡ ጕተናዬን ፡ ያየው ፡ ሰው ፡ ይናገር ፤
—ከሰው ፡ ራስ ፡ ሁሉ ፡ የኔ ፡ ያምር ፡ ነበር ። (ቀኛ ፡ ጎ ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ እንደኔ ፡ ጠጕር ፡ ያለ ፡ ምንም ፡ አልነበረም ፤ ያየው ፡ ሁሉ ፡ የሚያደ ንቀው ፡ ሐር ፡ የመሰለ ፡ ነበር ።
ወ ፡ ከመሳፍንቱ ፡ ሁሉ ፡ የኔ ፡ «ራስ» ፡ የተመሰገነ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ ነበር ፤ ጌትነቱ ፡ ክብሩና ፡ ማዕርጉ ፡ ከሁሉ ፡ የላቀ ፡ ነበር ።

992 ያን ፡ የነገርኩሽን ፡ የተውሽው ፡ እንደሆን ፡
—አንቺም ፡ ዘውድ ፡ አይደለሽ ፡ እኔም ፡ አክሊል ፡ አልሆን ። (1) (አ ፡ አ) ፡

ሠ ፡ የተነጋገርነው ፡ ቃል ፡ ከተዘነጋ ፡ በውነቱ ፡ ቁም ፡ ነገረኞች ፡ እንባ ልም ፤ ያንቺም ፡ ዘውዲቱነት ፡ የኔም ፡ አክሊሉነት ፡ ከንቱ ፡ ነው ።
ወ ፡ የለመንኩሽን ፡ ሹመት ፡ የማትፈጽሚልኝ ፡ ከሆንሽ ፡ ንግሥትነትሽ ፡ ለመቼ ፡ ነው ።

993 ያ ፡ እንግዳ ፡ ሞት ፡ መጣ ፡ እረግ ፡ ወየው ፡ ወየው ፤
—ለግሩ ፡ ውሃ ፡ አሙቄ ፡ በርጌ ፡ ሳልቈየው ።

ሠ ፡ የግር ፡ ውሃ ፡ ሳላሞቅና ፡ ሳልበርዝ ፡ እንግዳው ፡ የመጣ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ምን ፡ ይበጀኝ ፡ ይሆን ፤ እንዴት ፡ አፍር ፡ ይሆን ፡ የእግዜርን ፡ መ ንገድ ፡ ሳልከተል ።
ወ ፡ ጸባብ ፡ ወመቅዐን ፡ የተባለችውን ፡ የመንግሥተ ፡ ሰማይን ፡ በር ፡ መግቢያ ፡ የሚሆን ፡ ለነፍሴ ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ ሳልሠራ ፡ ያ ፡ ሞት ፡ ድን ገት ፡ ቢመጣ ፡ ምን ፡ ይውጠኝ ፡ ይሆን ።

---

(1) አለቃ ፡ አክሊሉ ፡ ንግሥተ ፡ ነገሥታት ፡ ዘውዲቱ ፡ ሳይነግሡ ፡ ፋሌ ፡ ተቀምጠው ፡ ሳሉ ፡ እንደ ፡ ትንቢት ፡ ተናግረውት ፡ የነበረው ፡ ስለ ፡ ተፈጸመ ፡ የተሰጣቸው ፡ ተስፋ ፡ በ መዘግየቱ ፡ ለማስታወስ ፡ ያኽል ፡ ያበረከቱት ፡ ግጥም ።

994 ያውና ፡ እዚያ ፡ ማዶ ፡ ፍሪዳ ፡ ተጥሏል ፤
—ልብ ፡ አልቈርጥም ፡ ብሎ ፡ ቢላዋው ፡ ደንዟል ።

ሠ ፡ ቢላዋው ፡ በጣም ፡ ከመደነዙ ፡ የተነሣ ፡ ከሥጋ ፡ ብልቶች ፡ ሁሉ ፡ በጣም ፡ ገር ፡ የሆነውን ፡ ልብ ፡ እንኳ ፡ አልቈርጥም ፡ አለ ።

ወ ፡ ልቤ ፡ ተስፋ ፡ አልቈርጥም ፡ ብሎ ፡ ይኸንን ፡ ዓለም ፡ ትቼ ፡ ለመሄድ ፡ ተቸግሪያለሁ ፤ የማደርገውን ፡ አጥቻለሁ ፤ ግራ ፡ ገብቶኛል ።

995 ያየሁትን ፡ ሁሉ ፡ እየተመኘሁ ፡
በሥጋ ፡ ገበያ ፡ እየተጕላላሁ ፡
እገዛለሁ ፡ ብዬ ፡ በከንቱ ፡ ደከምሁ ፤
—ቈርጦ ፡ መሄድ ፡ እንጂ ፡ ሌላ ፡ ደግ ፡ አጣሁ ።

ሠ ፡ በሥጋ ፡ ገበያ ፡ ከመዞርና ፡ ከመንከራተት ፡ የተሻለውን ፡ መርጦና ፡ አንዱን ፡ ብልት ፡ ቈርጦ ፡ መሄድ ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ ለማይሞላ ፡ ለሥጋዊ ፡ ኑሮ ፡ ከመጣርና ፡ ከመጋር ፡ ይህን ፡ ዓለም ፡ ትቶ ፡ መሄድና ፡ ተስፋ ፡ ቈርጦ ፡ በገዳም ፡ መኖር ፡ ይጠቅማል ።

996 ያ ፡ የወንድሜ ፡ ቤት ፡ ክፍት ፡ የመሰለው ፡
—ለካስ ፡ ዝግን ፡ ኖሯል ፡ እኔ ፡ ሳላውቀው ።

ሠ ፡ ክፍት ፡ መስሎኝ ፡ እወንድሜ ፡ ቤት ፡ ብሄድ ፡ ተዘግቶ ፡ አገኘሁት ፤ ለካ ፡ ዝግ ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ እኔ ፡ በረኃብ ፡ ስሞት ፡ በችግር ፡ ሳልቅ ፡ ለካ ፡ እወንድሜ ፡ ቤት ፡ ዝግኑ ፡ ክትፎው ፡ ይበላ ፡ ኖሯል ።

997 ያዘጋጀነውን ፡ ከየትም ፡ ከየትም ፡
—አንቺ ፡ ባይበላሽ ፡ እኔም ፡ አልበላሁም ።　(አ ፡ ገ ፡ ሐ)፡

ሠ ፡ አንቺ ፡ ካልበላሽ ፡ እኔም ፡ አልበላም ፤ ካንቺ ፡ ተለይቼ ፡ ለብቻዬ ፡ እኽል ፡ አልቀምስም ።

ወ ፡ አንቺ ፡ በአይብ ፡ ተመግበሽ ፡ ወስፋትሽን ፡ አሸነፍሽ ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ አልበላሁም ፤ ባዶ ፡ ሆዴን ፡ ነኝ ፤ እኽል ፡ አልቀመስኩም ።

998 ያ ፡ ደጃዝማች ፡ ተድላ ፡ መች ፡ ገንዘብ ፡ ወደደ ፤
—ተኵሶ ፡ አምዘግዝጎ ፡ ጥሎላቸው ፡ ሄደ ።　(1)

ሠ ፡ ተኵሶ ፡ ጠመንጃውን ፡ ወርውሮላቸው ፡ ሄደ ፤ ብረቱን ፡ ለመውሰድ፡ አልፈቀደም ፤ መጣሪያ ፡ አይሻም ።

ወ ፡ ጠላቱን ፡ ጥይቱ ፡ ቢያልቅበት ፡ በሽጕጥ ፡ ቅዝምዝም ፡ ገድሎት ፡ ሄደ ።

999 ያ ፡ ደብተራ ፡ ታሞ ፡ ምን ፡ አማረኝ ፡ ይላል ፤
—አይገኝም ፡ እንጂ ፡ እሱስ ፡ ማር ፡ ማር ፡ ይላል ።

---

(1) ደጃዝማች ፡ ተድላ ፡ ከዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ምስለኔ ፡ ከራስ ፡ እንግዳ ፡ ጋራ ፡ ሲዋጉ ፡ ተኵሰው ፡ ቢስቱ ፡ ጥይት ፡ ስለ ፡ አለቀባቸው ፡ በሽጕጥ ፡ ምዝግዝግ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ ገድለው፡ ስለ ፡ አመለጡ ፡ የተገጠመ ።

ሠ ፡ የታመመው ፡ ደብተራ ፡ ማር ፡ አማረኝ ፡ ይላል ፤ የማር ፡ ወለላ ፡
ቀምሼ ፡ በሞትኩ ፡ እያለ ፡ ይመኛል ።
ወ ፡ ደብተራው ፡ አቤቱ ፡ ጌታዬ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ይቅር ፡ በል ፡ የሙታንን ፡
ነፍስ ፡ ማር ፡ እያለ ፡ ይጸልያል ፤ መዋሥእቱን ፡ ይመራል ።

1000 ያገሩን ፡ ርቀት ፡ እናንት ፡ መች ፡ ዐውቃችሁ ፤
—ሞያ ፡ ማደሪያ ፡ ነው ፡ እኔ ፡ ልንገራችሁ ።

ሠ ፡ የምንሄድበት ፡ አገር ፡ ሩቅ ፡ ነው ፤ ውሎ ፡ ገባ ፡ አይደረስም ፤ ያው
ላል ፤ ያሳድራል ።
ወ ፡ ባለሞያነት ፡ ዕውቀትና ፡ የእጅ ፡ ብልኀት ፡ ኑሮን ፡ የሚያሻሽሉ ፡
ናቸው ።

1001 ያገራችን ፡ ቅመም ፡ ወጥ ፡ ያስተካክላል ፤
—ተግብጥ ፡ ምስሩ ፡ ሥጋችን ፡ ይሻላል ።

ሠ ፡ ተግብጥ ፡ ምስር ፡ ወጥ ፡ ሥጋ ፡ ወጥ ፡ ይሻላል ።
ወ ፡ ከግብጽ ፡ እየተላኩ ፡ ከሚመጡት ፡ ይልቅ ፡ ያገራችን ፡ ተወላጆች ፡
የሆኑ ፡ ጳጳሳት ፡ ይሻላሉ ።

1002 ይህ ፡ ሁሉ ፡ ሰዋስው ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ምስጢር ፡
—ቅኔ ፡ አንተ ፡ ጠፋህ ፡ ወይ ፡ መስፍን ፡ ሐረር ። (አ ፡ ደ) ፡

ሠ ፡ በሰዋስው ፡ በምስጢር ፡ የሚያሙህ ፡ ለምንድነው ፤ የማይገባህ ፡ መስ
ሏቸው ፡ ይሆን ፤ የሰዋስው ፡ ጌታ ፡ የግእዝ ፡ መምህር ፡ መሆንክን ፡
አልተረዱምን ፤ ቅኔ ፡ ካንተ ፡ የተረፈ ፡ መሆኑን ፡ አላወቁም ፡ ወይ ።
ወ ፡ ለኢትዮጵያ ፡ ሕዝብ ፡ ቅን ፡ አሳቢ ፡ የነበርከው ፡ ልዑል ፡ መኰንን ፡
በሞት ፡ ተለየኸን ፡ ወይ ፤ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ጠፋህ ፡ ወይ ።

1003 ይህስ ፡ አለማሰብ ፡ አለማፈር ፡ ነው ፤
—በገሃድ ፡ ቀን ፡ አርዶ ፡ ይበላል ፡ ወይ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ ዐይን ፡ ባይን ፡ በግልጽ ፡ የሰውን ፡ ከብት ፡ አርዶ ፡
ይበላል ።
ወ ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ በገሃድ ፡ ጾም ፡ አርዶ ፡ ይበላል ፤ ያባት ፡ የናቱን ፡
ልማድ ፡ ትቶ ፡ ሥርዐተ ፡ ጾምን ፡ ያፈርሳል ።

1004 ይህችን ፡ ሙሽራ ፡ አታይዋትም ፡ ወይ ፡
—መርገፏን ፡ ደርባ ፡ በጥበቧ ፡ ላይ ።

ሠ ፡ በጥበቡ ፡ ኩታዋ ፡ ላይ ፡ መርገፍ ፡ ያለበት ፡ ጌጥ ፡ ደርባበታለች ፤
ሙሽራዋ ፡ ጌጥ ፡ በጌጥ ፡ ሆናለች ።
ወ ፡ ሙሽራይቱ ፡ ያን ፡ ሁሉ ፡ ጥበብና ፡ ዕውቀት ፡ ይዛው ፡ ሞተች ፤ እመ
ቃብር ፡ ገባች ፤ በጫጕላነቷ ፡ ዐረፈች ።

1005 ይህ ፡ ነገር ፡ ለዝና ፡ ለጕራ ፡ ይበቃል ፤ (ራስ ፡ ኀ ፡ ተ ፡ ሃ) ፡
—አውራውን ፡ ጕዳና ፡ ማን ፡ ከልክሎ ፡ ያውቃል ።

ሠ ፡ በማን ፡ አገር ፡ ጥርጊያ ፡ ጕዳና ፡ ተከልክሎ ፡ ይታወቃል ፤ ማለፊያ ፡
ማግደሚያውን ፡ ማን ፡ ያግድ ፡ ይከለክል ፡ ነበር ።
ወ ፡ ባላባቱን ፡ ያገሩን ፡ ተወላጅ ፡ እኔን ፡ እንዴት ፡ ማለፊያ ፡ ታሳጡኛላ
ችሁ ፡ ትከለክሉኛላችሁ ።

1006 ይህን ፡ ምክራችንን ፡ ሴቱ ፡ እንዳይጠላው ፡
—ጕትቻ ፡ እንዲጠፋ ፡ ባልቦ ፡ እንዲሆን ፡ ነው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ምክራችን ፡ የዠሮው ፡ ጌጥ ፡ ጕትቻው ፡ ቀርቶ ፡ በእግር ፡ አልቦ ፡ ብቻ ፡ እንዲያጌጡ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ሴቶች ፡ ባሎቻቸውን ፡ አጥተው ፡ (ሞተውባቸው) ፡ ሴት ፡ አዳሪ ፡ እን ዳይሆኑ ፡ ወንዶች ፡ ጠላትን ፡ ጠንክሮ ፡ መከላከል ፡ አለባቸው ።

1007 ይህን ፡ የቅቤ ፡ ቅል ፡ በምን ፡ ልያዘው ፤
—ሐብሉ ፡ ተበጥሷል ፡ የማንጠልጠያው ።

ሠ ፡ የቅቤው ፡ ቅል ፡ መያዣ ፡ የለውም ፤ ማንጠልጠያው ፡ ተበጥሷል ።

ወ ፡ የወገን ፡ መመኪያ ፡ ዘመድ ፡ ሰብሳቢ ፡ የቤቱ ፡ ባላ ፡ የነበረው ፡ ሰው ፡ ሞተ ፤ እንጥስ ፡ ቢሉ ፡ ቅንጥስ ፡ ሆነ ።

1008 ይህን ፡ ያኽል ፡ ጥና ፡ አለ ፡ ወይ ፡ በረንታ ፤
—እነቆራ ፡ ሞቶ ፡ ዴንሳ ፡ የተፈታ ።

ሠ ፡ ብዙ ፡ ጥና ፡ ተጠርቶ ፡ ነበር ፤ እነቆራ ፡ ቢሞት ፡ ዴንሳ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ሄዶ ፡ ተፈታ ፤ ትልቅ ፡ የጕዞ ፡ ፍታት ፡ ተደረሰለት ።

ወ ፡ እነቆራ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ቢሞት ፡ ዴንሳ ፡ ያለው ፡ ሕዝብ ፡ ከባለ ጋራ ፡ እጅ ፡ ወደቀ ፤ ሰብሳቢ ፡ በማጣት ፡ ተበተነ ።

1009 ይህ ፡ የባላገር ፡ ልጅ ፡ በቅሎ ፡ ያላወቀ ፡
—ርካቡን ፡ ሳይረግጥ ፡ ሲወጣ ፡ ወደቀ ።

ሠ ፡ ልጁ ፡ ርካብ ፡ ሳይቈነጥጥ ፡ ለኮ ፡ ሳይጨብጥ ፡ እበቅሎ ፡ ላይ ፡ እወ ጣለሁ ፡ ብሎ ፡ ወደቀ ።

ወ ፡ አለሁ ፡ አለሁ ፡ ደረስሁ ፡ ደረስሁ ፡ ሲል ፡ ሞተ ፤ ዐፈር ፡ ሆነ ።

1010 ይህ ፡ የያዝኩት ፡ ሽክላ ፡ በጣሙን ፡ ከበደኝ ፤
—የወደቅሁ ፡ እንደሆን ፡ አፈርሰው ፡ መሰለኝ ።

ሠ ፡ አደናቅፎኝ ፡ ብወድቅ ፡ የያዝኩት ፡ ሽክላ ፡ አይተርፍም ፤ ዐፈር ፡ ይሆ ናል ፤ ይደቃል ።

ወ ፡ ሰው ፡ ዐፈር ፡ ነው ፤ ነፍስ ፡ ከተለየችው ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

1011 ይሉኛል ፡ አረጀ ፤ መች ፡ ምድር ፡ ይዣለሁ ፤
—የኰራሁ ፡ መስዬ ፡ መሬት ፡ ለቅቄአለሁ ።

ሠ ፡ ኵራት ፡ እንደ ፡ ያዘው ፡ ሰው ፡ መሬት ፡ መርገጥ ፡ ተጸይፌያለሁ ፤ በ ጥፍሬ ፡ እየቆምሁ ፡ እሄዳለሁ ።

ወ ፡ እንዳለው ፡ እንደ ፡ ተረፈው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡ መሬቱን ፡ ትቻለሁ ፤ በ ጥፍሬ ፡ እየቆምሁ ፡ እሄዳለሁ ።

1012 ይመችሃልና ፡ ለመሥራት ፡ ሰርዲን ፤
—ዓሣ ፡ ባሣ ፡ እንዲሆን ፡ ጣል ፡ ያን ፡ መረብህን ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ለሰርዲን ፡ የሚሆን ፡ ብዙ ፡ ዓሣ ፡ እንድትይዝ ፡ መረብህን ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ጣለው ፤ እወንዙ ፡ ውሃ ፡ ጨምረው ።

ወ ፡ በርትተህ ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ታግለህ ፡ ጣሊያን ፡ የያዘውን ፡ የመረብን ፡ ቀበሌ ፡ አስለቅቀው ፤ አሻግረህ ፡ አብረው ፤ አሳደው ።

1013 ይመጣለ ፡ ብለን ፡ ስንጠብቀው ፡
—ያን ፡ ጠላታችንን ፡ ቀን ፡ አልፎ ፡ አጣነው ።

ሠ ፡ ባለጋራችንን ፡ ሌሊት ፡ አድፍጠን ፡ ስንጠባበቀው ፡ ቀን ፡ በጊዜ ፡ አልፎ ፡ ኖሮ ፡ ሳናገኘው ፡ ቀረን ፤ ከእጃችን ፡ ሳይወድቅ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ክፉው ፡ ጊዜ ፡ የግፉ ፡ ዘመን ፡ ስላለፈ ፡ ጠላታችን ፡ ጠፋ ፤ ታላቅ ፡ አወዳደቅ ፡ ወደቀ ፤ ድል ፡ ሆነ ።

1014 ይመጣለ ፡ ብሎ ፡ ሲጠብቅ ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፡
—በዳሞት ፡ ተይዞ ፡ በላይ ፡ አለፈ ፡ አሉ ።

ሠ ፡ ይመጣል ፡ ተብሎ ፡ ሲጠበቅ ፡ በላይ ፡ አድርጎ ፡ በዳሞት ፡ በኩል ፡ ሄደ ።

ወ ፡ በላይ ፡ የማይቀረውን ፡ ሞት ፡ ሞተ ፤ ድርሻውን ፡ ተወጣ ።

1015 ይማርልኝ ፡ ብዬ ፡ በጌምድር ፡ ሰድጄ ፡
—ቀለም ፡ ገባው ፡ አሉ ፡ እሳት ፡ ሆነ ፡ ልጄ ። (1)

ሠ ፡ ልጄ ፡ ቀለም ፡ ይቀበላል ፡ ትምህርት ፡ ይገባዋል ፡ እሳት ፡ ሆኗል ፡ አሉ ።

ወ ፡ ለትምህርት ፡ በጌምድር ፡ የሄደው ፡ ልጄ ፡ በእሳት ፡ ተቃጠለ ፤ በሕ ይወቱ ፡ ነደደ ።

1016 ይሰሙኝ ፡ እንደሆን ፡ ጃንሆይ ፡ ልምከርዎ ፤
—የሰው ፡ ዕንጨት ፡ ማንደድ ፡ እንግዲህ ፡ ይብቃዎ ።

ሠ ፡ ጃንሆይ ፡ ምክሬን ፡ የሚቀበሉኝ ፡ ቢሆን ፡ የሰው ፡ ማገዶ ፡ ማንደድ ፡ ይቅርብዎ ።

ወ ፡ እባክዎ ፡ ሕዝብዎን ፡ በእሳት ፡ አያቃጥሉት ፤ እንደ ፡ ዕንጨት ፡ አያን ድዱት ፤ አይለብልቡት ።

1017 ይቈርጡኝም ፡ እንደሁ ፡ ይገሉኝም ፡ እንደሁ ፡ ይኸው ፡ ቆም ኩልዎ ፤
—ያ ፡ ለምጣም ፡ ምኒልክ ፡ ብዬ ፡ ሰደብኩዎ ። (ካ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ለምጣም ፡ ብዬዎታለሁ ፤ የሚያደርጉትን ፡ ያድርጉኝ ፤ የፈቀዱትን ፡ ይሥሩ ።

ወ ፡ መላ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የሚደሰትብዎ ፡ ሕዝብዎ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚያ ይብዎ ፡ ታላቅ ፡ ንጉሥ ፡ ነዎ ።

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ለትምህርት ፡ ከጐዣም ፡ በጌምድር ፡ ሂዶ ፡ የነበረውን ፡ ልጅ ፡ ከመም ህሩ ፡ ጋራ ፡ እቤት ፡ ዘግተው ፡ በእሳት ፡ ባቃጠሏቸው ፡ ጊዜ ፡ እናቲቱ ፡ በሙሾ ፡ ሐዘ ኗን ፡ የገለጠችበት ።

1018 ይበቃኛል ፡ ብዬ ፡ ስመካ ፡ በርስቴ ፡
—አወይ ፡ አለመማር ፡ ተቀበረ ፡ ሀብቴ ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ትምህርት ፡ ባለማወቄ ፡ ሥራ ፡ በማጣት ፡ ዕድሌ ፡ ተቀብሮ ፡ ቀረ ፤ ለቁም ፡ ነገር ፡ ሳልበቃ ፡ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ ሳልደርስ ፡ ብኩን ፡ ሆንኩ ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ ሀብቴ ፡ እግዚአብሔር ፡ ሳይምረው ፡ ቀረ ፤ ሞተ ፤ ተቀበረ ፤ ዐፈር ፡ ሆነ ።

1019 ይታመሳል ፡ አሉ ፡ ከፋና ፡ ቦረና ፤
—አማን ፡ አይደሉም ፡ ወይ ፡ እነራስ ፡ ጐበና ።

ሠ ፡ እነራስ ፡ ጐበና ፡ ጤና ፡ አይደሉም ፡ ወይ ፤ የሆኑት ፡ ነገር ፡ አለ ፡ ወይ ፤ አገር ፡ ሰላም ፡ አይደለም ፡ ወይ ።

ወ ፡ የራስ ፡ ጐበና ፡ የትውልድ ፡ አገር ፡ አማን ፡ አይደለም ፡ ወይ ።

1020 ይነሡ ፡ መምር ፡ ፍየል ፡ ከሳዎአለች ፤
—ባላሰብኩት ፡ ነገር ፡ ጣ〳 〵ብኝ ፡ ብላለች ።

ሠ ፡ ባልሠራሁት ፡ ሥራ ፡ መምሩ ፡ ማመልከቻ ፡ ጣፉብኝ ፡ ብላ ፡ ፍየል ፡ ከሳዎታለች ፤ አቤቱታ ፡ አቅርባብዎታለች ።

ወ ፡ ቈዳዬን ፡ ብራና ፡ እያደረጉ ፡ እንደ ፡ ወረቀት ፡ እያሣሡ ፡ መጻፊያ ፡ አደረጉት ፡ ብላ ፡ ፍየል ፡ ወደ ፡ እግዚአብሔር ፡ ታሳጣዎታለች ።

1021 ይናገሩኝና ፡ እናገራለሁ ፡ ስል ፡
—ባንተ ፡ አየን ፡ ይሉኛል ፡ መስታወት ፡ ይመስል ።

ሠ ፡ ሁሉ ፡ በኔ ፡ ይፈርዳል ፤ ሽማግሎቹ ፡ በደለኛ ፡ ያደርጉኛል ።

ወ ፡ ፊቴ ፡ እንደ ፡ መስተዋት ፡ ያበራ ፡ ይመስል ፡ ባንተ ፡ አየን ፡ ይሉኛል ።

1022 ይኸስ ፡ ጠጅ ፡ ቤታችሁ ፡ በጣም ፡ ይገርማል ፤
—በሚጠጣበት ፡ ቀን ፡ ይበጠብጣል ።

ሠ ፡ ጠጅ ፡ በመጠጫው ፡ ቀን ፡ ይበጠበጣል ፤ ይደባለቃል ።

ወ ፡ መጠጥ ፡ በቀመሰ ፡ ቍጥር ፡ ይበጠብጣል ፤ አገር ፡ ያሸብራል ፤ አምባጓሮ ፡ ያበቅላል ።

1023 ይኸ ፡ ቀጨሜቸው ፡ አያስቀምጥም ፡ ሲሉ ፡
—ይኸው ፡ ይነዳዋል ፡ ሰራዊቱን ፡ ሁሉ ። (አ ፡ በ) ፡ (ዘለ ፡ ቍ ፡ 789 ፡ 962) ፡

ሠ ፡ የቀጨሞው ፡ ፍሬ ፡ ይኸው ፡ ያስቀምጣል ፤ ሆድ ፡ ያጠራል ።

ወ ፡ ከልካዩ ፡ ሰራዊቱን ፡ በቀጨሞ ፡ አርጨሜ ፡ እየመታ ፡ ያበረዋል ፤ ወደ ፡ ኋላው ፡ ይነዳዋል ።

1024 ይኸ ፡ ቤት ፡ ማፍሰሱን ፡ አበዛው ፡ ምነው ፤
—ማለዳ ፡ ተነሥተን ፡ ነገ ፡ ልንከድነው ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ቤቱ ፡ ንገ ፡ ሊከፈከፍና ፡ ሊከደን ፡ ላንድ ፡ ቀን ፡ አዳር ፡ እያፈሰሰ ፡ አስቸገረን ፤ አላስቀምጥ ፡ አለን ።

ወ ፡ ነጋ ፡ አልነጋ ፡ ብለን ፡ በሌሊት ፡ መጥፋታችን ፡ ነው ፤ በጧት ፡ መኖ ብለላችን ፡ የማይቀር ፡ መሆኑ ፡ ነው ።

1025 **ይኸው ፡ አውሬው ፡ መጣ ፡ ዐውቄዋለሁ ፤**
**—በሉ ፡ እናንተ ፡ ዳኑ ፡ ይብላኝ ፡ ለታችሁ ።**

ሠ ፡ እናንተ ፡ ሕይወታችሁን ፡ አትርፉ ፤ ነፍሳችሁን ፡ አድኑ ፤ እኔን ፡ ሮጬ ፡ የማላመልጠውን ፡ አውሬው ፡ ይብላኝ ።

ወ ፡ የሞታችሁብኝ ፡ እንደ ፡ ሆን ፡ ይብላኝ ፡ ለኔ ፤ ወዴት ፡ እገባ ፡ ይሆን ።

1026 **ይኸው ፡ ይዘራል ፡ በየቀኑ ፡ ሰው ፤**
**—አንድም ፡ አልበቀለ ፡ የታል ፡ ቡቃያው ።**

ሠ ፡ የተዘራው ፡ እኽል ፡ አልበቀለም ፤ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ፤ ለቡቃያ ፡ እ ንኳ ፡ ሳይደርስ ፡ ጠፋ ።

ወ ፡ ያዳም ፡ ልጅ ፡ በየጊዜው ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ይጓዛል ፤ በየቀኑ ፡ ከ ዚህ ፡ ዓለም ፡ ይለያል ፤ ግን ፡ ከመቃብር ፡ የሚወጣ ፡ የለም ።

1027 **ይኸ ፡ የመንዝ ፡ ዘር ፡ በጃማ ፡ አልሰመረም ፤**
**—በቀለ ፡ ስንለው ፡ ጠፉ ፡ በመስከረም ።** (አ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ አዝመራችን ፡ በቀለ ፡ ብለን ፡ ስንደሰት ፡ ተመልሶ ፡ ጠፋ ፤ ሥራችን ፡ እንደ ፡ ዋለ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ከቤታችን ፡ ተስፋ ፡ የምናደርግበት ፡ በቀለ ፡ ወጣልን ፡ ስንል ፡ በሞት፡ ተቀጨ ፤ በወጣትነቱ ፡ ዐረፈ ።

1028 **ይኸ ፡ የራስ ፡ ድንኳን ፡ ጐኑ ፡ በተበሳ ፤**
**—አረጋይን ፡ እንዳይ ፡ ሲቀመጥ ፡ ሲነሣ ።**

ሠ ፡ ሽማግሌው ፡ ጨዋው ፡ ሰው ፡ ቍጭ ፡ ብድግ ፡ ሲል ፡ እንድመለከ ተው ፡ ምነው ፡ ድንኳኑ ፡ በተገለጠ ፤ ወይም ፡ በተቀደደ ።

ወ ፡ አረጋይን ፡ (አፈ ፡ ንጉሥ) ፡ በባለሟልነቱ ፡ ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ ሲል ፡ ባንደበቱ ፡ ሲናገር ፡ እንዳየው ፡ ምነው ፡ ድንኳኑ ፡ በተገለጠ ።

1029 **ይደርሳል ፡ ሰዓቱ ፡ ሳስብ ፡ ሌላ ፡ ሌላ ፤**
**—የተሰቀለውን ፡ ሥጋውን ፡ ሳልበላ ።**

ሠ ፡ የተንጠለጠለውን ፡ በሜንጦ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ ሥጋ ፡ ሳልበላ ፡ ሰዓት ፡ ደረሰብኝ ፤ የምሳው ፡ ጊዜ ፡ ተቃረበ ።

ወ ፡ በዕለተ ፡ ዐርብ ፡ የተሰቀለውን ፡ የክርስቶስን ፡ ሥጋ ፡ ወደሙ ፡ ሳልቀ በል ፡ ጊዜ ፡ ሞቴ ፡ መጣ ፤ እርጅና ፡ ደረሰ ።

1030 **ይጓደኀና ፡ አብርሀ ፡ ከትግሬ ፡ ተነሥተው ፡ ወደ ፡ ጐዣም ፡ ሲያልፉ ፡**
**ተመቻቸውና ፡ ይፋግ ፡ አራገፉ ።**

ሠ ፡ ይፋግ ፡ ለነጋዴ ፡ ማረፊያ ፡ የተመቸ ፡ በመሆኑ ፡ ይጎደጎና ፡ አብርሀ ፡ ጭነታቸውን ፡ እዚያ ፡ ሲደርሱ ፡ አራገፉ ።

ወ ፡ ይጎደጎና ፡ እብርሀ ፡ ይፋግ ፡ ላይ ፡ ሲደርሱ ፡ ያለ ፡ የሌላቸውን ፡ በሙሉ ፡ ተቀሙ ፤ ተዘረፉ ፤ ባዶ ፡ እጃቸውን ፡ እቤታቸው ፡ ገቡ ።

1031 ይድናል ፡ ብለን ፡ አሻግረን ፡ ስናይ ፡
—እንዲያ ፡ እንደ ፡ ፈራነው ፡ እውነት ፡ ሞተ ፡ ወይ ። (ማ ፡ ወ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ የመዳን ፡ ተስፋ ፡ የለኝም ፡ እያለ ፡ ይሠጋ ፡ እንደ ፡ ነበረ ፤ እውነትም ፡ ሞቶ ፡ ዐረፈን ።

ወ ፡ እንደ ፡ ተባለው ፡ ሁሉ ፤ እውነት ፡ ነገር ፡ ጠፍቶ ፡ ሐሰት ፡ ብቻ ፡ ሆነ ።

1032 ይገኝ ፡ መስሎን ፡ ነበር ፡ የመጣን ፡ ከተማ ፤
—እንግባ ፡ አገራችን ፡ እውነት ፡ ከጠፋማ ።

ሠ ፡ የምንፈልገው ፡ ሰው ፡ የማይገኝ ፡ ከሆነ ፡ በእውነትም ፡ ከታጣ ፡ ወደ ፡ አገራችን ፡ እንመለስ ።

ወ ፡ እውነት ፡ ነገር ፡ ከጠፋ ፡ ሐሰት ፡ ከነገሠ ፡ የመጣንበትን ፡ ጕዳይ ፡ ትተነው ፡ አገራችን ፡ እንግባ ።

1033 ደመና ፡ ነው ፡ ብዬ ፡ አዝኜ ፡ ነበር ፤
—ፀሓይስ ፡ ከወጣ ፡ ይሰጣ ፡ ያ ፡ ሣር ።

ሠ ፡ ዳመናው ፡ ከገለጠ ፡ ፀሓይ ፡ ከወጣ ፡ ሣሩ ፡ ይሰጣ ፤ ይድረቅ ።

ወ ፡ ፍርድ ፡ የሚያይ ፡ የድኻ ፡ ደም ፡ የሚበቀል ፡ ዳኛ ፡ ከተገኘስ ፡ በደለኛ ፡ ይቀጣ ፤ ነፍሰ ፡ ገዳይም ፡ ፍርዱን ፡ ይቀበል ።

1034 ደስ ፡ ያለው ፡ ይመስል ፡ ይህ ፡ ሁሉ ፡ ፍጥረት ፡
—እንቢ ፡ አልሄድም ፡ አለ ፡ አዘንተኛ ፡ ቤት ።

ሠ ፡ ሕዝቡ ፡ ደስ ፡ ያለው ፡ ይመስል ፡ ከኃዘን ፡ ቤት ፡ መሄድን ፡ ጠላ ።

ወ ፡ ሞት ፡ አጠቃን ፤ ሐዘን ፡ ከቤታችን ፡ የማይወጣ ፡ ሆነ ፤ በላይ ፡ በላዩ ፡ ይጨመር ፡ ዠመር ።

1035 ደኅና ፡ ሁኚ ፡ የኔ ፡ እት ፡ አንተም ፡ የኔ ፡ ወንድም ፤
—አካሌን ፡ ታጣሁኝ ፡ አልፈልግም ፡ ዓለም ።

ሠ ፡ ጤና ፡ ከሌለኝ ፡ አካለ ፡ ጕደሎ ፡ ከሆንኩ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ መኖር ፡ አልፈልግም ።

ወ ፡ ወንድሜ ፡ አካሌ ፡ ከሞተብኝ ፡ ትዳርና ፡ ንብረት ፡ አልፈልግም ፤ መንኜ ፡ ወደ ፡ ገዳም ፡ እገባለሁ ።

036 ደንቢያና ፡ ፎገራን ፡ የላም ፡ አገር ፡ ትቶ ፡
—ወተት ፡ ወተት ፡ ይላል ፡ እከተማ ፡ ገብቶ ።

ሠ ፡ የላሙን ፡ የወተቱን ፡ አገር ፡ ጥሎ ፡ መጥቶ ፡ እከተማ ፡ ገብቶ ፡ ወተት ፡ ይፈልጋል ።
ወ ፡ ከብት ፡ አርብቶ ፡ አርሶ ፡ ቈፍሮ ፡ በባላገር ፡ እንደ ፡ መኖር ፡ እከ ተማ ፡ ውስጥ ፡ ይንቀዋለላል ፤ ይወጣል ፤ ይወርዳል ፤ ይዋትታል ።

1037 ደጅ ፡ ጠኚ ፡ ጕርሻውን ፡ ተቀበለ ፡ ወይ ፤
—ልዑል ፡ ጥፍት ፡ ያሉት ፡ ሳናስብ ፡ ሳናይ ።

ሠ ፡ ደጅ ፡ ጠኚውን ፡ ሳይሸኙ ፡ መኳንንቱን ፡ ሳያሰናብቱ ፡ ሹልክ ፡ ብለው ፡ ሄደው ፡ ዕልም ፡ ብለው ፡ የቀሩት ፡ ለምንድነው ።
ወ ፡ ልዑል ፡ ማህለ ፡ ሥላሴ ፡ ምነው ፡ ሳናስበው ፡ ድንገት ፡ ጠፉ ፤ አሳ ዛኝ ፡ ሞት ፡ ደረሰባቸው ።

1038 ደጃች ፡ ዐምዴ ፡ ጠፍቶ ፡ ያገኘው ፡ ማነው ፤
—ቀጨማ ፡ እንካ ፡ ያሉት ፡ በሣጥን ፡ ከተው ። (1)

ሠ ፡ የጠቋሚ ፡ ገንዘብ ፡ የሰጡት ፡ ደጃች ፡ ዐምዴን ፡ ማን ፡ አግኝቶ ፡ ነው ።
ወ ፡ ደጃች ፡ ዐምዴ ፡ በሣጥን ፡ ተከቶ ፡ ቀጨማ ፡ ተቀበረ ፤ እንግዲህ ፡ ወዴት ፡ ይገኛል ፤ ትልቁ ፡ ወገናችን ፡ በሞት ፡ ተለየን ።

1039 ደግስና ፡ ይብላ ፡ ተወዳጅ ፡ ሕዝብህ ፤
—ዓለም ፡ ያወቀልህ ፡ ግብረ ፡ መልካም ፡ ነህ ።

ሠ ፡ ግብረ ፡ ሰፊ ፡ ድግስ ፡ የሚዋጣልህ ፡ መሆንህን ፡ ዓለም ፡ ዐውቆል ሃል ፤ ሕዝብ ፡ ተረድቶታል ።
ወ ፡ ታላላቅ ፡ ሥራ ፡ የሠራህ ፡ ለሕዝብህ ፡ መልካም ፡ ነገር ፡ ያደረግህ ፡ ንጉሥ ፡ መሆንህን ፡ ዓለም ፡ ዐውቆታል ።

1040 ደኅሽ ፡ ስለሌለ ፡ መጣፋችንን ፡
በገንዘብህ ፡ ገዝተህ ፡ ባሕር ፡ ዐረቡን ፡
—ወይ ፡ አንተ ፡ ደጕሰው ፡ ራስ ፡ መኰንን ።

ሠ ፡ ደኅሽ ፡ ከጠፋ ፡ መጻፋችንን ፡ አንተው ፡ ደጕሰው ፤ ጠርዘው ።
ወ ፡ ራስ ፡ መኰንን ፡ እንዳንተ ፡ ቸር ፡ ደግ ፡ ርኅሩኅ ፡ ሰው ፡ ወዳጅ ፡ የ ሆነ ፡ መስፍን ፡ አልነበረም ።

1041 ዱሮም ፡ ልማዱ ፡ ነው ፡ የኛ ፡ ቤት ፡ አዝመራ ፤
—አበባ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ፍሬም ፡ አያፈራ ።

ሠ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ የኛ ፡ ቤት ፡ አዝመራ ፡ ፍሬ ፡ አይሰጥም ፤ በአ በባውና ፡ በእንቡጥነቱ ፡ ይቀራል ።
ወ ፡ እኛ ፡ ቤት ፡ ዘር ፡ አይወጣም ፤ ልጅ ፡ አያድግበትም ፤ ባጭር ፡ ይቀ ጫል ፤ ለወግ ፡ ለማዕርግ ፡ የሚደርስ ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ የሚበቃ ፡ የለም።

---

(1) ደጃዝማች ፡ ዐምደ ፡ ሚካኤል ፡ ሀብተ ፡ ሥላሴ ፡ ቀጨማ ፡ በሚባለው ፡ በሞጃዎች ፡ መካነ ፡ መቃብር ፡ በተቀበሩ ፡ ጊዜ ፡ የተገጠመ ።

1042 ዲቃላ ፡ ነው ፡ ብሎ ፡ አገር ፡ ሲታመስ ፡
—ቍርጥ ፡ እንዳባቱ ፡ ሆነ ፡ ዮሐንስ ።　　(መሸሻ ፡ ግዛው) ፡

ሠ ፡ ዮሐንስ ፡ ያባቱን ፡ መልክ ፡ ይዟል ፤ መሰል ፡ ልጁ ፡ ነው ፤ በትክክል ፡ እሱኑ ፡ ሆኗል ።

ወ ፡ ዐፄ ፡ ዮሐንስ ፡ እንደ ፡ ሃይማኖት ፡ አባቱ ፡ እንደ ፡ መጥምቁ ፡ ዮሐንስ ፡ ሆነ ፤ አንገቱን ፡ ለሰይፍ ፡ ሰጠ ፤ ለሀገሩ ፡ በሰማዕትነት ፡ ሞተ ።

1043 ዳኝነትን ፡ ይዞ ፡ ሐሰትን ፡ ለማጥፋት ፡
—ያማለ ፡ ያማለ ፡ አልተገኘም ፡ እውነት ።

ሠ ፡ ሐሰት ፡ ነገርን ፡ አጥፍቶ ፡ እውነትን ፡ ለመመሥረት ፡ ያም ፡ ቢል ፡ ያም ፡ ቢል ፡ አልሆነም ፤ ማናቸውም ፡ ሰው ፡ ቢጣጣር ፡ እውነት ፡ አልተገኘም ።

ወ ፡ ከሳሽም ፡ ተከሳሽም ፡ ቢምል ፡ እውነቱ ፡ አልተገኘም ፤ አልተገለጠም ፤ በመሐላ ፡ ፍራቻ ፡ ሰው ፡ ወደ ፡ እውነት ፡ ሊመለስ ፡ አልቻለም፤

1044 ዳዊቱን ፡ ግንዘቱን ፡ ይዘው ፡ ሲፈቱት ፡
—እንቢ ፡ ብሎ ፡ ሄደ ፡ ወዳባቱ ፡ ርስት ።

ሠ ፡ ቢመክሩት ፡ ቢሉት ፡ ቢሠሩት ፡ አሻፈረኝ ፡ ብሎ ፡ ወደ ፡ አባቱ ፡ መሬት ፡ ሄደ ።

ወ ፡ የማይቀረውን ፡ ሞት ፡ ሞተ ፤ ባባቱ ፡ በቅድም ፡ አያቱ ፡ መንገድ ፡ ሄደ ።

1045 ዳዊቱን ፡ ጣል ፡ አርጎ ፡ ሄዷል ፡ ወንድሜ ፤
—እኔም ፡ እሄዳለሁ ፡ ፋንታዬን ፡ ደግሜ ።

ሠ ፡ ድርሻዬን ፡ ደግሜ ፡ ፋንታዬን ፡ ተወጥቼ ፡ እሄዳለሁ ፤ የሚደርሰኝን ፡ አንድ ፡ ሁለት ፡ መዝሙር ፡ ጸልዬ ፡ እንዛለሁ ።

ወ ፡ ደግሞ ፡ እንደ ፡ ወንድሜ ፡ እኅቴ ፡ ፋንታዬ ፡ ከሞተች ፡ ዓለምን ፡ ጥዬ ፡ እሄዳለሁ ፤ እኔም ፡ እንደ ፡ እሷ ፡ በሞት ፡ እከተላለሁ ።

1046 ዳዊቴን ፡ ወሰደው ፡ የማላውቀው ፡ ልጅ ፤
—የማይቀር ፡ ገንዘቤን ፡ ደግሞት ፡ ይስጠኝ ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ ዳዊቴን ፡ ደግሞበት ፡ ይመልስልኝ ፤ አንጡራ ፡ ገንዘቤን ፡ ይስጠኝ ።

ወ ፡ ሞት ፡ የማይቀር ፡ ከሆነ ፡ ጣር ፡ የሌለበትን ፡ መልካም ፡ ሞት ፡ ያድለኝ ፤ ደግ ፡ ዕረፍትን ፡ ይስጠኝ ፤ ሥቃዬን ፡ ሳያበዛ ፡ ይውሰደኝ ።

1047 ዳዊቴን ፡ ደግሜ ፡ አሌፋቱ ፡ ቀረኝ ፤
—እባክህ ፡ አምላኬ ፡ ሔት ፡ ክፍሌን ፡ ንገረኝ ።

ሠ ፡ እባክህ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ከአሌፋት ፡ ውስጥ ፡ ሔት ፡ ክፍልየ ፡ የሚባለውን ፡ የጸሎት ፡ መዝሙር ፡ ግለጽልኝ ።

ወ ፡ አምላኬ ፡ ሆይ ፡ ቤቴ ፡ ንብረቴ ፡ የሚስፋፋበትን ፡ ዕድሌ ፡ የሚቃናበትን ፡ መንገድ ፡ የት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ አስመልክተኝ ፤ ዕጣ ፡ ክፍሌ ፡ የሚሆነውን ፡ የማድርለትን ፡ ጌታ ፡ ግለጥልኝ ።

1048 ዳዊት ፡ እንዴት ፡ ይሙት ፡ ሳንተዋወቀው ፤
—የሚመጣውን ፡ ቀን ፡ በገና ፡ የሚያውቀው ።

ሠ ፡ ወደ ፡ ፊት ፡ የሚሆነውን ፡ ነገር ፡ አስቀድሞ ፡ የሚያውቀውን ፡ ዳ
ዊትን ፡ ያኽል ፡ ሰው ፡ ሳንተዋወቀው ፡ እንዴት ፡ ይሙት ።

ወ ፡ በገና ፡ በመደርደር ፡ ፈጣሪውን ፡ ያመሰግን ፡ የነበረ ፡ መዝሙር ፡ ዐ
ዋቂ ፡ ዳዊትን ፡ ሳንተዋወቀው ፡ ሞተ ።

1049 ድልኸና ፡ ቅቤው ፡ ሞልቶ ፡ በቤትህ ፡
—ምን ፡ ቸገረህና ፡ በባዶ ፡ በላህ ።

ሠ ፡ ወጥ ፡ ሳይጠፋ ፡ መበያ ፡ ሳይታጣ ፤ ለምንድነው ፡ ደረቁን ፡ የምትመገበው ።

ወ ፡ የብዙ ፡ ሰራዊት ፡ የተሟላልህ ፡ ጌታ ፡ ስትሆን ፡ ለምንድነው ፡ ባሬራ ፡
የበላህ?

1050 ድርብ ፡ አያሻንም ፡ ባሁኑ ፡ ጊዜያችን ፤
—ጥበብ ፡ ሆኗልና ፡ የዛሬው ፡ ልብሳችን ።

ሠ ፡ ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ ጥበብ ፡ ኩታ ፡ ለባሽ ፡ ሆኗል ፤ ድርብ ፡
መልበስ ፡ ቀርቷል ።

ወ ፡ በዛሬው ፡ ዘመን ፡ ጥበብን ፡ ለማግኘት ፡ ዕውቀትን ፡ ለማፍራት ፡ ሁላ
ችንም ፡ እንጣጣራለን ፤ ሕፃናት ፡ ጠንክሮ ፡ ለመማር ፡ ታጥቃችሁ ፡
ተነሡ ።

1051 —ድንበሩን ፡ አልፋችሁ ፡ ሑዳዴን ፡ አታብሉ ፤
ክስ ፡ ያቀረብኩ ፡ እንደሁ ፡ ጉድ ፡ እንዳትባሉ ።

ሠ ፡ ወሰን ፡ አልፋችሁ ፡ ሑዳዴን ፡ አታብሉ ፤ ከብቶቻችሁን ፡ ጠብቁ ፤ ከ
ልክሉ ።

ወ ፡ ሕግ ፡ አፍርሳችሁ ፡ ጾም ፡ አትሻሩ ፡ በሑዳዴ ፡ ምድር ፡ ፍሪዳ ፡ አርዳ
ችሁ ፡ ምግብ ፡ አዘጋጅታችሁ ፡ አትብሉ ።

1052 ድንገት ፡ ቢመቻችሁ ፡ ብትጠይቁኝ ፡
—ከታችኛው ፡ ክፍል ፡ ከስሩ ፡ ቤት ፡ ነኝ ።

ሠ ፡ ልትጠይቁኝ ፡ ብትሹ ፡ ከታችኛው ፡ ግቢ ፡ እምድር ፡ ቤቱ ፡ ውስጥ ፡
ፈልጉኝ ፤ እዚያ ፡ እገኛለሁ ።

ወ ፡ ያለሁት ፡ ከወህኒ ፡ ቤት ፡ ነውና ፡ ቢመቻችሁ ፡ ጠይቁኝ ።

1053 ድግህ ፡ አጠረህ ፡ ወይ ፡ ሱሪህ ፡ ጠበበህ ፡ ወይ ፡ የናቴ ፡ ልጅ ፡
ዋሴ ፤
—እኔን ፡ ባጠለቀኝ ፡ ከግር ፡ እስከ ፡ ራሴ ።

ሠ ፡ ለኔ ፡ ይበዛብኛል ፤ መላ ፡ ሰውነቴን ፡ ያጠልቀኛል ፤ ዶሮ ፡ በጋን ፡
ይሆናል ።

ወ ፡ ሐዘን ፡ በዛብኝ ፤ እንባ ፡ እንደ ፡ ውሃ ፡ በቁመቴ ፡ ሙሉ ፡ አጠለቀኝ ።

1054 ድግን ፡ ካጠበቁት ፡ በጣምም ፡ አያስሮጥ ፤
—አትስነፍ ፡ ወዳጄ ፡ ተውተርትረህ ፡ አምልጥ ።

ሠ ፡ ትጥቅህን ፡ ፈተህ ፡ ድግህን ፡ ጠቅለህ ፡ አምረህ ፡ ሩጥ ፤ ባዶ ፡ ወገብህን ፡ ሆነህ ፡ ሽሽ ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ብለህ ፡ ተፍጨርጭረህ ፡ ተግተርትረህ ፡ ከጠላት ፡ እጅ ፡ አምልጥ ፤ አጥብቀህ ፡ ሽሽ ፤ እጅህን ፡ አውጣ ።

1055 ድጓውን ፡ ክተቱት ፡ አስተጋቡት ፡ በጣም ፤
—በቃ ፡ ተከተተ ፡ እንግዲህ ፡ አይመጣም ።

ሠ ፡ ድጓው ፡ ወደ ፡ ማኅደሩ ፡ ገባ ፤ እቦታው ፡ ተመለሰ ፤ ሁለተኛ ፡ አይወጣም ።

ወ ፡ ሊቁ ፡ «በቃ» ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ወረደ ፤ የሱ ፡ ነገር ፡ እንግዲህ ፡ አለቀ ፤ ደቀቀ ።

1056 ድጓ ፡ ጾመ ፡ ድጓ ፡ ተሰቅሎ ፡ ከቤቴ ፡
—እኔን ፡ የሚቈጨኝ ፡ ሳልማር ፡ መቅረቴ ።

ሠ ፡ ድጓ ፡ ጾመ ፡ ድጓ ፡ እያለኝ ፡ መጽሐፍ ፡ ሳላጣ ፡ በስንፍናዬ ፡ ሳልማር ፡ ደንቈሮ ፡ ሆኜ ፡ መቅረቴ ፡ ያሳዝነኛል ።

ወ ፡ ንስሓ ፡ ሳልገባ ፡ ከፈጣሪዬ ፡ ይቅርታን ፡ ሳላገኝ ፡ መሞቴ ፡ ኀሊናዬን ፡ ያስጨንቀዋል ፤ ያሳዝነኛል ።

1057 ጀንበር ፡ በመስኮቷ ፡ ስትወጣ ፡ እያያችሁ ፡
—እንዳትታለሉ ፡ ቀን ፡ አለ ፡ መስሏችሁ ።

ሠ ፡ ፀሐይ ፡ ብዥ ፡ ብዥ ፡ ስትል ፡ እያያችሁ ፡ ቀኑ ፡ ያልመሸ ፡ እንዳይመስላችሁ ፤ ብርሃን ፡ ያለ ፡ መስሏችሁ ፡ ዐጓጕል ፡ እንዳትሆኑ ።

ወ ፡ ደኅና ፡ ጊዜ ፡ ያለ ፡ እንዳይመስላችሁ ፤ ሰዓቱ ፡ አልቋል ፤ ጊዜው ፡ ከፍቷል ።

1058 ጃንሆይ ፡ አይጨክኑ ፡ በጠላት ፡ ወታደር ፤
—ማርኩት ፡ ብለው ፡ ልከው ፡ ቢታረቅ ፡ ደግ ፡ ነበር ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

1 ሠ ፡ ጠላትዎም ፡ ቢሆን ፡ ይቅር ፡ ለእግዚአብሔር ፡ ምሬሃለሁ ፡ ቢሉት ፡ ቢታረቁት ፡ ደግ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ለጠላት ፡ ጊዜ ፡ አይስጡት ፤ አሁኑኑ ፡ ማርካችሁ ፡ አምጡት ፡ ብለው ፡ ጦር ፡ ይላኩ ፤ እጁን ፡ ያሲዙ ።

2 ሠ ፡ ቢስማማ ፡ ዕርቅ ፡ ቢያደርግ ፡ ጠቡ ፡ ቢቀርበት ፡ ደግ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ሰላምን ፡ የማይፈልግ ፡ ከሆነ ፡ ጠላታችንን ፡ ወግቶ ፡ ድል ፡ ማድረግና ፡ ማረቅ ፡ የተገባ ፡ ነው ።

1059 ጃንሆይ ፡ ቀሚስዎ ፡ ቁመቱ ፡ ቢረዝም ፡
—ዘርፋፋ ፡ ተባሉ ፡ በመላው ፡ ዓለም ።

ሠ ፡ ጕታታ ፡ ዘርፋፋ ፡ ተባሉ ፤ ቀልጣፋነትዎ ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ዘረ ፡ መልካም ፡ መሆንዎ ፡ በዓለም ፡ ታወቀ ፤ የከበረ ፡ ደም ፡ እንዳ
ለዎ ፡ ተረጋገጠ ፤ እግዚአብሔር ፡ በልጅዎ ፡ አከበረዎ ።

1060 —ጃንሆይ ፡ ጥላ ፡ አይወዱም ፡ ጣይ ፡ ካልመጣባቸው ፤
ባርኔጣ ፡ ይዘዋል ፡ አውልቀው ፡ በጃቸው ።

ሠ ፡ ጃንሆይ ፡ እጅግ ፡ ጣይ ፡ ካልሆነ ፡ ሙቀት ፡ ካልበዛና ፡ ቀኑ ፡ ካልገ
ረረ ፡ ጥላ ፡ ለመያዝ ፡ አይፈቅዱም ፤ አይወዱም ።

ወ ፡ ጃንሆይ ፡ ተጋፍተው ፡ ካልደፈሯቸው ፡ አይነኩም ፤ ካልደረሱባ
ቸው ፡ በሰው ፡ አይደርሱም ።

1061 ጃኖማ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ እለብስ ፡ የለም ፡ ወይ ፤
—ብርቅ ፡ ይሆንብኛል ፡ ጥበብ ፡ ለብሰው ፡ ሳይ ። (ብ፡ጌ፡ኀ፡ወ፡ሥ)፡

ሠ ፡ ጥበብ ፡ ኩታ ፡ በለበሱ ፡ ሰዎች ፡ እቀናለሁ ፤ ድንቅ ፡ ነገር ፡ መስሎ ፡
ይታየኛል ።

ወ ፡ ዕውቀት ፡ ያለው ፡ የተማረ ፡ ሰው ፡ ሳይ ፡ እደሰታለሁ ፤ የጥበብ ፡ ቤተ ፡
ሰብ ፡ ባለመሆኔ ፡ እቈጫለሁ ።

1062 ጆ(ጐ)ሮዬ ፡ እየሰማ ፡ እያየሁት ፡ ባይኔ ፡
—ሳቅነው ፡ የገደለኝ ፡ መች ፡ አጣሁት ፡ እኔ ።

ሠ ፡ ሆዴ ፡ እያወቀ ፡ ልቤ ፡ እየተረዳው ፡ ከማይሆን ፡ ሰው ፡ ገጥሜ ፡ ለሞት ፡
በቃሁ ።

ወ ፡ ሣቅ ፡ ልቤን ፡ አፈረሰው ፤ ቧልትና ፡ ዋዛ ፡ ፈዛዛ ፡ መሣቅ ፡ መሣሣቅ ፡
ወደ ፡ ክፉ ፡ ነገር ፡ አደረሰኝ ።

1063 ገለውሃል ፡ ብዬ ፡ በጣሙን ፡ ሳዝን ፡
—ማርከውህ ፡ አገኘሁ ፡ እሠይ ፡ ወዳጄን ።

ሠ ፡ ገድለውሃል ፡ ብዬ ፡ ሳዝን ፡ ስተክዝ ፡ ነፍስህ ፡ ድኖ ፡ ተማርከህ ፡ በማ
ግኘቴ ፡ ደስ ፡ አለኝ ።

ወ ፡ ማርን ፡ ከውሃ ፡ ውስጥ ፡ አገኘሁ ፤ የምወደውን ፡ ጠጅ ፡ ጠጣሁ ፤ ተደ
ሰትኩ ።

1064 ገላጋይ ፡ መች ፡ ጠፉ ፡ ሰው ፡ ሞልቶ ፡ በደጅ ፡
—አልገላገልም ፡ ብላ ፡ ሄደች ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ ያገር ፡ ሽማግሌ ፡ ቢለምናት ፡ ጨዋ ፡ የተባለ ፡ ተሰብስቦ ፡ ቢመከ
ራት ፡ እንቢ ፡ ብላ ፡ ሄደች ።

ወ ፡ በወሊድ ፡ ተጨንቃ ፡ ሳትገላገል ፡ ነፍሰ ፡ እግዚአብሔር ፡ ይዛ ፡ ሞ
ተች ፤ አሳዛኝ ፡ ዕረፍት ፡ ዐረፈች ።

1065 ገበያ ፡ ወጥቼ ፡ ብመለከተው ፡
—በጣም ፡ በዝቶ ፡ አየሁት ፡ ሥጋ ፡ ፈላጊው ።

ሠ ፡ ገበያ ፡ ሄጄ ፡ ብዙ ፡ ሥጋ ፡ ፈላጊ ፡ አይቼ ፡ መጣሁ ፤ ሁሉ ፡ ሥጋ ፡
ጠያቂ ፡ ነው ።

ወ ፡ ባሁኑ ፡ ጊዜ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ ሕፃን ፡ ሽማግሌው ፡ ለሥጋዊ ፡ ኑ
ሮው ፡ ታታሪ ፡ ነው ፤ ለነፍሱ ፡ የሚያስብና ፡ እሞታለሁ ፡ የሚል ፡ የለም ።

1066 ገብስ ፡ አርሚ ፡ ሲለኝ ፡ ልቤ ፡ እየታከተ ፡
ጤፍ ፡ አርሚ ፡ ሲለኝ ፡ ልቤ ፡ እየታከተ ፡
ነዶ ፡ አግዝ ፡ ሲለኝ ፡ ልቤ ፡ እየታከተ ፡
—እንግዲህ ፡ ልረፈው  መከር  ተከተተ ።

ሠ ፡ አረም ፡ ከማረም ፡ ነዶ ፡ ከመሸከም ፡ ዐረፍሁ ፤ መከር ፡ ተሰበሰበ ፤
አዝመራችን ፡ አልቆ ፡ በውጭ ፡ ያለው ፡ እኽል ፡ ሁሉ ፡ እጐተራ ፡ ገባ ።
ወ ፡ ሥራ ፡ ሲያዘኝ ፡ ይሰለቸኝ ፡ የነበረው ፡ ትጉሁ ፡ ባሌ ፡ ሞተ ፤ መቃ
ብር ፡ ገባ ፤ ብቻዬን ፡ ቀረሁ ።

1067 ገና ፡ ለሚመጣው ፡ ለማታው ፡ እንግዳ ፡
—እንዳትዘነጊ ፡ አለብን ፡ ፍሪዳ ።

ሠ ፡ ማታ ፡ የሚመጣው ፡ እንግዳችን ፡ ፍሪዳ ፡ የሚያስፈልገው ፡ ነው ፤
አስቢበት ፤ እንዳትዘነጊ ።
ወ ፡ በሕይወታችን ፡ መጨረሻ ፡ የሚያስፈራ ፡ የሞት ፡ ዕዳ ፡ አለብን ፤
ዕድሜያችን ፡ ሲያልቅ ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ የሞት ፡ ፍዳ ፡ ይጠብቀናል ፤
ማሰብ ፡ መሥጋት ፡ ያሻናል ።

1068 ገና ፡ ሳይሠራ ፡ ሳይዋቀር ፡ ቤቱ ፡
—በማገር ፡ ተቀምጠው ፡ አለቃ ፡ ተቤቱ ። (1) (ን. ኃ. መ)

ሠ ፡ አንዱ ፡ ሳይያዝ ፡ ገና ፡ በመማገር ፡ ሳለ ፡ አለቃ ፡ በሚሠሩት ፡ ቤት ፡
ይኰሩ ፡ ዠመር ።
ወ ፡ አለቃ ፡ እንዲህ ፡ የሚታበዩት ፡ ማን ፡ በሚገዛው ፡ አገር ፡ ላይ ፡ ተቀ
ምጠው ፡ ነው ። ገዣቸውስ ፡ ማን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ዘንግተው ፡ ነው ።

1069 —ገናን ፡ ዘመድ ፡ የለኝ ፡ ወዴት ፡ እውላለሁ ፤
ከድንጋይ ፡ ሥር ፡ ሆኘ ፡ አሳልፈዋለሁ ።

ሠ ፡ የገና ፡ ለት ፡ ሕዝቡ ፡ ሲበላ ፡ ሲጠጣ ፡ እኔ ፡ ከድንጋይ ፡ አጠገብ ፡
ተቀምጬ ፡ ልውል ፡ ነው ፤ ዓመት ፡ በዓሉ ፡ ዐውዳመት ፡ ሳይመስለኝ ፡
ሊቀር ፡ እኮ ፡ ነው ።
ወ ፡ ታላቅ ፡ ክብር ፡ ያለው ፡ ዘመድ ፡ ወገን ፡ የለኝ ፤ እንደ ፡ ምን ሆኜ ፡ እ
ኖራለሁ ፤ ማንስ ፡ ይረዳኛል ።

1070 ገና ፡ ጣይ ፡ ስትወጣ ፡ እንዲህ ፡ ያላበው ፡
—ቀትር ፡ ሲሆንማ ፡ የት ፡ ሊገባ ፡ ነው ። (አ. አ.)

ሠ ፡ ገና ፡ ሲነጋ ፡ ጨረር ፡ ሳትወጣ ፡ እንዲህ ፡ የወበቀው ፡ ቀኑ ፡ ሲገር ፡
ቀትር ፡ ሲሆን ፡ የት ፡ ሊደርስ ፡ ነው ።
ወ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ የምታበረታታው ፡ ጦር ፡ እንዲህ ፡ ያሸበረው ፤ አባ ፡
ቀትርማ ? ፡ ሲመጣ ፡ ጣሊያን ፡ እንዴት ፡ ይሆን ፤ የት ፡ ይደርስ ።

(1) በንጉሥ ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ ዘመነ ፡ መንግሥት ፡ ይኖሩ ፡ የነበሩ ፡ አለቃ ፡ ወልደ ፡
ጊዮርጊስ ፡ የሚባሉ ፡ መምሕር ፡ ቤት ፡ ለመሥራት ፡ መማገር ፡ ይዘው ፡ ሳሉ
ሲጠሩ ፡ ፈጥነው ፡ ባለመምጣታቸውና ፡ በመንጓደዳቸው ፡ ንጉሥ ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡
ያደረጉባቸው፡ ፡ተግሣጽ ፤

1071 ገንዘብህን ፡ ለሽቶ ፡ እንዳታባክን ፡
—በስኂን ፡ ታሽታለች ፡ ወይዘሮ ፡ መነን ። (አ ፡ በ) ፡

ሠ ፡ ሽቶ ፡ በመግዛት ፡ ገንዘብህን ፡ አታባክን ፤ ወይዘሮ ፡ መነን ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ መልካም ፡ መዐዛ ፡ ያለውን ፡ የስኂን ፡ ሽቶ ፡ ተቀብታለች ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ስኂን ፡ መነንን ፡ ታላቅ ፡ ግብረ ፡ ገብነት ፡ በመላበት ፡ መልካም ፡ አስተዳደግ ፡ ቀጥታ ፡ አሳድጋታለች ፤ በጠባይዋ ፡ ሥጋት ፡ አይደርብህ ።

1072 ጉ(ጐ)ልበቴ ፡ ፊት ፡ ሂዶ ፡ በኋላ ፡ ቀርቼ ፡
—በጭቃ ፡ እለፋለሁ ፡ መሻገሪያ ፡ አጥቼ ።

ሠ ፡ መልካው ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ከጭቃው ፡ ውስጥ ፡ ገብቼ ፡ እማስናለሁ እለፋለሁ ።

ወ ፡ መመኪያዬ ፡ ሞቶብኝ ፡ ይኸው ፡ በጭቃ ፡ ሹም ፡ እየታዘዝሁ ፡ እንገላታለሁ ፤ እታሰራለሁ ፤ እፈታለሁ።

1073 ጉ(ጐ)ዞ ፡ በዛ ፡ ብለው ፡ ምኒልክ ፡ አይታክቱ ፤
—ባሕር ፡ ታዘልቃለች ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ጃንሆይ ፡ ለመንገድ ፡ አይሰልቹ ፤ ፀሓይዋ ፡ እንደ ፡ ሆነች ፡ አልተሸቈለቈለችም ፤ ገና ፡ ባሕር ፡ ታደርሳለች ።

ወ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ ገና ፡ እስከ ፡ ባሕረ ፡ ኤርትራ ፡ ሳትለይ ፡ ጠንክራ ፡ አብራ ፡ የምትዘምት ፡ ናት ፤ ጠላትን ፡ ካገር ፡ ጠርገው ፡ ያስወጡ ።

1074 ጋላ ፡ ብርድ ፡ አይችልም ፡ ከቤቱ ፡ ከወጣ ፤
—እዩት ፡ ገል ፡ አንሥቶ ፡ እሳት ፡ ሊጭር ፡ መጣ ።

ሠ ፡ እሳት ፡ ለመውሰድ ፡ ገል ፡ ይዞ ፡ መጣ ።

ወ ፡ ገላን ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ የሚያስከትለውን ፡ አዙሮ ፡ ማየት ፡ ተስኖት ፡ ጠብ ፡ ለማንሣት ፡ እዩት ፡ ጦር ፡ ይዞ ፡ ሲመጣ ፤ አንቀኸርቅሮታልና ፡ ምሱን ፡ ሊቀበል ፡ ነው ።

1075 ጋናችን ፡ ተሰብሮ ፡ አካፋያችን ፡
—ማን ፡ ዕቃ ፡ ይለናል ፡ እንግዲህ ፡ እኛን ።

ሠ ፡ እንግዲህ ፡ ዕቃ ፡ የሚለምነን ፡ ሰው ፡ የለም ፤ ጋናችን ፡ ተሰብሯል ።

ወ ፡ መፈሪያችን ፡ መከበሪያችን ፡ ከሞተ ፡ እንግዲህ ፡ እኛን ፡ ማን ፡ ከሰው፡ ይቈጥረናል ፤ ማንስ ፡ ከቁም ፡ ነገር ፡ ያገባናል ።

1076 ጌታው ፡ ከብቶችዎን ፡ ማስጠበቅ ፡ ትተው ፡
—ድኻውን ፡ አፋጁት ፡ እኽል ፡ አብልተው ።

ሠ ፡ ከብቶችዎ ፡ የሰው ፡ እኽል ፡ ሲያጠፉ ፡ ሐይ ፡ ባለማለትዎ ፡ ድኻው ፡ ተማረረ ፤ አዘነብዎ ።

ወ ፡ ያበሉት ፡ ያጠጡት ፡ ሕዝብዎ ፡ በሞትዎ ፡ እጅግ ፡ አዘነ ፤ እንባ ፡ በንባ ፡ ተራጨ ።

1077 ጌታው ፡ ደጃች ፡ ዘውዴ ፡ እንዲህ ፡ ነው ፡ ሰልፍዎ ፤
—ጋሻዎን ፡ ፊት ፡ አርገው ፡ ፈረስ ፡ በኋላዎ ።

ሠ ፡ ሰልፍዎ ፡ የተዘባረቀ ፡ ነው ፤ ጋሻ ፡ በኋላ ፡ ፈረስ ፡ ከፊት ፡ በመሆን ፡ ፈንታ ፤ ፈረስ ፡ በኋላዎ ፡ ጋሻ ፡ በፊትዎ ፡ አድርገዋል ።

ወ ፡ ጀግንነትዎ ፡ ታላቅ ፡ ነው ፤ የጠላትን ፡ ጋሻ ፡ እንደ ፡ ወንፊት ፡ መበሳሳት ፡ ልማድዎ ፡ ነው ፤ እጦር ፡ ሜዳ ፡ ገብተው ፡ በጀግንነት ፡ ይዋጋሉ ።

1078 ጌታ ፡ የወሰነው ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ላይቀር ፡
—ባይወጣስ ፡ ባይወርድስ ፡ ባይለፋስ ፡ ምን ፡ ነበር ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡ (ዘለ ፡ ቍ ፡ 857) ፡

ሠ ፡ ማናቸውም ፡ ነገር ፡ ያለጌታ ፡ ፈቃድ ፡ የማይደረግ ፡ መሆኑን ፡ ሲያ ውቅ ፡ ባይወጣ ፡ ባይወርድ ፡ ባይለፋ ፡ ምን ፡ ነበር ።

ወ ፡ ጌታው ፡ ያሰበው ፡ ጒዳይ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የማይቀር ፡ መሆኑን ፡ እያ ወቀ ፡ ዐጒል ፡ አሳብ ፡ አምጥቶ ፡ እስከ ፡ መደብደብና ፡ እስከ ፡ መመ ታት ፡ ባይደርስ ፡ ደግ ፡ ነበር ።

1079 ጌታ ፡ የውሽ ፡ ሄዱ ፡ የዳ ፡ ጥለውኝ ፤
—ውሃ ፡ ዋና ፡ እንኳ ፡ አላውቅ ፡ ዋ ፡ ምን ፡ ይበጀኝ ።

ሠ ፡ ወንዙ ፡ «የዳ» ፡ የተባለው ፡ ሞልቷል ፤ መዋኘት ፡ አልችልም ፤ ጌታዬ ፡ ብቻቸውን ፡ እማዶ ፡ ናቸው ፤ ምን ፡ ይሻለኛል ፤ ማን ፡ ያሻግረኛል ።

ወ ፡ ጌታዬ ፡ ጥለውኝ ፡ ሞቱ ፡ እኔ ፡ ችግር ፡ አላውቅ ፤ የሰው ፡ እጅ ፡ ማየት ፡ አልወድ ፤ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ይዋጠኝ ፡ ይሆን ፤ ይህን ፡ ዓለም ፡ እን ዴት ፡ እዘልቀው ፡ ይሆን ።

1080 ጌታዬ ፡ ምኒልክ ፡ ጃኖ ፡ አለምንሁም ፡ በቅሎ ፡ አለምንሁም ፤
—ዓምና ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ዘንድሮስ ፡ የለሁም ።

ሠ ፡ ገንዘብ ፡ የነበረዎት ፡ አዱኛ ፡ የተረፈዎት ፡ ዓምና ፡ ነበር ፤ ዘንድሮስ ፡ ተቸግረዋል ፤ ለራስዎም ፡ አይበቃዎትም ፤ አልቋል ።

ወ ፡ በሕይወተ ፡ ሥጋ ፡ የነበሩት ፡ ዓምና ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ዘንድሮ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ የሉም ፤ መሞትዎን ፡ ኀሊናችን ፡ ዐውቆታል ፤ ልቦናችን ፡ ተረድቶታል ።

1081 ጌታዬ ፡ ምኒልክ ፡ እግዚአብሔር ፡ ያጥናዎ ፤
—በየበሩ ፡ ቋሚ ፡ አንድ ፡ ወንድም ፡ ሞተዎ ።

ሠ ፡ በየጠሩ ፡ በር ፡ አለሁ ፡ የሚል ፡ ብዙ ፡ ጒራ ፡ የሚመልስ ፡ ታማኝ ፡ ወንድም ፡ ሞተብዎ ።

ወ ፡ ይተማመኑበት ፡ የነበረው ፡ ወንድምዎ ፡ ቃኘው ፡ መኰንን ፡ ሞተ ፤ እጅግ ፡ ተጐዱ ፤ እግዚአብሔር ፡ ያጥናዎ ።

1082 ጌታዬ ፡ ነበሩ ፡ ገዥዬ ፡ ነበሩ ፡ ወዲህም ፡ ዘመዴ ፤
—መንገድ ፡ አወጡና ፡ ሄዱበት ፡ በሆዴ ።

ሠ ፡ የኔ ፡ ጌታ ፡ በሆዴ ፡ ላይ ፡ መንገድ ፡ ከፈቱ ፤ ጐዳና ፡ አበጁ ።

ወ ፡ ያበሉኝ ፡ ያጠጡኝ ፡ የነበሩት ፡ ጌታዬ ፡ ሞቱብኝ ፤ እንግዲህ ፡ ምን ፡ ይበጀኛል ።

1083 ጌታዬም ፡ እንደ ፡ ሰው ፡ ባሰት ፡ እየማለ ፡
—አንድ ፡ እንጀራ ፡ ብለው ፡ ሙት ፡ የለኝም ፡ አለ ።

ሠ ፡ ጌታዬም ፡ አንድ ፡ እንጀራ ፡ እባክህ ፡ ስጠኝ ፡ ብዬ ፡ ብለምነው ፡ ምንም ፡ የለኝም ፡ አለኝ ፤ ሙት ፡ ብሎ ፡ ማለ ።

ወ ፡ ፈጣሪዬን ፡ እንጀራ ፡ አሳልፍልኝ ፡ ብዬ ፡ ብጸልይ ፡ ተድላ ፡ ደስታን ፡ ሳያድለኝ ፡ ቀረ ፤ እንደዚሁ ፡ ተጐላልተህ ፡ ተቸግረህ ፡ ሙት ፡ አለኝ ።

1084 ጌታዬ ፡ ያንተን ፡ ቤት ፡ መላው ፡ ሲዘርፈው ፡
—እኔም ፡ ላም ፡ አመጣሁ ፡ ወርሬ ፡ እንደ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ጌታዬ ፡ ቤትህ ፡ ሲዘረፍ ፡ ሲበዘበዝ ፡ አይቼ ፡ እኔም ፡ አንድ ፡ ላም ፡ ነድቼ ፡ አመጣሁ ።

ወ ፡ እኔም ፡ ለማማት ፡ ለትዝብት ፡ ወደዚያው ፡ መጣሁ ።

1085 ጌታዬ ፡ ይወቁት ፡ ዐይኔ ፡ ጠፋልዎ ፡
—የፈተፈቱበት ፡ ነክቶብኝ ፡ ጣትዎ ።

ሠ ፡ ፍትፍት ፡ በያዙበት ፡ ጣትዎ ፡ የነኩት ፡ ዐይኔ ፡ መጥፋቱ ፡ ነው ፤ ያቃጥለኛል ፤ ይለበልበኛል ።

ወ ፡ ከፍትፍቱ ፡ እየጠቀለለ ፡ ከጮማው ፡ እየቈረጠ ፡ ያጐርሠኝ ፡ የነበረው ፡ ጣትዎ ፡ ሞተው ፡ በመገነዙ ፡ በመፍረሱ ፡ ዐይኔ ፡ አልቅሶ ፡ መጥፋቱ ፡ ነው ፤ ባዬ ፡ አልታገድ ፡ አለኝ ።

1086 ግራርና ፡ ወይራ ፡ ሞልቶ ፡ በደጅዎ ፡
—ንጉሥ ፡ የሰው ፡ ዕንጨት ፡ ምነው ፡ ማንደድዎ ።

ሠ ፡ ማገዶ ፡ ሳይጠፋ ፡ በደጅዎ ፡ ግራርና ፡ ወይራ ፡ ሞልቶ ፡ ለምን ፡ ሰው ፡ የሰበረውን ፡ ዕንጨት ፡ ይማግዳሉ ።

ወ ፡ ንጉሥ ፡ ሆይ ፡ ለምን ፡ ሰውን ፡ እንደ ፡ ዕንጨት ፡ ያነዱታል ፤ ሕዝብ ዎን ፡ በሳት ፡ ያቃጥሉታል ።

1087 ግራ ፡ ቀኝ ፡ ደጋፊ ፡ ሳሉ ፡ አሽከሮችዎ ፡
መልኩ ፡ ሰው ፡ መሆኑን ፡ ሲያውቀው ፡ ልቦናዎ ፡
—ልጆች ፡ አስቀድመው ፡ ምነው ፡ መሄድዎ ።

ሠ ፡ መሸምገልዎን ፡ መድከምዎን ፡ ልብዎ ፡ እያወቀ ፡ ደጋፊዎችዎን ፡ ትተው ፡ ሊረዱዎት ፡ የማይችሉትን ፡ ልጆች ፡ አስቀድመው ፡ ለምን ፡ ይሄዳሉ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ ጌታዬ ፡ ልጆችዎ ፡ በሞት ፡ ሲቀድሙ ፡ ርስዎም ፡ ሳይሰነብቱ ፡ ተከትለው ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተለዩ ፤ ዘር ፡ ሳይተርፍዎት ፡ ቀረ ።

1088 ግርማዊ ፡ አባ ፡ ጠቅል ፡ በጣም ፡ ጻድቅ ፡ ነዎ ፤
—ኢየሱስ ፡ ሥራዎን ፡ የገለጠልዎ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ግርማዊ ፡ በጣም ፡ ምእመን ፡ ነዎ ፤ ኢየሱስ ፡ ሥራውን ፡ ታምራቱን ፡ ገለጠልዎ ።

ወ ፡ መልካም ፡ ሥራዎ ፡ ጽኑ ፡ ሃይማኖትዎ ፡ የኢየሱስን ፡ ቤተ ፡ መቅደስ ፡
በማሳነጽዎ ፡ ተገለጠ ፤ ታወቀ ።

1089 ግርማዊት ፡ እቴጌ ፡ ጥሪውን ፡ አክብረው ፡ ቢመጡ ፡ ልጅዎ ፡
—እንዴት ፡ ማሰናበት ፡ ቀረ ፡ ከቤትዎ ።

ሠ ፡ ልጅዎ ፡ ሊጠይቁዎትና ፡ ሊያዩዎት ፡ ቢመጡ ፡ ለምን ፡ ሳያሰናብቷ
ቸው ፡ ቀሩ ፤ ለምን ፡ ወደ ፡ ቤታቸው ፡ አልመለሷቸውም ።

ወ ፡ ልጅዎ ፡ ልዑል ፡ ሣህለ ፡ ሥላሴ ፡ እንደ ፡ ርስዎ ፡ ከዚህ ፡ ዓለም ፡ ተ
ለዩ ፤ ሳይሰነብቱ ፡ በሕፃንነት ፡ ባጭር ፡ ተቀጩ ።

1090 ግባተ ፡ መሬቱን ፡ አትድገሙ ፡ እናንተ ፤
—ታዞ ፡ ሄዷል ፡ እንጂ ፡ ልጄ ፡ መቼ ፡ ሞተ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 493 ፡ 569) ፡

ሠ ፡ ልጄ ፡ የሄደው ፡ በትእዛዝ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ ወደ ፡ ሞት ፡ አገር ፡ አይደ
ለም ፤ ጸሎተ ፡ ፍትሐት ፡ አታድርሱ ፡ ግባተ ፡ መሬት ፡ አትድገሙ ።

ወ ፡ ልጄን ፡ ዐዞ ፡ ይዞት ፡ ሄደ ፤ የባሕር ፡ አውሬ ፡ ወሰደው ።

1091 ግድግዳውም ፡ ቆመ ፥ ባጡም ፡ ተዋቀረ ፥ ዋ ፡ ምን ፡ ይከደናል ፤
—ማጭድስ ፡ ካመጣህ ፡ ና ፡ እኛ ፡ ሣር ፡ አይተናል ።

ሠ ፡ ማጭድ ፡ ካለህ ፡ ሣር ፡ አይጠፋም ፤ ና ፡ እኛ ፡ ያየንበትን ፡ ቦታ ፡ እና
ሳይሃለን ።

ወ ፡ እኛ ፡ አሳራችን ፡ በዝቷል ፤ መከራ ፡ ሥቃይ ፡ አይተናል ፤ የምናደር
ገውን ፡ አጥተናል ።

1092 ግድግዳው ፡ ቢረዝም ፡ ምን ፡ ባጡ ፡ ቢያምር ፡
—የምድር ፡ ቤት ፡ ነውና ፡ መፍረሱም ፡ አይቀር ።

ሠ ፡ ቤት ፡ መሠረቱ ፡ ግድግዳው ፡ ካልጠነከረ ፡ ምንም ፡ ጣራው ፡ ቢያ
ምር ፡ እምብዛም ፡ አይቈይም ፤ ቶሎ ፡ ይፈርሳል ፤ ዕድሜ ፡ የለውም ።

ወ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ ላይ ፡ ትዳር ፡ ቢያምር ፡ ንብረት ፡ ቢዳብር ፡ ገንዘብ ፡
ቢጠራቀም ፤ ሀብት ፡ ቢሰበሰብ ፡ ውሎ ፡ አድሮ ፡ መፍረሱ ፡ አይቀ
ርም ።

1093 ጐመን ፡ ቀቅል ፡ አሉኝ ፡ ምን ፡ ጊዜ ፡ ሊበስል ፤
—ይኸንን ፡ ቀንጥሼ ፡ እዘልቀው ፡ ይመስል ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አሁን ፡ ባሁን ፡ ጐመኑን ፡ ቀንጥሼ ፡ ከትፌ ፡ ለመቀቀልና ፡ ለማብ
ሰል ፡ አልችልም ፤ ሰዓት ፡ ደርሷል ።

ወ ፡ ይኸን ፡ ክፉ ፡ ቀን ፡ የማልፈው ፡ አይመስለኝም ፤ እንዴት ፡ እንደም
ዘልቀው ፡ አላውቅም ።

1094 ጐራዴ ፡ መታጠቅ ፡ ሸክም ፡ መሰለኝ ፤
—እስኪ ፡ እንዳባታየር ፡ መተህ ፡ አሳየኝ ። (1)

---

(1) የፈረስ ፡ ስማቸው ፡ አባታየር ፡ ስለ ፡ ሆነው ፡ ስለ ፡ ፈታውራሪ ፡ አየለ ፡ የተነገረ ።

ሠ ፡ ጐራዴ ፡ መታጠቅ ፡ አላውቅበትም ፤ ሸክም ፡ ይመስለኛል ፤ እስኪ ፡ እንደ ፡ አባታየር ፡ ያለውን ፡ ትጥቅ ፡ ናና ፡ አሳየኝ ።

ወ ፡ እንደ ፡ አባታየር ፡ በጐራዴህ ፡ ክንፍ ፡ ክንፉን ፡ ብለህ ፡ ቋንዣ ፡ ቋንዣውን ፡ ሙተህ ፡ አሳየኝ ፤ አንዠቴን ፡ አርሰኝ ።

1095 ጐባጣ ፡ ነህ ፡ አሉኝ ፤ ጐባጣ ፡ ነኝ ፡ ወይ ፤
—ከሰው ፡ አልጣላም ፡ ዠርባዬን ፡ ሳላይ ። (አ ፡ መ) ፡

ሠ ፡ ጐባጣ ፡ መሆን ፡ አለመሆኔን ፡ ሳላውቅ ፡ ከሰው ፡ ደርሼ ፡ አልጣላም ፤ ዐርፌ ፡ እቀመጣለሁ ።

ወ ፡ ወገን ፡ ሳላበጅ ፡ ጓደኛ ፡ ሳይኖረኝ ፡ በከንቱ ፡ ደርሼ ፡ አምባጓሮ ፡ አላነሣም ።

1096 ጐንደር ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ ያንተማ ፡ አገርህ ፡
—ከዚህ ፡ ጭቅነቱን ፡ ማነው ፡ የሾመህ ።

ሠ ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ባልተወለድክበት ፡ ቦታ ፡ ጭቃ ፡ ሹምነቱን ፡ የሰጠህ ፡ ማነው ፤ ለዚህ ፡ ወግና ፡ ማዕርግ ፡ ማን ፡ አደረሰህ ።

ወ ፡ በሰው ፡ አገር ፡ ዘመድ ፡ አዝማድ ፡ በሌለበት ፡ ሞተህ ፡ ወደ ፡ መቃብር ፡ ገባህ ፤ ዐፈር ፡ ሆነህ ፡ ቀረህ ።

1097 ጐንደር ፡ እንሂድ ፡ ብሎ ፡ ካገሬ ፡ አውጥቶኝ ፡
—እሱ ፡ መቄት ፡ ገባ ፡ ጨጭሆ ፡ ጥሎኝ ።

ሠ ፡ ካገሬ ፡ አውጥቶኝ ፡ እኔን ፡ ጨጭሆ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ጥሎኝ ፡ እሱ ፡ ወደ ፡ መቄት ፡ ሄደ ፤ በማላውቀው ፡ አገር ፡ አውላላ ፡ ሜዳ ፡ ላይ ፡ ተወኝ ።

ወ ፡ ወደ ፡ ጐንደር ፡ ሲሄድ ፡ መንገድ ፡ ላይ ፡ ሞተ ፤ ተቀበረ ፤ መቃብር ፡ ገባ ።

1098 ጐንደርን ፡ ለማልቀስ ፡ ብሄድ ፡ በቀደም ፡
—ነዶ ፡ አሮ ፡ አገኘሁት ፡ ተቃጥሎ ፡ በጣም ። (1) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 304) ፡

ሠ ፡ ከለቅሶው ፡ ለመድረስ ፡ ብሄድ ፡ አዘነተኛው ፡ እጅግ ፡ አዝኖ ፡ ከስሎ ፡ በሐዘን ፡ ተጨብጦ ፡ አገኘሁት ።

ወ ፡ ጐንደር ፡ አገሬን ፡ ለማየት ፡ ብሄድ ፡ ቤቱ ፡ ተቃጥሎ ፡ ሕዝቡ ፡ ተሰዶ ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ፤ ያለሰው ፡ ቀርቶ ፡ አየሁት ።

1099 ጐንጆች ፡ ሲሳደቡ ፡ ለነገም ፡ አይሉ ፤
—ስጊን ፡ በጸሎቱን ፡ ቈማጣ ፡ አሉት ፡ አሉ ። (2) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 151) ፡

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ራስ ፡ ዐሊን ፡ ድል ፡ አድርገው ፡ ለመንገሥ ፡ ባሰቡ ፡ ጊዜ ፡ ጐንደሮች ፡ የንጉሥ ፡ የዘር ፡ ደም ፡ የለዎትምና ፡ አይገባዎም ፡ በማለት ፡ ተቃወሟቸው ። በኋላ ፡ ግን ፡ አባ ፡ ሰላማ ፡ ተከራክረው ፡ እንዲነግሡ ፡ ሆነ ፤ ይሁን ፡ እንጂ ፡ ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ቂም ፡ ይዘው ፡ ኖሮ ፡ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ ጐንደርን ፡ አቃጠሉት ፤ ካህናቱንም ፡ አስደበደቡት ፤ አንድ ፡ ዓመት ፡ ካ፩ ፡ ወር ፡ ያኽልም ፡ ከተማው ፡ ምድረ ፡ በዳ ፡ ሆኖ ፡ ከቈየ ፡ በኋላ ፡ በዚህ ፡ ጊዜ ፡ ከመከራው ፡ ያመለጠች ፡ ሴት ፡ ያለቀሰችው ።

(2) ስጊን ፡ በጸሎቱ ፡ የሚባለውን ፡ ሰው ፡ ቆማ ፡ ወደሚባል ፡ ቀበሌ ፡ ሲሄድ ፡ ጠላቶቹ ፡ ገድለው ፡ ስለ ፡ ጣሉት ፡ አንዲት ፡ አልቃሽ ፡ የገጠመችው ።

ሠ ፡ የጐንጂ ፡ ሰዎች ፡ ይሉኝታ ፡ የላቸውም ፡ ተሳዳቢዎች ፡ ናቸው ፡ ስኒን ፡ በጸሎቱንም ፡ እንኳ ፡ ቈማጣ ፡ ብለው ፡ ሰደቡት ፡ አሉ ።

ወ ፡ ጐንጆች ፡ ስኒን ፡ በጸሎቱ ፡ የሚባለውን ፡ ሰው ፡ ደብድበው ፡ ቆማ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ጥለውት ፡ ሄዱ ።

1100 ጐድን ፡ ተዳቢቱን ፡ ተፍትፊህ ፡ ጥበሰው ፤
—እስኪበላ ፡ አሞቱን ፡ አያውቅምና ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ሥጋው ፡ በሐሞት ፡ መለወስ ፡ አለመለወሱን ፡ ሰው ፡ ካልቀመሰውና ፡ ካልበላው ፡ አስቀድሞ ፡ አያውቀውም ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሲበላና ፡ ሲጠጣ ፡ ሞት ፡ ያለበት ፡ አይመስለውም ፤ ለሥጋው ፡ እንደ ፡ ጣረ ፡ እንደ ፡ ጋረ ፡ ሞት ፡ ድንገት ፡ ነጥቆ ፡ ይወስደዋል ።

1101 ጐጃ(ዣ)ምስ ፡ ምን ፡ አለ ፡ ዳሞትስ ፡ ምን ፡ አለ ፡ ይህንን ፡ ሲሰማ ፤
—የጁ ፡ ተለቀሰ ፡ የበለው ፡ ተሰማ ።

ሠ ፡ የጐዣሙና ፡ የዳሞቱ ፡ ባላባት ፡ በለው ፡ ተሰማ ፡ ሞቶ ፡ የጁ ፡ ላይ ፡ የለቀስተኛው ፡ ውሎ ፡ ተዋለ ፤ ሲለቀስ ፡ ሰነበተ ።

ወ ፡ ስላበላ ፡ ስላጠጣ ፡ ስለጁ ፡ ቸርነት ፡ ተለቀሰለት ።

1102 ጐጃ(ዣ)ምና ፡ ዳሞት ፡ ሲሄድ ፡ በመብራት ፡
—ማታ ፡ አይተው ፡ ሄዱ ፡ አሉ ፡ እኒያ ፡ የኔ ፡ አባት ።

ሠ ፡ አባቴ ፡ ቀኑ ፡ መሽቶ ፡ በጨለማ ፡ ዕንቅፋት ፡ እንዳይመታቸው ፡ እያሰሉ ፡ በዝግታ ፡ እየተራመዱ ፡ ሄዱ ፡ አሉኝ ።

ወ ፡ አባቴ ፡ መቅሠፍትና ፡ ቍጣ ፡ ደርሶባቸው ፡ ተግሣጽም ፡ አግኝቷቸው ፡ ሄዱ ፡ አሉ ።

1103 ጠላት ፡ በጨለማ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ይገኛል ፤
—ቀን ፡ አይቶ ፡ መጣላት ፡ ይሻል ፡ ይመስለኛል ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ጠላትን ፡ በጨለማ ፡ ለማጥቃት ፡ ከመሞከር ፡ ቀን ፡ ብርሃን ፡ ሲታይ ፡ መጣላት ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ ከዘመናይ ፡ ጋራ ፡ ከመጋጨት ፡ መታገሥ ፡ ማሳለፍ ፡ ይሻላል ።

1104 ጠላቶች ፡ መሣሪያ ፡ ቢደግኑብን ፡
—ያድነናል ፡ ብለን ፡ ካቡን ፡ ተጠጋን ።

ሠ ፡ ጥይት ፡ እንዳይመታን ፡ ግንቡን ፡ ከለላ ፡ ካቡን ፡ ምሽግ ፡ አደረግን ።

ወ ፡ ከረኃብ ፡ ያድነናል ፡ ከችግር ፡ ያወጣናል ፡ በማለት ፡ ወደ ፡ አቡኑ ፡ ተጠጋን ፤ የጳጳሱ ፡ ጥገኞች ፡ ሆንን ።

1105 ጠላ ፡ ጠላ ፡ ብለው ፡ ሁሉ ፡ አወሩብህ ፤
—ሰዉ ፡ ምን ፡ ይጠጣል ፡ አንተስ ፡ ከጠላህ ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ጠላህን ፡ ትጠጣለህ ፤ ሰው ፡ የሚቀምሰው ፡ አጥቶ ፡ ተቸግሯል ፤ ላንቃው ፡ ደርቆ ፡ ምላሱ ፡ ታስሮ ፡ ተጨንቋል ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ያንተ ፡ ፈቃድ ፡ ካልሆነ ፡ አንተ ፡ ከተጣላህ ፡ የሚበላውስ ፡ የሚጠጣውስ ፡ ከወዴት ፡ ይገኛል ።

1106 ጠምጇ ፡ ነበረ ፡ ልዘራ ፡ ዳጕሳ ፡
—ለካስ ፡ ረስቼው ፡ ዘር ፡ የለኝም ፡ እሳ ።

ሠ ፡ አዝመራ ፡ ለማዝመር ፡ ወደ ፡ እርሻዬ ፡ ሄጄ ፡ በሬ ፡ ጠምጄ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፡ የዘር ፡ እኽል ፡ የለኝም ፤ ወደ ፡ ማሳው ፡ የገባሁት ፡ ዘር ፡ ሳሊዝ ፡ የምበትነው ፡ ሳይኖረኝ ፡ ባዶ ፡ እጄን ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ለካ ፡ ዘመዶቼ ፡ ሁሉ ፡ በሞት ፡ አልቀዋል ፤ ያለዘር ፡ ብቻዬን ፡ ቀር ቻለሁ ።

1107 ጠቦት ፡ ግዛ ፡ ብለው ፡ ልከውኝ ፡ ከመ(ሸ)ሼ ፡
—በግ ፡ አስቤ ፡ ለራት ፡ እስከ ፡ መች ፡ ደርሼ ።

ሠ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ እንደ ፡ ልቤ ፡ ካልተራመድሁ ፤ በግ ፡ አስቤ ፡ እንዴት ፡ ለራት ፡ አደርሳለሁ ፤ በጉስ ፡ መቼ ፡ ታርዶ ፡ ለራት ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ ዘር ፡ በመዝሪያው ፡ ወራት ፡ በክረምት ፡ ካልሠራሁ ፡ ካላረስኩ ፡ በጋ ፡ ሲመጣ ፡ መስከረም ፡ ሲጠባ ፡ ባስበው ፡ ትዳር ፡ መቼ ፡ ይቃናል ፤ ለ ቤተ ፡ ሰቤስ ፡ ምግብ ፡ ከወዴት ፡ አገኛለሁ ።

1108 ጠይቄው ፡ ነበረ ፡ ቤት ፡ እንዲያከራየኝ ፤
—እጅ ፡ በጅ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ቀን ፡ አልሰጥም ፡ አለኝ ።

ሠ ፡ አስቀድመህ ፡ ገንዘቡን ፡ እጅ ፡ በጅ ፡ ካልሰጠኸኝ ፡ ቤቱን ፡ አላከራ ይህም ፡ አለኝ ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ከደኅና ፡ ጊዜ ፡ ሳያደርሰኝ ፡ ለቁም ፡ ነገር ፡ ሳያበቃኝ ፡ ቀረ ፤ ይኸውና ፡ የሰው ፡ እጅ ፡ ዘላለም ፡ እንዳሳየኝ ፡ ይኖራል ።

1109 ጠጅም ፡ አላገኘን ፡ ከተለየናችሁ ፤
—አውራው ፡ ከተያዘ ፡ ማሩን ፡ እባካችሁ ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ንቡ ፡ እቀፎው ፡ ከገባ ፡ አውራው ፡ ከተያዘ ፡ እንግዲህ ፡ ማር ፡ አብ ሉን ፤ ከወለላው ፡ ስጡን ።

ወ ፡ የመሪያችን ፡ እጁ ፡ ከተያዘ ፡ እኛን ፡ ተከታዮቹን ፡ ማሩን ፤ ይቅርታ ፡ አድርጉልን ።

1110 ጠጅ ፡ ሞልቶ ፡ ካኖሩት ፡ እንዳይጐድል ፡ ዐውቃለሁ ፤
—ሰውን ፡ ጠጣው ፡ መሬት ፡ እንዴት ፡ እሆናለሁ ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ጠጣው ፡ ወይስ ፡ መሬት ፤ ያ ፡ ሙሉ ፡ የነበረው ፡ ጠጅ ፡ ከምን ፡ ደረሰ ፤ የት ፡ ገባ ፤ ምን ፡ ወሰደው ።

ወ ፡ የአዳምን ፡ ልጅ ፡ ሞት ፡ እየወሰደ ፡ መቃብር ፡ እየዋጠ ፡ ጨረሰው ፤ የሰው ፡ ልጅ ፡ በሞት ፡ አለቀ ፤ ተጠነፈፈ ።

1111 ጠጅ ፡ አማረኝ ፡ ስላት ፡ ማሩን ፡ ታስጭናለች ፤
ራበኝም ፡ ስላት ፡ እኽሉን ፡ ታስጭናለች ፤
በረደኝም ፡ ስላት ፡ ሸማ ፡ ትልካለች ፤
—ሌባዬ ፡ ተይዛ ፡ ባልጋ ፡ ትሄዳለች ። (ራስ ፡ ዐ) ፡

---

(1) ልጅ ፡ ኢያሱ ፡ በተያዙ ፡ ጊዜ ፡ ነጋድራስ ፡ ተሰማ ፡ እሸቴ ፡ በልጅ ፡ ኢያሱ ፡ ምክንያት ፡ የታሰርነውን ፡ ሁሉ ፡ ምሕረት ፡ አድርጉልን ፡ ለማለት ፡ በፈሊጥ ፡ ይቅርታ ፡ የጠየ ቁበት ።

ሠ ፡ ማሬን ፡ ጠጄን ፡ የሰረቀችብኝ ፡ እኽሌን ፡ ሸማዬን ፡ የወሰደችብኝ ፡ ሌባ ፡ ተይዛ ፡ ትሄዳለች ፡ የማይገባም ፡ ሥራ ፡ ሠርታለች ።

ወ ፡ ከባሏ ፡ እየሸሸገች ፡ ጠጁን ፡ ማሩን ፡ የምትልክልኝ ፡ እኽል ፡ ሸማ ፡ የ ምትሰጠኝ ፡ ረዳቴ ፡ ሞታ ፡ አስከሬኗ ፡ ባልጋ ፡ ይሄዳል ።

1112 ጠጅ ፡ ሰጠሁ ፡ ብሎ ፡ ምንድን ፡ ያስደንቃል ፤
ጠላ ፡ ሰጠሁ ፡ ብሎ ፡ ምንድን ፡ ያስደንቃል ፤
—እንጀራ ፡ ማሳላፍ ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ያውቃል ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ) ፡

ሠ ፡ ድግስ ፡ ማስተናበር ፡ ማእድ ፡ መሥራትና ፡ እንጀራ ፡ ማሳለፍ ፡ አስፋ፡ ወሰን ፡ ይችላል ፤ ማስተናገድ ፡ ያውቃል ።

ወ ፡ ልዑል ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ኃ ፡ ሥ ፡ ሰውን ፡ በትዳሩ ፡ በንብረቱ ፡ መደ ገፍ ፡ በችግሩ ፡ ጊዜ ፡ መርዳት ፡ የውቃል ።

1113 ጠጅ ፡ አስጥሎ ፡ ሄደ ፡ ይናጮችን ፡ ዱሪ ፡
—በዘመቻ ፡ እንኳ ፡ አይደል ፡ ያውም ፡ በወራሪ ።

ሠ ፡ በዘመቻ ፡ ሳይሆን ፡ በወራሪነት ፡ አገሩን ፡ ገዝቶ ፡ ዱሪ ፡ ይናጮችን ፡ ማር ፡ አስገበራቸው ።

ወ ፡ የሚያበላ ፡ የሚያጠጣ ፡ ጌታቸውን ፡ በወረራ ፡ ገድሎ ፡ ሄደ ፤ አገሩን ፡ ያለመሪ ፡ አስቀረው ።

1114 ጠፋብሁ ፡ ይሉኛል ፡ ከቃ ፡ ቤት ፡ ሸማሁ ፤
—እናቴን ፡ እናቴን ፡ እንዴት ፡ ተጐዳሁ ።

ሠ ፡ ልብስ ፡ ጠፋብዎት ፡ አሉ ፤ እምዬ ፡ በጣም ፡ ተጐዱ ።

ወ ፡ ወየው ፡ ወየው ፡ እናቴን ፡ አጣሁ ፤ እምዬን ፡ ያኽል ፡ ሰው ፡ ሞት ፡ ነጠቀኝ ።

1115 ጣፍጦኝ ፡ እንዳልበላ ፡ ይምረረው ፡ ብለኸኝ ፡
—ምነው ፡ በሥጋ ፡ አሞት ፡ ጨምረህ ፡ ሰጠኸኝ ።

ሠ ፡ ይምረረው ፡ ይጐምዝዘው ፡ ብለህ ፡ ሥጋውን ፡ በሐሞት ፡ ለውሰህ ፡ የሰጠኸኝ ፡ ለምንድነው ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ ሲጨንቅ ፡ ሲጠበብ ፡ ይኑር ፡ ብለህ ፡ ፈራሽ ፡ በስ ባሽ ፡ ሥጋን ፡ አልብሰህ ፡ ፈጠርከኝ ፤ ምነው ፡ ሞት ፡ የማይቀርለት ፡ ሥጋን ፡ ሰጠኸኝ ።

1116 ጤና ፡ በማጣቷ ፡ አዝኜ ፡ ስኖር ፡
—ደግሞ ፡ ባልጋ ፡ ሄደች ፡ ወይ ፡ አለማፈር ።

ሠ ፡ ዕረፍት ፡ የሌላት ፡ ባለጌይቱ ፡ ልጅ ፡ ያደረገችውን ፡ ረስታ ፡ እንደ ፡ ገና ፡ ወደ ፡ ባሏ ፡ ዘንድ ፡ ተመለሰች ፡ እኮ ።

ወ ፡ ጤና ፡ በማጣቷ ፡ ሳዝን ፡ ሞተችና ፡ አስከሬኗ ፡ በአልጋ ፡ ሄደን ፤ ዓለም ፡ አላፊ ፡ ጠፊ ፡ ነው ፡ እኮ ።

1117 ጥለኸኝ ፡ አትሂድ ፡ ጠብቀኝ ፡ ወንድሜ ፤
—እንዴት ፡ ልደርስብህ ፡ ዐፈር ፡ ተሸክሜ ።

ሠ ፡ ዐፈር ፡ ተሸክሜ ፡ ካንተ ፡ እኩል ፡ ሙራመድ ፡ አልቻልኩምና ፡ አባ
ክህ ፡ ጥለኸኝ ፡ አትሂድ ፤ ቆመህ ፡ ጠብቀኝ ።

ወ ፡ አብረን ፡ መሞት ፡ ይገባ ፡ ነበር ፤ ዳሩ ፡ ግን ፤ አሣሺ ፡ ሥጋ ፡ በመል
በሴ ፡ በሞት ፡ ልከተልህ ፡ አልቻልኩም ።

1118 ጥርን ፡ የካቲትን ፡ ወጣች ፡ ከኔ ፡ ቤት ፤
—አሁን ፡ ለመጋቢት ፡ ምን ፡ ቀለብ ፡ አላት ።

ሠ ፡ በመጋቢት ፡ ወር ፡ ምን ፡ ትመገብ ፡ ይሆን ፤ ምን ፡ ቀለብ ፡ አላት ።

ወ ፡ የገዳሙ ፡ እመ ፡ ምኔት ፡ (መጋቢዋ) ፡ የምትበላው ፡ የላትም ፤ ቀ
ለብ ፡ አልቆባት ፡ ተቸግራለች ።

1119 —ጥቅር ፡ መረሬ ፡ ነው ፡ ገና ፡ ዱሮ ፡ ነቅቷል ፤
—የሚዘራበትን ፡ ያው ፡ ገበሬው ፡ ያውቃል ።

ሠ ፡ መረሬው ፡ መሬት ፡ ነቅቷል ፤ ተሠነጣጥቋል ፤ ተፈነካክቷል ፤ በላዩ ፡
ላይ ፡ የሚዘራውን ፡ የሰብል ፡ ዐይነትና ፡ ወቅቱን ፡ ለይቶ ፡ የሚያው
ቀው ፡ ያው ፡ ባሕሪውን ፡ የመረመረው ፡ ገበሬው ፡ ነው ።

ወ ፡ ጥቅር ፡ ባለጋሮቹ ፡ በተንኰል ፡ እንደ ፡ ተነሡበትና ፡ ለማጥቃትም ፡
እንደ ፡ ታጠቁበት ፡ ቀድሞውኑ ፡ ዐውቆት ፡ ተገንዝቦት ፡ ተቀምጧል ።
አሸናፊውን ፡ ባለድሉን ፡ ግን ፡ የሚያውቀው ፡ ፈጣሪ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

1120 ጥቂት ፡ እንኳ ፡ ሳላርስ ፡ ገበሬ ፡ ይሉኛል ፤
—ዋቶአደር ፡ መሆኔን ፡ ማን ፡ ይነግርልኛል ።

ሠ ፡ ሳላርስ ፡ ሳልቈፍር ፡ ሰው ፡ ገበሬ ፡ ይለኛል ፤ ዘዋሪ ፡ ዋቶ ፡ አዳሪ ፡ መሆ
ኔን ፡ ያወቀልኝ ፡ የለም ።

ወ ፡ ገበሬ ፡ አለመሆኔንና ፡ ወታደርነቴን ፡ አሁን ፡ ማን ፡ ያስረዳልኛል ።

1121 ጥቂት ፡ ወሬ ፡ አውሩልኝ ፡ ጀግኖች ፡ እባካችሁ ፤
ስትጨፈጭፉት ፡ በሾተል ፡ ገብታችሁ ፤
ስትሸከሽኩት ፡ በሳንጃ ፡ ገጥማችሁ ፤
ስትጠዘጥዙት ፡ እንደ ፡ ንብ ፡ ከባችሁ ፤
—ጋዙን ፡ ስታስፈጁት ፡ ማአስከለከላችሁ ። (1) (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ጠላትን ፡ ስትጨፈጭፉት ፡ ስትጠዘጥዙት ፡ መከራውን ፡ ስታስጨ
ርሱት ፡ ዘሩን ፡ እንዳታጠፉት ፡ ማን ፡ ከለከላችሁ ፤ ማን ፡ አስጣላ
ችሁ ።

ወ ፡ ጠላት ፡ በብርቱ ፡ በመጠቃቱ ፡ መርዝ ፡ ሲያፈስባችሁ ፡ ጋዝ ፡ ሲጨ
ርስባችሁ ፡ መከላከያውን ፡ «ማስክ» ፡ እንዳታገኙ ፡ አደረገባችሁ ።

1122 ጥቅምም ፡ አላገኘሁ ፡ አየሁት ፡ ሁሉን ፤
—አሁንስ ፡ ጨርሼ ፡ ሆኛለሁ ፡ በድን ።

---

(1) ባ፲፱፻፳፰ ዓ ፡ ም ፡ ኢትዮጵያ ፡ ከጣሊያን ፡ ጋራ ፡ በተዋጋችበት ፡ ጊዜ ፡ ከወዳጅ ፡ አገር ፡
በገንዘቧ ፡ ገዝታ ፡ ያስመጣችውን ፡ በራስ ፡ ላይ ፡ የሚጠለቅ ፡ «ማስክ» ፡ የሚባል ፡
የመርዝ ፡ መከላከያ ፡ መሣሪያ ፡ ሙሶሊኒ ፡ ወደ ፡ ኢትዮጵያ ፡ እንዳይገባ ፡ ስላስከለ
ከለ ፡ የተገጠመ ።

ሠ ፡ ዛሬስ ፡ ሰውነቴ ፡ ፈዘዘ ፤ ግራ ፡ ገባኝ ፤ በድን ፡ ሆንሁ ፤ የማደርገውን ፡ አጣሁት ።

ወ ፡ ኀዘን ፡ ጠቅልዬ ፡ ያለ ፡ የሌለውን ፡ ይገፍ ፡ ድን ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ተቀምጫለሁ ።

1123 ጥንቱንስ ፡ መቼ ፡ አልኩህ ፡ የጅማ ፡ ሰው ፡ አምጣ ፤
—ተከፋ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ከጅማ ፡ መች ፡ ታጣ ።

ሠ ፡ የከፋ ፡ ተወላጅ ፡ የሆነ ፡ ሰው ፡ አምጣልኝ ፡ አልኩ ፡ እንጂ ፤ የጅማ ፡ ሰውማ ፡ መቼ ፡ አጣሁ ።

ወ ፡ ተቀያሚ ፡ ከዳተኛ ፡ መች ፡ ታጣ ፤ በየዱሩ ፡ ይገኛል ።

1124 ጥንት ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ የረከሰ ፡ ሥጋ ፤
—ዛሬስ ፡ ነፍስ ፡ ሆኗል ፡ ባለብዙ ፡ ዋጋ ።　(ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ሥጋ ፡ በጣም ፡ ተወዷል ፤ ከቀድሞ ፡ ዋጋው ፡ በብዙ ፡ ጨምሯል ፤ በትንሽ ፡ ገንዘብ ፡ አይገኝም ።

ወ ፡ ባሁኑ ፡ ዘመን ፡ ነፍስን ፡ ለማዳን ፡ በጎ ፡ ሥራ ፡ መሥራት ፡ ተወደደ ፤ ለሥጋው ፡ ማድላት ፡ ቀረ ።

1125 ጫጉን ፡ አርደህ ፡ በልተህ ፡ አልጠገብክምና ፤
—ደግሞ ፡ አርድልሃለሁ ፡ እዚያው ፡ እመጣና ። (1) (ዘለ ፡ ቍ ፡ 59) ፡

ሠ ፡ ጫጉን ፡ በልተህ ፡ ሆድህ ፡ ካልሞላ ፡ አንጀትህ ፡ ካልደረሰ ፤ እዚያው ፡ መጥቼ ፡ ሌላ ፡ ከብት ፡ አርድልሃለሁ ።

ወ ፡ በሬዬን ፡ ጫጉን ፡ ደፍረህ ፡ ከበላህ ፡ መጥቼ ፡ አርድሃለሁ ፤ ሬሳ ፡ በሬሳ ፡ አደርግሃለሁ ።

1126 ጭብጥ ፡ ጥሬ ፡ ሰጥተን ፡ ቍዬልን ፡ ብንላት ፡
—ይችስ ፡ የምትቈላው ፡ የምታምሰው ፡ ናት ።　(ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ ይችስ ፡ ፡ ልጅ ፡ የሰጠናትን ፡ እኽል ፡ ቈልታ ፡ ሳትጨርሰው ፡ አትቀርም ።

ወ ፡ ይህች ፡ ልጅ ፡ ጤናም ፡ አትሰጥ ፤ የምትበጠብጥ ፡ ሰላም ፡ የምትነሣ ፡ ናት ።

1127 ፀሓይ ፡ ወጣ ፡ ብሎ ፡ ምንድን ፡ ያስመርራል ፤
—ይዘገያል ፡ እንጂ ፡ ደመናን ፡ ይቀራል ።　(መጺ ፡ ቍ ፡ 6).
(ዘለ ፡ ቍ 1፡56 ፡ 804) ፡

ሠ ፡ ፀሓዩ ፡ ቢበረታም ፡ ደግሞ ፡ በተራው ፡ ዳመና ፡ ሳይመጣ ፡ አይቀርም ፤ ቀኑ ፡ ጉም ፡ ጭጋግ ፡ እንደሚሆን ፡ አይጠረጠርም ።

ወ ፡ ይዋል ፡ ይደር ፡ እንጂ ፡ የሰው ፡ ደም ፡ ፈሶ ፡ በከንቱ ፡ ይቀራልን ፤ የጊዜው ፡ ጊዜ ፡ መገለጡ ፡ ከፍርድ ፡ ሸንጎ ፡ መድረሱ ፡ ጥርጥር ፡ የለውም ።

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ጫጉ ፡ የሚባል ፡ ባንገቱ ፡ ቃጭል ፡ የተደረገለት ፡ አንድ ፡ በሬ ፡ ነበራቸው ፤ በሄደበት ፡ ሁሉ ፡ ያገኘውን ፡ ይበላ ፡ ስለ ፡ ነበር ፡ የላስታ ፡ ሕዝብ ፡ ደፍሮ ፡ ዐርዶ ፡ ስለ ፡ በላው ፡ ንጉሡ ፡ በመበሳጨት ፡ የተናገሩት ።

1128 ፈረሰኛ ፡ ታቦት ፡ እንግዲህ ፡ አላምን ፤
—በፈረስ ፡ ቀደሙት ፡ መርቆሬዎስን ።

ሠ ፡ ፈረሰኛውን ፡ ሰማዕት ፡ መርቆሬዎስን ፡ በፈረስ ፡ ቀደሙት ፡ በግልቢያ ፡ በሽቅድድም ፡ የሚበልጡት ፡ ተገኙ ።

ወ ፡ የቅዱስ ፡ መርቆሬዎስን ፡ ጽላት ፡ ማረኩት ፤ በፈረስ ፡ ቀዳማይ ፡ አድርገው ፡ ወሰዱት ።

1129 ፈረስ ፡ በቅሎ ፡ ይዞ ፡ ከሚከተለው ፤
—እቤቱ ፡ ያለውን ፡ ይወደዋል ፡ ሰው ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ፈረስ ፡ በቅሎ ፡ እየሳበ ፡ የሚከተለውን ፡ ትቶ ፡ እቤት ፡ የቀረውን ፡ አሽከር ፡ ሰው ፡ ይወደዋል ።

ወ ፡ ገንዘብ ፡ ያለውን ፡ ሀብት ፡ ንብረት ፡ ያበጀውን ፡ ሁሉ ፡ ይወደዋል ፤ ጉንበስ ፡ ቀና ፡ ይልለታል ፤ ያረግድለታል ።

1130 ፈረስና ፡ በቅሎ ፡ መጣብር ፡ ሆኖም ፡
—መርገፍ ፡ ለጣይቱ ፡ አይገባትም ።

ሠ ፡ መጣብርና ፡ መረባት ፡ ቢያስፈልግም ፡ ቅሉ ፡ የመርገፍ ፡ ጌጥ ፡ ለጣይቱ ፡ አይገባትም ።

ወ ፡ እንደ ፡ ውበቷና ፡ እንደ ፡ ታላቅነቷ ፡ እቴጌ ፡ ጣይቱ ፡ የምትሞት ፡ አትመስልም ፤ ነገር ፡ ግን ፡ ሞት ፡ ለፍጡር ፡ ሁሉ ፡ የማይቀር ፡ ሆኖ ፡ ሞተች ፤ ረገፈች ።

1131 ፈረስ ፡ ያለልጓም ፡ ይወጣል ፡ ወይ ፡ ደጅ ፤
—በል ፡ ልባቡን ፡ ይዘህ ፡ አንከባለው ፡ እንጅ ።

ሠ ፡ በል ፡ ለኮውን ፡ ይዘህ ፡ ፈረሱን ፡ አንደባለው ፤ ይንከባለል ።

ወ ፡ እባቡን ፡ በጅህ ፡ ይዘህ ፡ በመሬት ፡ ላይ ፡ ውቃው ፡ ዘርረው ።

1132 ፈክራ ፡ ፈክራ ፡ ምንም ፡ አልቀረች ፤
—አልፋ ፡ ከሴቶቹ ፡ ወንድ ፡ አሰለፈች ። (አ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ከሴቶቹ ፡ ተራ ፡ ወጥታ ፡ አልፋ ፡ ተርፋ ፡ ወንድ ፡ ታስልፍ ፡ ዠመር ።

ወ ፡ ከሴቶቹ ፡ ሁሉ ፡ «አሰለፈችን» ፡ የሚመስላትና ፡ የሚያኽላት ፡ የለም፤ የሴት ፡ ወንድ ፡ ናት ።

1133 ፈጣሪ ፡ ድግስህን ፡ እንዳታሳንሰው ፤
—እንቢ ፡ ብሎ ፡ አይቀርም ፡ አንት ፡ የጠራኸው ፡ ሰው ።

ሠ ፡ የጋበዝኸውና ፡ የጠራኸው ፡ ሁሉ ፡ አንድም ፡ ሳይቀር ፡ በሙሉ ፡ መጪ ፡ ነውና ፡ ድግስህ ፡ እንዳያንስ ።

ወ ፡ አንተ ፡ ቢሞት ፡ የጠራኸው ፡ ፍጡር ፡ በኀይሉ ፡ በጕልበቱ ፡ ተመክቶ ፡ ላንድ ፡ ሰኮንድ ፡ እንኳ ፡ በሕይወት ፡ ለመኖር ፡ አይችልምና ፤ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ ምሕረትህ ፡ ይቅርታህ ፡ የበዛ ፡ ይሁን ።

1134 ፈጥኜ ፡ እመጣለሁ ፡ ብሎ ፡ የነበረ ፤
—እረ ፡ አሞት ፡ ይሆናል ፡ ከዋለ ፡ ካደረ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ቶሎ ፡ እመለሳለሁ ፡ ብሎ ፡ ሂዶ ፡ እዚያው ፡ ሰነበተ ፤ ምናልባት ፡ ታሞ ፡ ይሆናል ፤ በደኅናው ፡ እንዲህ ፡ አልዘገየም ።

ወ ፡ የሚበላ ፡ የሚቀመስ ፡ ከጠፋ ፡ ረኃብ ፡ ከዋለ ፡ ካደረ ፡ ነፍስ ፡ ማጥፋቱ ፡ ሰው ፡ መግደሉ ፡ አይቀርም ።

1135 ፊታውራሪ ፡ ቾኰል ፡ ሸማው ፡ አልቆበት ፡
—እንዲያው ፡ ተንጠልጥሎ ፡ ግንዱን ፡ አየሁት ። (1)

ሠ ፡ ልብሱ ፡ አልቆበት ፡ ዕርቃኑን ፡ ሥጋውን ፡ ቆሞ ፡ አየሁት ።

ወ ፡ ፊታውራሪ ፡ ቾኰል ፡ ዕራቊቱን ፡ ተሰቅሎ ፤ ዕንጨት ፡ ላይ ፡ ተንጠልጥሎ ፤ አየሁት ።

1136 ፊት ፡ ለፊት ፡ ተቀምጦ ፡ ከሚበላው ፡ ሰው ፡
—በጥግ ፡ የቆመው ፡ ነው ፡ የሚጠቀመው ። (ዮ ፡ ን) ፡

ሠ ፡ ከማእድ ፡ ቀርቦ ፡ ፊት ፡ ለፊት ፡ ተቀምጦ ፡ ከሚመገበው ፡ ሰው ፡ በጐን ፡ ያለው ፡ በኋላ ፡ የቆመው ፡ ይጠቀማል ፤ እስኪበቃው ፡ ይመገባል ።

ወ ፡ ሠርቶ ፡ ደክሞ ፡ ከሚኖረው ፡ ይልቅ ፡ ወገን ፡ አስታዋሽ ፡ ያለው ፡ ይጠቀማል ።

1137 ፊት ፡ ማያ ፡ መስተዋት ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ገዛችሁ ፤
—የሰው ፡ ፊት ፡ የሚያሳይ ፡ እኽል ፡ ካለላችሁ ።

ሠ ፡ እኽል ፡ እንደ ፡ መስተዋት ፡ ፊት ፡ ሲያሳይ ፡ እናንተ ፡ መስተዋት ፡ የምትገዙት ፡ ለምንድነው ።

ወ ፡ እኽል ፡ ማጣት ፡ የሰውን ፡ ፊት ፡ ያሳያል ፤ በሰጪው ፡ ፊት ፡ ላይ ፡ የመጠላትንና ፡ የመናቅን ፡ መልክ ፡ ያሳያል ።

1138 ፋሲካ ፡ ሊገደፍ ፡ ዞረ ፡ ገብረ ፡ ሰላም ፤
—ተነሣ ፡ ጐዣሜ ፡ ሁለተኛ ፡ አትበላም ።

ሠ ፡ ዳግመኛ ፡ ገበታ ፡ አትቀርብም ፤ ሁለት ፡ ጊዜ ፡ መጋበዝ ፡ አትችልም ፤ ተነሥ ፤ ለባለተራ ፡ ልቀቅ ።

ወ ፡ የጐዣም ፡ ወታደር ፡ ጦር ፡ መጥቷልና ፡ ተነሣ ፤ ተዘጋጅተህ ፡ ታጥቀህ ፡ ጠብቅ ።

1139 ፍርድ ፡ ለማግኘት ፡ ነው ፡ ያሰብነው ፡ እኛም ፤
—ዋቢ ፡ አናሳልፍም ፡ ሳንፈጣጠም ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ፍርድ ፡ ሳናገኝ ፡ ከዳኛ ፡ ሳንደርስ ፡ ነገሩን ፡ አንተውም ፤ ዋቢ ፡ አናሳልፍም ፤ ዋስ ፡ አንሰጥም ።

ወ ፡ እዚያው ፡ እንተላለቃለን ፡ እንጂ ፤ ጠላትን ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ የዋቢ ፡ ሸበሌን ፡ ወንዝ ፡ አናሻግረውም ።

---

(1) ዐፄ ፡ ቴዎድሮስ ፡ ደጃች ፡ ተድላን ፡ ለመውጋት ፡ ጐዣም ፡ መጥተው ፡ ሳሉ ፡ ጀግናው ፡ ፊታውራሪ ፡ ቾኰል ፡ «ለጋበዴሳ» ፡ ላይ ፡ ተይዞ ፡ በባሶ ፡ ገበያ ፡ ስለ ፡ ተሰቀለ ፡ አንዲት ፡ ሴት ፡ ያለቀሰችው ።

1140 ፍቀድልኝ ፡ አምላክ ፡ እንድጠይቅህ ፤
ያ ፡ ሰውዬ ፡ ቆሞ ፡ እየለመነህ ፤
—ስለ ፡ ምን ፡ መለስከው ፡ አትቁም ፡ ብለህ ።

ሠ ፡ ሰውዬው ፡ ከደጃፍህ ፡ ቆሞ ፡ ስመ ፡ እግዚአብሔር ፡ ጠርቶ ፡ ሲለምንህ ፡ ምንም ፡ ሳትሰጥ ፡ አትቁም ፡ ብለህ ፡ ለምን ፡ መለስከው ።

ወ ፡ ፈጣሪዬ ፡ ሆይ ፡ ለምን ፡ ያን ፡ ሰው ፡ ባጭር ፡ ቀጨኸው ፤ የዕድሜ ፡ ድኻ ፡ አደረግኸው ፤ ሕይወትን ፡ ነሣኸው ።



ምዕራፍ ፡ ፫ ።

## የፍቅር ፡ ዘፈን ።

1 ለግድግዳው ፡ ነወይ ፡ የምትቸገሪ ፤
—ቈርጨልሻለሁ ፡ እንግዲህ ፡ ቤት ፡ ሥሪ ።

ሠ ፡ ለግድግዳ ፡ የሚሆነውን ፡ ዕንጨት ፡ ቋሚውን ፡ አግዳሚውን ፡ አዘጋጅቼልሻለሁና ፡ እንግዲህ ፡ ቤትሽን ፡ ሥሪ ፤ መኖሪያሽን ፡ አብጂ ።

ወ ፡ እኔ ፡ ያንቺ ፡ ነገር ፡ በቅቶኛል ፤ አንዠቴ ፡ ቈርጦልኛልና ፡ የምትፈልጊውን ፡ ማድረግ ፡ ትችያለሽ ።

2 ላሚቷ ፡ እንድትከሳ ፡ ጥጃዋ ፡ እንድትሞት ፡
—ምን ፡ የቈረጠው ፡ ነው ፡ እንዲህ ፡ ያለባት ።

ሠ ፡ ለጥጃዋ ፡ የምትጠባው ፡ ሳይተውላት ፡ ላሟን ፡ እንዲህ ፡ ሙልጭ ፡ አድርጎ ፡ ማን ፡ አለባት ፤ ጥጃዋ ፡ እንድትሞት ፡ ነውን ።

ወ ፡ በጣም ፡ የሚያምር ፡ የተሞናደለ ፡ ባት ፡ አላት ።

3 ላሞቹ ፡ ደረቁ ፤ ጥጆቹ ፡ አብረው ፡ ዋሉ ፤
—አሁን ፡ የት ፡ ይገኛል ፡ ወተት ፡ ወተት ፡ ቢሉ ።

ሠ ፡ ላሞቹ ፡ ከነጠፉ ፡ ጥጆቹ ፡ አብረው ፡ ከዋሉ ፡ በኋላ ፡ ወተት ፡ የት ፡ ይገኛል ፤ ለጥጆቹም ፡ እንኳ ፡ አይበቃ ።

ወ ፡ ቀድሞ ፡ ያላደራጁትን ፡ ለማግኘት ፡ ቢጥሩ ፡ ቢወጡ ፡ ቢወርዱ ፡ ቢዋትቱ ፡ ትርፉ ፡ ድካም ፡ ነው ።

4 ላረቄውም ፡ ኰራሽ ፤ ለውስኪውም ፡ ኰራሽ ፤ አንቺ ፡ ግድ ፡ የለሽም ፤
—የወደድሽው ፡ ጠላ ፡ አልተገኘልሽም ።

ሠ ፡ አንቺ ፡ የፈለግሽው ፡ መጠጥ ፡ ጠላ ፡ አልተገኘም ፤ ዐረቄና ፡ ውስኪ ፡ እንዳትጠጪም ፡ አልፈቀድሽም ።

ወ ፡ የወደድሽው ፡ ሰው ፡ ሳይወድሽ ፡ ቀረ ፤ ፍቅርሽ ፡ ቅጥ ፡ አጣ ።

5 ልሂድ ፡ እዚያ ፡ ማዶ ፡ ፀሓይ ፡ እወጣበት ፤
—እነሜቴ ፡ መንደር ፡ ገና ፡ ጥላ ፡ አለበት ።

ሠ ፡ የእነሜቴን ፡ ሰፈር ፡ ጥላ ፡ ዐርፎበታል ፤ ደመና ፡ አንዣቦበታል ፤ ፀሓይ ፡ የለበትም ።

ወ ፡ በጊዜ ፡ ወደ ፡ ቤቴ ፡ ልሻገር ፤ እነሜቴ ፡ መንደር ፡ አንባጓሮ ፡ አይጠፋም ፤ ጠብ ፡ መነሣቱ ፡ አይቀርም ።

6 ሐኪም ፡ ቤት ፡ አልሄደች ፡ ያለችው ፡ ከቤት ፡
—እኔ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ላርጋት ፡ ያችን ፡ ሰው ፡ አሟት ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 189) ፡

ሠ ፡ ያችን ፡ ልጅ ፡ በጣም ፡ አሟታል ፤ ሐኪም ፡ አላያትም ፤ ምን ፡ ማድረግ ፡ ይበጃል ።

ወ ፡ ያችን ፡ ሰው ፡ ያሟታል ፤ ይቦጭቋታል ፤ ጥሬ ፡ ሥጋዋን ፡ ይበሏታል ፤ እንዴት ፡ አድርጌ ፡ ስሟን ፡ ልጠብቅላት ፤ ከሐሜት ፡ ላድናት ።

7 ሁል ፡ ጊዜ ፡ ባሬራ ፡ ትበያለሽ ፡ ወይ ፤
—ምነው ፡ አንዳንድ ፡ ቀን ፡ ወጥ ፡ አትይም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ለምን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በአሬራ ፡ ትበያለሽ ፤ አልፎ ፡ አልፎ ፡ አንዳንድ ፡ ቀን ፡ ለምን ፡ ወጥ ፡ ስጡኝ ፡ አትዪም ፤ መበያ ፡ አድርጉልኝ ፡ ብለሽ ፡ አትጠይቂም ።

ወ ፡ ለምን ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ በቤት ፡ ትቀመጫለሽ ፤ አንዳንድ ፡ ቀን ፡ እንኳ ፡ ለምን ፡ ለሽርሽር ፡ እደጅ ፡ አትወጪም ፤ እንደ ፡ ጓደኞችሽ ፡ አትሆኝም ።

8 መልካም ፡ ጠጁን ፡ ትቶ ፡ የተጣራውን ፡
—ደግሞ ፡ ይባክናል ፡ ሰው ፡ ወዶ ፡ ጠላን ።

ሠ ፡ በመልካም ፡ ሆኖ ፡ ተዘጋጅቶ ፡ የቀረበ ፡ ጠጅ ፡ እያለ ፡ ሰው ፡ ጠላን ፡ እየወደደ ፡ በየመሸታው ፡ ቤት ፡ ይዞራል ።

ወ ፡ ሰውዬው ፡ ያቺን ፡ ፍቅር ፡ የማታውቅ ፡ ወረተኛ ፡ ሴት ፡ ወዶ ፡ ለማግኘት ፡ ይለፋል ።

9 መሸሸግ ፡ እንዴት ፡ ነው ፡ መደበቅ ፡ እንዴት ፡ ነው ፤
—የሠራ ፡ አካላትህ ፡ ይታየኛል ፡ ምነው ።

ሠ ፡ አሁን ፡ መደበቅ ፡ መሸሸግ ፡ ያልከው ፡ ነው ፡ ወይ ፤ መላ ፡ ሰውነትህ ፡ አካልህ ፡ አልተሰወረኝም ።

ወ ፡ ምንም ፡ እንኳ ፡ ከቀረህ ፡ ብዙ ፡ ቀን ፡ ቢሆን ፡ በዐይነ ፡ ኅሊናዬ ፡ አይሃለሁ ፤ በውኔም ፡ በሕልሜም ፡ የምመለከተው ፡ አንተኑ ፡ ነው ።

10 መንደረኛው ፡ ሁሉ ፡ እሳት ፡ ጫሪ ፡ ነው ፤
—ያንን ፡ ገል ፡ አደራ ፡ ሰው ፡ እንዳይነካው ።

ሠ ፡ ያንን ፡ የሳት ፡ መጫሪያ ፡ ሸክላ ፡ ማንም ፡ ሰው ፡ እንዳይነካው ፤ ውርድ ፡ ከራሴ ፡ ነው ።

ወ ፡ ያንን ፡ መሳይ ፡ ውብ ፡ ሰውነት ፡ ይዘሽ ፡ ከማንም ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ እንዳትወድቂ ፤ እንዳትገጥሚ ፤ መጠንቀቅ ፡ ይገባሻል ።

11 መካን ፡ ኮሶ ፡ ጠጣሁ ፡ የማያድነኝ ፤
—ደግሞ ፡ ሁለተኛ ፡ ታይቶ ፡ ሊገለኝ ።

ሠ ፡ ኮሶ ፡ መልሶ ፡ ተጠናወተኝ ፤ ደጋግሞ ፡ ታየኝ ፤ በየጊዜው ፡ ያስደነግጠኝ ፡ ዠመር ።

ወ ፡ ትዝታው ፡ ሳይረሳኝ ፡ ደግሞ ፡ ብቅ ፡ ብቅ ፡ እያለ ፡ በናፍቆት ፡ ሰቀቀን ፡ ገደለኝ ።

12 መውረዱንስ ፡ ወረድሽ ፡ ጨኖ ፡ ለጕዳይ ፤
—ተሳስተሽ ፡ መቅረት ፡ ይገባሻል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ለጕዳይሽ ፡ ጨኖ ፡ ብትሄጂ ፡ በዚያው ፡ ጠፍተሽ ፡ መቅረት ፡ ቤትሽን ፡ መርሳትና ፡ መዘጋት ፡ ይገባሽ ፡ ነበርን ።

ወ ፡ ሃይማኖትሽን ፡ አርክሰሽ ፡ ከስላም ፡ ጋራ ፡ በልተሽ ፡ ዐንኰል ፡ ሆነሽ፡ በሰው ፡ አገር ፡ መቅረት ፡ ይገባሻልን ።

13 መደቡን ፡ ሠርተሽው ፡ ፀሐይ ፡ ባይነካው ፡
—ትመቻለሽ ፡ አንች ፡ ከዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ መደቡን ፡ ሠርተሽ ፡ ፀሐይ ፡ ሳታሞቂው ፡ ብትቀሪ ፡ ወዮልሽ ፡ መመታት ፡ አይቀርልሽም ፤ አሳር ፡ ያገኝሻል ።

ወ ፡ ሰውነትሽ ፡ ምቹ ፡ ነው ፤ ከማንም ፡ ይልቅ ፡ አንቺ ፡ ታስደስቻለሽ ።

14 መጥቼ ፡ ባስጠይቅ ፡ አላገኘሁሽም ፤
—ምክንያቱን ፡ እንጃ ፡ አንቺ ፡ ቤት ፡ የለሽም ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ መጥቼ ፡ አጣሁሽ ፤ አንቺ ፡ ከቤት ፡ አልነበርሽም ፤ ወደ ፡ ውጭ ፡ ሄደሽ፡ ኖሯል ፡ መሰለኝ ።

ወ ፡ መኖሪያሽ ፡ የማይታወቅ ፤ መቀመጫ ፡ ቤት ፡ የሌለሽ ፡ ዘዋሪ ፡ ነሽ ፤ ትዳረ ፡ ፈት ፡ ነሽ ።

15 መጨነቅ ፡ መጠበብ ፡ ለጠጅ ፡ ብቻ ፡ ነው ፤
—ለጠላ ፡ መድኀኒት ፡ ተወት ፡ ማድረግ ፡ ነው ።

ሠ ፡ በጣም ፡ የሚያስቸግረው ፡ የጠጅ ፡ አምሮት ፡ ብቻ ፡ ነው ፡ እንጂ ፤ የጠላ ፡ ውልታ ፡ በቀላሉ ፡ ሊተውና ፡ ሊረሳ ፡ ይቻላል ።

ወ ፡ ፍቅር ፡ ላልያዘውና ፡ ጥላቻ ፡ ላደረበት ፡ ሰው ፡ መድኀኒቱ ፡ ተወት ፡ ለቀቅ ፡ ማድረግ ፡ ነው ፤ የሚበጀው ፡ መለያየቱ ፡ ነው ።

16 ማነው ፡ እኔን ፡ ትምርት ፡ አታውቅም ፡ የሚል ፤
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ ታምሩን ፡ ሳነበው ፡ ስውል ።

ሠ ፡ ተአምር ፡ ሳነብ ፡ እየዋልሁ ፡ ማነው ፡ እኔን ፡ አልተማረችም ፤ ማይምን ፡ ናት ፡ የሚለኝ ።

ወ ፡ አሁን ፡ እኔን ፡ ፍቅር ፡ አታውቅም ፡ የሚለኝ ፡ ማነው ፤ አቶ ፡ ታምሩን ፡ ልቡን ፡ ነክቼው ፡ የሚያደርገውን ፡ አሳጥቼው ፡ እያዩኝ ።

17 ማነው ፡ ያቀጠነው ፡ የራስ ፡ ዐሊን ፡ ጠጅ ፤
—ከማሩ ፡ አይመስለኝም ፡ በጥባጩ ፡ ነው ፡ እንጂ ።

ሠ ፡ የራስ ፡ ዐሊ ፡ ጠጅ ፡ የተበላሸው ፡ ማር ፡ አንሶት ፡ አይደለም ፤ ጠጅ ፡ ጣዩ ፡ አጥፍቶት ፡ ነው ፡ እንጂ ።

ወ ፡ የራስ ፡ ዐሊን ፡ ቤት ፡ ያፈረሰው ፡ ሰባቂና ፡ ነገር ፡ አመላላሽ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ የባሴ ፡ ጠብ ፡ አልነበረም ፤ አምባጓሮ ፡ አልተደረገም ።

18 ምቀኛስ ፡ ቢበዛ ፡ ሰውስ ፡ ቢጠላሽ ፡
—ምን ፡ ችግር ፡ አለብሽ ፡ አንቺ ፡ ብዙ ፡ ነሽ ፤

ሠ ፡ አንች ፡ አጋር ፡ የተረፈሽ ፡ ደጎና ፡ ወገን ፡ ያለሽ ፡ ዘመደ ፡ ብዙ ፡ ነሽ ፤ ምቀኛና ፡ ጠላት ፡ ምንም ፡ ሊያደርግሽ ፡ አይችልም ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ብዙነሽ ፡ አንች ፡ ምንም ፡ ዐይነት ፡ ችግር ፡ የለብሽም ፤ ሁሉ ፡ በደጅሽ ፡ ነው ።

19 ምነው ፡ ብታስጠሪኝ ፡ እኔን ፡ አስታውሰሽ ፤
—እደጅ ፡ ተቀምጬ ፡ እቤቴ ፡ ሳመሽ ።

ሠ ፡ እዚሁ ፡ ሥራ ፡ ፈትቼ ፡ ሳመሽ ፡ ብታስጠሪኝ ፡ ምን ፡ ነበር ።

ወ ፡ እኔን ፡ እንኳ ፡ ጥቂት ፡ ሳያፍር ፡ እደጅ ፡ ተቀምጬ ፡ እያየኝ ፡ እዚሁ ፡ በዚሁ ፡ አንችን ፡ ሳመሽ ፤ ዐይን ፡ ባይን ፡ ከሚስቴ ፡ ጋራ ፡ ይሣሣቅ ፡ ዠመር ።

20 ምነው ፡ ትፈራለህ ፡ ወንዱ ፡ ልጅ ፡ በሌቱ ፤
—አለፋና ፡ ስሄድ ፡ እኔ ፡ እንኳ ፡ ሴቲቱ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ሴቷ ፡ እንኳ ፡ በጨለማ ፡ ያለመብራት ፡ ስሄድ ፡ አንተን ፡ ወንዱን ፡ ልጅ ፡ ምን ፡ አስፈራህ ።

ወ ፡ አለፋ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ና ፤ እዚያ ፡ ድረስ ፡ እንገናኝ ።

21 ምነው ፡ አልተሰፋ ፡ ኩታ ፡ ቀሚስሽ ፤
—አሰፋው ፡ ነበረ ፡ ቁጭ ፡ ብዬ ፡ ሳመሽ ።

ሠ ፡ ሥራ ፡ ፈትቼ ፡ ሳመሽ ፡ ብትነግሪኝ ፡ ኖሮ ፤ ኩታ ፡ ቀሚስሽን ፡ አሰፋልሽ ፡ ነበር ።

ወ ፡ እኔን ፡ እንኳ ፡ ጥቂት ፡ ሳያፍር ፤ እደጅ ፡ ተቀምጬ ፡ እያየኝ ፤ እዚሁ ፡ በዚሁ ፡ አንችን ፡ ሳመሽ ፤ ዐይን ፡ ባይን ፡ ከሚስቴ ፡ ጋራ ፡ ይሣሣቅ ፡ ዠመር ። ( ቍ ፡ 19 ) ፡ ዘፈን ፡

22 ምነው ፡ እዚያ ፡ ድረስ ፡ አትመጣም ፡ ወይ ፡ እዚህ ፤
—አውሬ ፡ እንኳ ፡ አትፈራ ፡ ጨለማ ፡ የለብህ ።

ሠ ፡ አውሬ ፡ ያሠጋኛል ፡ እንዳትል ፡ ቀኑ ፡ አልመሸም ፤ ጨለማ ፡ የለም ፤ ያውሬ ፡ መውጫው ፡ አልደረሰም ።

ወ ፡ ጠይብን ፡ አውሬ ፡ አይተናኰለውም ፤ ጨለማ ፡ አይፈራም ፤ ዥብ ፡ አያሠጋውም ።

23 ምኑንም ፡ ምኑንም ፡ እያሉ ፡ እያወሩ ፡
—ሥራዬን ፡ አስፈቱኝ ፡ ያምሮቴ ፡ ጀንበሩ ።

ሠ ፡ ያልሆነ ፡ የሆነውን ፡ እየቀባጠሩ ፤ የቈጥ ፡ የባጡን ፡ እያወሩ ፡ ያምሮቴ ፡ ጀንበሩ ፡ ሥራ ፡ አላሠራም ፡ አሉኝ ፤ ጊዜዬን ፡ በወሬ ፡ አባከኑት ።

ወ ፡ አቶ ፡ ያምሮቴ ፡ ጀንበሩ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁን ፡ እያመጡ ፡ እየነገሩኝ ፡ ከሚስቴ ፡ ከሥራ ፡ ይፍቱ ፡ አለያዩኝ ፤ መልካም ፡ ትዳሬን ፡ አስፈረሱኝ ።

24 ምናምኑን ፡ በልቶ ፡ ሆዴን ፡ ከማለት ፡
—ጦም ፡ ውሎ ፡ ጦም ፡ አድሮ ፡ ጥሩ ፡ መሸመት ።

ሠ ፡ አሠሩን ፡ ገሰሱን ፡ እየበሉ ፡ ሆድን ፡ ከመታመም ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ተቸግሮ ፡ ጥሩ ፡ መሸመት ፡ ይበጃል ።

ወ ፡ ቸኵሎ ፡ ዘሯ ፡ ካልታወቀ ፡ ሴት ፡ እጅ ፡ ከመግባት ፡ ታግሦ ፡ ጊዜን ፡ ጠብቆ ፤ አቻ ፡ ለአቻ ፡ ከጥሩ ፡ ዘር ፡ መጋባት ፡ እጅግ ፡ መልካም ፡ ነው ።

25 ምንም ፡ ቢበዛባት ፡ ሌት ፡ ከቀን ፡ ብትሠራ ፡
—ፈርጣ ፡ ገረዲቱ ፡ አትወጣም ፡ ተመራ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ሥራ ፡ ቢበዛባት ፡ ሌት ፡ ተቀን ፡ ያለዕረፍት ፡ እንድትሠራ ፡ ቢያደርጓት ፡ ገረዲቱ ፡ ኑሮ ፡ መሯት ፡ ሥራ ፡ ሰልችቷት ፡ ፈርጥጣ ፡ አትመጣም ።

ወ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ ቢሆን ፡ ፋርጣ ፡ የምትባለው ፡ አገር ፡ ከመራ ፡ እጅ ፡ አትወጣም ፤ ለርሱ ፡ እንደ ፡ ርስተ ፡ ጕልት ፡ የምትቈጠር ፡ ናት ።

26 ምንም ፡ ድኻ ፡ ብሆን ፡ ባይኖረኝም ፡ ተድላ ፡
—ለጠጅ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ አልጓጓም ፡ ለጠላ ።

ሠ ፡ ምንም ፡ ድኻ ፡ ብሆን ፡ ጠጅ ፡ እንጂ ፡ ጠላ ፡ አያምረኝም ፤ ለብቅል ፡ እምብዛም ፡ አልጓጓም ።

ወ ፡ እኔ ፡ የምጨነቀው ፡ ለምወደው ፡ ሰው ፡ ነው ፤ ለጠላሁት ፡ ግን ፡ ደንታ ፡ የለኝም ፤ አልጨነቅም ።

27 ምንም ፡ አልናገር ፡ እኔ ፡ ዝም ፡ እላለሁ ፤
—አንቺ ፡ ውላውለሽ ፡ መምጣትሽን ፡ ዐውቃለሁ ።

ሠ ፡ ውላውላ ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ሄደሽ ፡ ውለሽ ፡ መምጣትሽን ፡ ጎሊናዬ ፡ ዐውቆታል ፤ ልቡናዬ ፡ ተረድቶታል ፤ ምንም ፡ መናገር ፡ አልፈቅድም ።

ወ ፡ ውል ፡ ገብተሽ ፡ ቃል ፡ አስረሽ ፡ ቀጠሮ ፡ ተቀብለሽ ፡ መምጣትሽን ፡ መመለስሽን ፡ ዐውቄዋለሁ ፤ ክፉ ፡ በጎ ፡ ከመናገር ፡ ቢቀር ፡ ይሻላል ።

28 ምን ፡ ተናግሬያለሁ ፡ የበደሉኝን ፤
—ስሞተኛ ፡ እያሉ ፡ ያጠፉት ፡ ስሜን ።

ሠ ፡ ካንደበቴ ፡ የወጣ ፡ ነገር ፡ ሳይኖር ፡ ስምዎን ፡ በክፉ ፡ ሳላነሣ ፤ ለምንድነው ፡ አሉባልተኛ ፡ የሚያደርጉኝ ፤ ስሞተኛ ፡ የሚያሰኙኝ ።

ወ ፡ ባልሠራሁት ፡ ሥራ ፡ ስሜን ፡ የሚያጠፉት ፡ ሴሰኛ ፡ የሚያደርጉኝ ፡ ለምንድነው ።

29 ምንኛ ፡ ደግ ፡ ነው ፡ ስሜነኛ ፡ መሆን ፤
—ተወገራ ፡ ልቤ ፡ ታገኛት ፡ እንደሆን ።

ሠ ፡ ከላሙ ፡ አገር ፡ ከወገራ ፡ ሄጄ ፡ ወተቱን ፡ አልቤ ፡ የማገኛት ፡ ብሆን ፡ እሰጣታለሁ ።

ወ ፡ ልቤ ፡ የማይሆንልህን ፡ ለማግኘት ፡ አትጨነቅ ፤ በከንቱ ፡ አትሣቀይ ።

30 ምን ፡ ያለ ፡ ገበሬ ፡ የማይገባው ፡ ምክር ፤
—ይህች ፡ ብትታረስ ፡ ዘር ፡ ትሆን ፡ ነበር ።

ሠ ፡ ይህች ፡ መሬት ፡ ብትታረስ ፡ ጠፍ ፡ ሆና ፡ ባታድር ፡ ኖሮ ፡ ብዙ ፡ እ ኽል ፡ ታስገኝ ፡ ነበር ።

ወ ፡ ባራስነቷ ፡ በሚገባ ፡ ብትታረስ ፡ እንዳትጐዳ ፡ ብትጠበቅ ፡ ዘር ፡ ትሰጥ ፡ ነበር ።

31 ምን ፡ ያሉ ፡ ቄስ ፡ ናቸው ፡ ተዝካር ፡ የለመዱ ፤
—አስታርቁኝ ፡ ብላቸው ፡ ፍታት ፡ ብለው ፡ ሄዱ ።

ሠ ፡ ከሚስቴ ፡ ያስታርቁኝ ፡ ሽምግልና ፡ ይዩልኝ ፡ ብዬ ፡ ብለምናቸው ፡ ተዝካር ፡ የለመዱት ፡ ቄሱ ፡ ፍታት ፡ አለብኝ ፡ ብለው ፡ ሄዱ ።

ወ ፡ ቄሱን ፡ ከሚስቴ ፡ ያስታርቁኝ ፡ ከባለቤቴ ፡ ያማልዱኝ ፡ ብላቸው ፡ ምን ፡ ታደርግልሃለች ፡ ፍታት ፡ ተዋት ፡ ብለው ፡ እንድለያይ ፡ ገፋፍ ተውኝ ፡ ሄዱ ።

32 ምን ፡ ያላት ፡ አሽከር ፡ ናት ፡ ቀልድ ፡ የለመደች ፤
—ባጠብቃት ፡ ዝም ፡ አለች ፤ ባላላት ፡ ሄደች ።

ሠ ፡ አጥብቄ ፡ ብይዛት ፡ ዐርፋ ፡ ተቀመጠች ፤ አላልቼ ፡ ብጨብጣት ፡ ጥላኝ ፡ ነጐደች ፤ ቀልደኛይቱ ፡ አሽከር ፡ ግራ ፡ አገባችኝ ።

ወ ፡ ያች ፡ አሽከር ፡ ባል ፡ ያላት ፡ ኖራ ፡ ሄደች ፤ የማላዛልቃት ፡ መሆኔን ፡ ዐውቃ ፡ ወደ ፡ ባሏ ፡ ተመለሰች ።

33 ምን ፡ ያላት ፡ አሽከር ፡ ናት ፡ የተክለፈለፈች ፤
—ቅድም ፡ በልቤ ፡ ላይ ፡ አሁን ፡ ባይኔ ፡ አለፈች ።

ሠ ፡ ክልፍልፍ ፡ አሽከር ፡ አሁንም ፡ አሁንም ፡ በፊቴ ፡ ትሄዳለች ፤ ታል ፉለች ፤ ታገድማለች ።

ወ ፡ የዚያች ፡ ያሽከር ፡ ነገር ፡ አልሆነልኝም ፤ ሁኔታዋ ፡ ባይኔ ፡ ይታየኛል፤ ትዝታዋ ፡ በልቤ ፡ ይወጣል ፤ ይወርዳል ።

34 ሞኝ ፡ ሰው ፡ ይመስል ፡ የምትፈራ ፡ ምነው ፤
—ሰተት ፡ ብለህ ፡ ግባ ፡ ቤት ፡ ለንግዳ ፡ እንጂ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ምን ፡ ያስፈራሃል ፤ ቤት ፡ ለእግዚአብሔር ፡ እንግዳ ፡ የተሠራ ፡ ነው ፤ ሰተት ፡ ብለህ ፡ ግባ ፤ ቅርታ ፡ አይሰማህ ፤ ሥጋት ፡ አይግባህ ።

ወ ፡ ላንተ ፡ ለወዳጄ ፡ ለንግዳ ፡ ያልሆነ ፡ ቤት ፡ ለማን ፡ ሊሆን ፡ ነው ፤ ሳትገነግን ፡ ሰተት ፡ ብለህ ፡ ግባ ፤ እንደ ፡ ልብህ ፡ ሁንበት ።

35 ሞያችሁን ፡ ሁሉ ፡ መርምረን ፡ ዐውቀናል ፤
—ቢሆን ፡ ጠላችሁን ፡ በጣም ፡ አድንቀናል ።

ሠ ፡ ከሞያችሁ ፡ ከባልትናችሁ ፡ ሁሉ ፡ ጠላችሁ ፡ የሚደነቅ ፡ ነው ፤ ከጠጅ ፡ የሚያስመርጥ ፡ ነው ።

ወ ፡ ፍቅራችሁ ፡ እንጂ ፡ ጠባችሁ ፡ አያድርስ ፡ ነው ፤ አንባጓሯችሁ ፡ ክፉ ፡ ነው ፤ ቶሎ ፡ አይበርድም ፤ የእግር ፡ እሳት ፡ ነው ።

36 ሥጋ ፡ ቢወስድላት ፡ ጕድን ፡ ተዳቢት ፡
—አልበላም ፡ አለችው ፡ አለዡላሊት ። (1)

ሠ ፡ ሥጋው ፡ ከያይነቱ ፡ ተቈርጦ ፡ ቢሄድላት ፡ ከዡላሊት ፡ በቀር ፡ ሌላ ውን ፡ አልበላም ፡ አለች ።

ወ ፡ ከተሰበሰበው ፡ ዐዛውንት ፡ ሁሉ ፡ ብላታ ፡ ዡላሊትን ፡ ብቻ ፡ ወደ ደች ፤ ቀልቧ ፡ ከርሱ ፡ ላይ ፡ ዐረፈ ።

37 ሰምቻለሁና ፡ ያብርሃምን ፡ ገድል ፤
—እንግዳ ፡ ሳይመጣ ፡ አልቀምስም ፡ እኽል ።

ሠ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ እንግዳ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ ሳሊዝ ፤ እኽል ፡ አልቀምስም ፤ እራትም ፡ ሆነ ፡ ምሳ ፡ አልበላም ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ እንግዳ ፡ ካልመጣ ፡ እኽል ፡ ባፌ ፡ አይዞርም ፤ ወዳጄን ፡ ሳ ሊዝ ፡ ምንም ፡ አልቀምስም ።

38 ሰዉ ፡ ሁሉ ፡ አብዝቶ ፡ ይጠጣል ፡ በጣም ፤
—እኔስ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ከልኬ ፡ አላልፍም ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 71)፡

ሠ ፡ ሰው ፡ ከዐቅሙ ፡ በላይ ፡ ከመጠን ፡ አሳልፎ ፡ አብዝቶ ፡ መጠጥ ፡ ይጠጣል ፤ ለክቶ ፡ መጥኖ ፡ መጠጣትን ፡ አይፈቅድም ፤ እኔ ፡ ግን ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ከልክ ፡ በላይ ፡ አልጠጣም ።

ወ ፡ እኔ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ ከወይዘሮ ፡ ልኬ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ አልመኝም ፤ ከርሷ ፡ በቀር ፡ ልቤ ፡ የሚፈቅደው ፡ የለም ።

39 ሰዎች ፡ መጥተው ፡ ነበር ፡ ጩኸቱን ፡ ሰምተው ፤
—ተመልሰው ፡ ሄዱ ፡ ይምታታ ፡ ብለው ።

ሠ ፡ ጩኸቱን ፡ ሰምተው ፡ የመጡት ፡ ገላጋዮች ፡ ይባባል ፡ ይጨፋጨፍ ፡ ይራኰት ፡ ብለው ፡ ተመልሰው ፡ ሄዱ ፤ ለመገላገልና ፡ ጠቡን ፡ ለማብ ረድ ፡ ሳይፈቅዱ ፡ ቀሩ ።

ወ ፡ የመጡት ፡ ገላጋዮች ፡ ይምታት ፡ ይበላት ፡ ይደብድባት ፡ እያሉ ፡ ተመለሱ ።

40 ሱሪዬን ፡ አንጥፌ ፡ ልተኛ ፡ ደጅሽ ፤
—ከቤት ፡ እንዳልገባ ፡ አንችም ፡ ነት ፡ የለሽ ።

ሠ ፡ ሱሪዬን ፡ አንጥፌ ፡ ከደጅ ፡ ልተኛ ፤ መቼም ፡ ምንጣፍ ፡ የሚሆን ፡ ቍርበት ፡ ነት ፡ ባንች ፡ ቤት ፡ አልተገኘ ።

ወ ፡ አንች ፡ ተጠራጣሪ ፡ ነሽ ፤ ሰውን ፡ ማመን ፡ አይሆንልሽም ፤ እምነት ፡ ከልብሽ ፡ ላይ ፡ የለም ።

---

(1) ብላታ ፡ ዡላሊት ፡ የሚባል ፡ ሰው ፡ በደጃዝማች ፡ ጓሉ ፡ ትእዛዝ ፡ የደጃች ፡ ዘውዴን ፡ ሚስት ፡ ወይዘሮ ፡ ድንቅነሽን ፡ አስኰብልሎ ፡ ይዞ ፡ በጌምድር ፡ ወደ ፡ ራስ ፡ ጉግሳ፡ ስለ ፡ ሄደና ፡ በወዳጅነትም ፡ ስለ ፡ ታማ ፡ የተነገረ።

41 ሳናረጅ ፡ ሳናፈጅ ፡ ልጅነት ፡ እያለን ፡
—መቅረታችን ፡ ነው ፡ ወይ ፡ እንዲህ ፡ ተነካክተን ።

ሠ ፡ ሰውነታችን ፡ ሳይደክም ፡ በዕድሜ ፡ ሳንገፋ ፡ በልጅነታችን ፡ ገርጅፈን ፡ ወደቅን ፤ ተጐሳቈልን ።

ወ ፡ የኔና ፡ ያንቺ ፡ ነገር ፡ ይኸው ፡ ሆኖ ፡ መቅረቱ ፡ ነው ፡ ወይ ፤ ፍቅራችን ፡ ከጋብቻ ፡ ሳይደርስ ፡ እንዲሁ ፡ በኾምር ፡ መቅረቱ ፡ ነውን ።

42 ሴቱን ፡ ሁሉ ፡ ወስዶ ፡ በጽኑ ፡ አሰራቸው ፤
—እነዚህን ፡ ስንኳ ፡ ምነው ፡ ባላላቸው ።

ሠ ፡ ሴቶቹን ፡ በሙሉ ፡ ወስዶ ፡ አሰራቸው ፤ ምነው ፡ እነዚህን ፡ እንኳ ፡ እስራት ፡ ባለጸናባቸው ፤ እግረ ፡ሙቁን ፡ ባላላላቸው ።

ወ ፡ እነዚህ ፡ ባል ፡ አላቸው ፤ ሴት ፡ አዳሪ ፡ አይደሉ ፤ ምነው ፡ ባያንገላታቸው ።

43 ሴቲቱ ፡ ልጅ ፡ ወንዱን ፡ እንዴት ፡ ደፈረችኝ ፤
—እስካሁን ፡ ያመኛል ፡ ልቤን ፡ የመታችኝ ።

ሠ ፡ ልቤን ፡ ክፉኛ ፡ የመታችኝ ፡ እስካሁን ፡ ድረስ ፡ ይሰማኛል ፤ ያመኛል ፤ በጣም ፡ ጐድታኛለች ፤ ደብድባኛለች ።

ወ ፡ ልቤ ፡ በርሷ ፡ ፍቅር ፡ ተነክቷል ፤ ትዝታዋ ፡ ያነኋልለኛል ፤ የምሠራውን ፡ ያሳጣኛል ፤ ያንጀዋልለኛል ።

44 ሴቲቱ ፡ ትግያ ፡ ምንኛ ፡ ለመደች ፤
—ይሣቅበት ፡ ብላ ፡ ወንዱን ፡ ጥላኝ ፡ ሄደች ።

ሠ ፡ መሣቂያ ፡ መዘባበቻ ፡ ይሁን ፡ ብላ ፡ ወንዱን ፡ ልጅ ፡ ሴቲቱ ፡ በትግል ፡ ጣለችኝ ፤ እሰው ፡ ፊት ፡ አዋረደችኝ ።

ወ ፡ እባዶ ፡ ቤት ፡ ያለሰው ፡ ብቻዬን ፡ ትታኝ ፡ ሄደች ፤ ሚስቴ ፡ ያገር ፡ መሣቂያ ፡ አደረገችኝ ።

45 ሴቶች ፡ ተበራቱ ፡ አታብዙ ፡ ድካም ፤
—ሥራ ፡ ብቻ ፡ ሆኗል ፡ ባል ፡ አልተገኘም ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ የዕረፍት ፡ ጊዜ ፡ አልተገኘም ፤ መደዳውን ፡ ሥራ ፡ ብቻ ፡ ሆኗል ፤ መተንፈሻ ፡ ሰዓት ፡ የለም ፤ ሥራ ፡ በዝቷል ።

ወ ፡ ባል ፡ ችግር ፡ ሆኗል ፤ ሁሉ ፡ ወንደ ፡ ላጤ ፡ በመሆኑ ፡ ሚስት ፡ አግብቶ ፡ ትዳር ፡ ይዞ ፡ መኖር ፡ ቀረ ።

46 ሴቶች ፡ ተበራቱ ፡ አትሁኑ ፡ ሰነፍ ፤
—በሥራ ፡ ቀን ፡ ሠርቶ ፡ በባል ፡ ነው ፡ ማረፍ ።

ሠ ፡ በሥራ ፡ ሰዓት ፡ ሥራን ፡ ሠርቶ ፡ በበዓል ፡ ጊዜ ፡ ማረፍ ፡ መልካም ፡ ነው ።

ወ ፡ ወግ ፡ ማዕረግ ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የሚኖረው ፡ ከባል ፡ ጋራ ፡ ሲኖሩ ፡ ነው ፤ ሴት ፡ የምትከበረውና ፡ የምትታፈረው ፡ ከወንድ ፡ ጋራ ፡ ስትሆን ፡ ነው ።

47 ሴቶች ፡ ልምከራችሁ ፡ ይቅርባችሁ ፡ በውነት ፡
—ገንዘብ ፡ ባላነሰኝ ፡ እያሉ ፡ መቄጨት ።

ሠ ፡ ሴቶች ፡ ተመከሩ ፤ በገንዘብ ፡ ተቸገርን ፡ ሀብት ፡ አጣን ፡ እያላችሁ፡ መበሳጨቱንና ፡ መቄጨቱን ፡ ተዉት ፤ በያዛችሁት ፡ እጃችሁ ፡ ባለው ፡ ለመርካት ፡ ሞክሩ ።

ወ ፡ ሴቶች ፡ ባሌ ፡ አቻዬ ፡ አይደለም ፤ እኩያዬ ፡ ካልሆነ ፡ ሰው ፡ ጋራ ፡ ተጋባሁ ፡ እያሉ ፡ መቄጨት ፡ ይቅርባችሁ ።

48 ሸጋ ፡ ልጅ ፡ አርግዤ ፡ ጠንቶብኛል ፡ ምጡ ፤
—እኔም ፡ እህ ፡ እላለሁ ፡ እናንተም ፡ አድምጡ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ እህ ፡ እያልኩ ፡ አምጣለሁ ፤ እናንተም ፡ ማርያም ፡ ማርያም ፡ እያላችሁ ፡ ልትረዱኝ ፡ ሞክሩ ፤ የሕፃኑን ፡ መምጣት ፡ አድምጡ ።

ወ ፡ እኔ ፡ ወዳጄ ፡ የት ፡ እንደ ፡ ደረሰ ፡ እህ ፡ እያልኩ ፡ እጠያይቃለሁ ፤ እናንተም ፡ በየበኩላችሁና ፡ በየፊናችሁ ፡ አፈላልጉኝ ።

49 ቀሚሴንም ፡ ሰጠሁ ፡ ድርቤንም ፡ ሰጠሁ ፡ አለቀ ፡ ስለቱ ፤
—ለመርጡለ ፡ ማርያም ፡ ለዚያች ፡ ለደብሪቱ ።

ሠ ፡ ለመርጡለ ፡ ማርያም ፡ ደብር ፡ ቀሚሴንም ፡ ድርቤንም ፡ ሰጠሁ ፤ በሙሉ ፡ ስለቴን ፡ አደረስሁ ፤ ብፅዓቴን ፡ አበረከትሁ ።

ወ ፡ ያለ ፡ የሌለውን ፡ ሀብቴን ፡ ቀሚሱ ፤ ድርቡ ፡ ሳይቀር ፡ ለወይዘሮ ፡ ደብሪቱ ፡ ሰጠሁ ፤ ገንዘቤ ፡ በሙሉ ፡ እሷን ፡ በመሸንገል ፡ አለቀ ።

50 ቀድሞ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ በልጅነትሽ ፤
—ምን ፡ ትሆኝኛለሽ ፡ አሁንማ ፡ አድገሽ ።

ሠ ፡ ዛሬስ ፡ አልፈልግሽም ፤ አካልሽ ፡ አድጓል ፤ ሰውነትሽ ፡ ጠንክሯል ፤ ዕድሜሽ ፡ እየገፋ ፡ ሄዷል ።

ወ ፡ አፍላሽ ፡ ካለቀ ፡ ለዛሽ ፡ ከጠፋ ፤ ምን ፡ ትሆኝኛለሽ ፤ «አድገሽ» ፡ ዛሬ ፡ ምንም ፡ አታደርጊልኝም ፤ አልፈልግሽም ።

51 ቅቤ ፡ ረከሰ ፡ አሉ ፡ በየገበያው ፤
—አዬ ፡ ጉድ ፡ ትቀባ ፡ የማታረጀው ።

ሠ ፡ ቅቤ ፡ ተረከሰ ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ ከተገኘ ፡ ትግዛ ፤ ትቀባ ፤ ትተባበስ ፤ ወዛ ፡ ትበል ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ትቀባ ፡ እርጅና ፡ የማይለውጣት ፡ ናት ፤ መግደርደር ፡ ትወዳለች ፤ ትቀናለች ።

52 በሐምሌ ፡ በናሴ ፡ እንዲያ ፡ ስዋትት ፡
—እንዴት ፡ በመስከረም ፡ ባበባ ፡ ልሙት ።

ሠ ፡ የረኃቡን ፡ የችግሩን ፡ ወራት ፡ ሐምሌና ፡ ነሐሴን ፡ በደኅና ፡ አልፌ ፡ እንዴት ፡ ሊጠባ ፡ ሲደርስ ፡ አዝመራ ፡ ማበብ ፡ ሲዠምር ፡ በመስከረም ፡ ልሙት ።

ወ ፡ የወይዘሮ ፡ አበባ ፡ ፍቅር ፡ እንዴት ፡ አሸንፎ ፡ አስጨንቆ ፡ ይግደለኝ ።

53 በምን ፡ ምክንያት ፡ ነው ፡ የተቈጡት ፡ ጌታ ፤
—ተገፋ ፡ ማደሯን ፡ እኛ ፡ አልሰማን ፡ ማታ ።

ሠ ፡ ቀሚሷን ፡ ተገፋ ፡ የሌሊት ፡ ልብሷን ፡ ተቀምታ ፡ ዕራቍቷን ፡ ማደሯን ፡ እኛ ፡ መቼ ፡ ሰማንና ፡ ጌታ ፡ በደፈናው ፡ ይቈጡናል ፤ ባላወቅነው ፡ ነገር ፡ ይዘልፉናል ።

ወ ፡ ገፋ ፡ ከሚባለው ፡ አሽከር ፡ ጋራ ፡ ክብሯን ፡ ቀንሳ ፡ ማደሯን ፡ እኛ ፡ መቼ ፡ ዐወቅን ፤ ይኸን ፡ ጉድ ፡ መቼ ፡ ሰማንና ፡ ጌታችን ፡ ይቈጡናል ።

54 በምን ፡ እንዲህ ፡ በዛ ፡ በጣም ፡ ያንቺ ፡ ጣጣ ፤
—ሁል ፡ ጊዜ ፡ ከቤትሽ ፡ እንግዳ ፡ አይታጣ ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 121) ፡

ሠ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ካንቺ ፡ ቤት ፡ የእግዚአብሔር ፡ እንግዳ ፡ አይታጣም፤ ብቻሽን ፡ በልተሽ ፡ ጠጥተሽ ፡ አታውቂም ፤ ቤትሽ ፡ ያለሰው ፡ አያድርም ።

ወ ፡ ወዳጅሽ ፡ እንግዳ ፡ ካንቺ ፡ ቤት ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አይጠፋም ፤ ካንቺ ፡ ጓዳ ፡ አይወጣም ፤ የፈለገው ፡ ሁሉ ፡ በውርርድ ፡ ካንቺ ፡ ቤት ፡ ያገኘዋል ።

55 በሬ ፡ በሬ ፡ ሆኗል ፡ የሚሸጠው ፡ ከብት ፤
—አሁን ፡ የት ፡ ይገኛል ፡ የላም ፡ አካላት ። (ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ የላም ፡ ሥጋ ፡ አሁን ፡ የት ፡ ይገኛል ፤ በየገበያ ፡ የሚሸጠው ፡ በየልኳንዳ ፡ የተሰቀለው ፡ የበሬ ፡ ሥጋ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ወ ፡ አሁን ፡ ውርጭና ፡ ብርድ ፡ ያላቈራረፈደው ፡ የለሰለሰ ፡ የላመ ፡ ሰውነት ፡ እንዳንቺ ፡ ያለ ፡ የት ፡ ይገኛል ።

56 በሦስቱ ፡ ሥላሴ ፡ አማጥኜሃለሁ ፤
—አንተም ፡ አገዳደል ፡ እኔም ፡ ሞት ፡ ዐውቃለሁ ።

ሠ ፡ በሦስቱ ፡ ሥላሴ ፡ ይገዤሃለሁና ፡ አትግደለኝ ፡ ከጨከንክ ፡ ግን ፡ ለመግደል መቻልክን ፡ እኔም ፡ ሟች ፡ መሆኔን ፡ እረዳዋለሁ ።

ወ ፡ የወደድከኝን ፡ ያህል ፡ እኔም ፡ እወድሃለሁ ፡ የፍቅራችን ፡ ኃይል ፡ ተመዛዛኝ፡ ነው ። አንተ ፡ በፍቅር ፡ መጣል ፡ እንደምትችል ፡ እኔም ፡ መቀበል ፡ እችላለሁ ።

57 በሰብል ፡ መካከል ፡ ስትነዳ ፡ ብዙ ፡ ላም ፡
—እንዴት ፡ ያለች ፡ ልጅ ፡ ናት ፡ እኽል ፡ አታስበላም ።

ሠ ፡ እረኛይቱ ፡ ጠንቃቃ ፡ ናት ፤ ሰብል ፡ አታስጠፋም ፤ የተዘራ ፡ እኽል ፡ አታስበላም ፤ ከብቶቹን ፡ በጥንቃቄ ፡ ትጠብቃለች ፤ ታግዳለች ።
ወ ፡ የልጅቷ ፡ ፍቅር ፡ ኀይለኛ ፡ ነው ፤ እኽል ፡ አያስበላም ፤ የሚያደርጉትን ፡ ያሳጣል ፤ ብርቱ ፡ ነው ።

58 በሸዋ ፡ በትግሬ ፡ ደግሞም ፡ በጐዣም ፡
—እንዳንች ፡ ያለ ፡ ደጋን ፡ እኔ ፡ አላየሁም ።

ሠ ፡ በየትም ፡ አገር ፡ ያንችን ፡ የመሰለ ፡ ደጋን ፡ አላየሁም ፤ ጥጥ ፡ መንደፊያ ፡ መሣሪያሽ ፡ ከሁሉ ፡ የተለየ ፡ ነው ።

ወ ፡ በሸዋ ፡ በትግሬና ፡ በጐዣምም ፡ እንዳንች ፡ ያለ ፡ ደጋን ፡ እግር ፡ አ
ላየሁም ፤ የእግርሽ ፡ ጐባጣነት ፡ በሬ ፡ ከነቀንዱ ፡ ያሾልካል ።

59 በሸዋ ፡ በትግሬ ፡ ደግሞም ፡ በጐዣም ፤
—እንዳንች ፡ ሴት ፡ አስለቃሽ ፡ በምድር ፡ አላየሁም ።

ሠ ፡ እግር ፡ እስኪነቃ ፡ ቢሄዱ ፡ እንዳንች ፡ ያለ ፡ ሙሾ ፡ አውራጅ ፡ አል
ቃሽ ፡ አይገኝም ፤ መልካም ፡ አስተዛዛኝ ፡ ነሽ ።

ወ ፡ ወንዶቹን ፡ በመንጠቅ ፡ ወዳጆቻቸውን ፡ በውበትሽ ፡ በመማረክ ፡
እንዳንች ፡ ሴቶችን ፡ የሚያስቈጭና ፡ የሚያስለቅስ ፡ የለም ።

60 በሽተኛው ፡ ብዙ ፡ መድኀኒት ፡ ያነሰው ፤
—እኔስ ፡ ምን ፡ ፈቀረኝ ፡ ያልተለከፈ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ በበሽታው ፡ የተነደፈው ፡ ሰው ፡ ብዙ ፡ ነው ፤ መድኀኒቱ ፡ ለሕሙማኑ ፡
በቂ ፡ አይደለም ፤ በሽታው ፡ ያሊያዘው ፡ ምንኛ ፡ ዕድለኛ ፡ ነው ።

ወ ፡ በፍቅር ፡ ያልተነደፈ ፡ ትዝታ ፡ ያላደረበት ፡ ሰው ፡ ምንኛ ፡ ታደለ ።

61 በቅሎ ፡ ሲጭኑ ፡ ባይ ፡ አህያ ፡ ጭኛለሁ ፤
—ያችው ፡ ተነከታብኝ ፡ እደበድባለሁ ።

ሠ ፡ አህያዬን ፡ ጭነት ፡ ጐድቶብኝ ፡ ተነከታለች ፤ ተገጥባለች ፤ ዠርባዋ ፡
የበለጠ ፡ እንዳይጐዳ ፡ ድብዳቡን ፡ አመቻችላታለሁ ።

ወ ፡ አንድ ፡ የማትረባ ፡ መልከ ፡ ጥፉ ፡ ሚስት ፡ ብትኖረኝ ፡ ሀያጅ ፡ ሆና
ብኝ ፡ በየነጋው ፡ እቀጣታለሁ ፤ እደበድባታለሁ ።

62 በቅሎዬ ፡ ተጭና ፡ መቆሻን ፡ ዕወቂ ፤
—አንች ፡ አስቢ ፡ ለኔ ፡ እንዳትነጠቂ ።

ሠ ፡ በቅሎዬን ፡ ተጠንቅቀሽ ፡ አስቢ ፤ አስጐትቺ ፤ እንዳትነጠቂ ፡ ሁኚ ።

ወ ፡ አንቺ ፡ ለኔ ፡ ለጐኔ ፡ አስቢ ፤ ጠብቀሽና ፡ ተጠንቅቀሽ ፡ ያዥኝ ፤ እን
ዳትነጠቂ ፡ ሁኚ ።

63 በብዙ ፡ በሽታ ፡ ስሣቀይ ፡ ቈይቼ ፡
—ዛሬስ ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ፡ ጤናዬን ፡ አግኝቼ ።

ሠ ፡ ያማቅቀኝ ፡ የነበረው ፡ በሽታዬ ፡ ለቆኝ ፡ ሰውነቴ ፡ አገግሞ ፡ ጤናዬ ፡
ተመልሶ ፡ ደስ ፡ ብሎኛል ።

ወ ፡ ወዳጄን ፡ ጤናዬን ፡ በማግኘቴ ፡ ደስታ ፡ ተሰምቶኛል ፤ ዐይን ፡ ባይን ፡
በመተያየት ፡ ሰውነቴ ፡ ረክቷል ።

64 በባል ፡ እየሠሩ ፡ ብዙ ፡ ሀብት ፡ ከማግኘት ፡
—ባል ፡ እያከበሩ ፡ መኖር ፡ በድኽነት ።

ሠ ፡ በዓል ፡ ሽሮ ፡ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ አፍርሶ ፡ ብዙ ፡ ሀብት ፡ ከማግ
ኘት ፡ ከመበልጸግና ፡ ንብረትን ፡ ከማሻሻል ፤ በዓልን ፡ እያከበሩ ፡
በድኽነትና ፡ በችግር ፡ መኖር ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ በባል ፡ ላይ ፡ እየሄዱ ፡ ሀብትን ፡ ከመሰብሰብ ፡ ካንድ ፡ ባል ፡ ረግቶ ፡ ተቸግሮ ፡ መኖር ፡ ይሻላል ።

65 በችኰላ ፡ መጣሁ ፡ አገርሽን ፡ ሳላይ ፤ (ወደ ፡ ዘለሰኛ ፡ የሚዞር ፡)
—የሠራሽው ፡ እልፍኝ ፡ ደራ ፡ ኰራ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ የሠራሽው ፡ ቤት ፡ ዘበጠ ፤ ወይስ ፡ ኰራ ፤ እንዴት ፡ ሆነ ።

ወ ፡ ደራ ፡ ገዥውን ፡ አልቀበልም ፡ ብሎ ፡ ትዕቢት ፡ አደረበት ፡ ወይ ፤ መሸፈቱ ፡ ጦር ፡ መፈለጉ ፡ ነወይ ።

66 በኖርሁበት ፡ ሁሉ ፡ ባለፈው ፡ ዘመኔ ፡
—እንዳንች ፡ ጥሩ ፡ በጥባጭ ፡ አላየሁም ፡ እኔ ።

ሠ ፡ በዕድሜዬ ፡ ልክ ፡ ከቶ ፡ እንዳንች ፡ ያለ ፡ ጠጅ ፡ ዐዋቂ ፡ አላየሁም ።

ወ ፡ ደኅናውን ፡ ነገር ፡ የሚያጠፋ ፡ ጥሩውን ፡ አሳብ ፡ የሚበጠብጥ ፡ እን ዳንች ፡ ያለ ፡ መጥፎ ፡ ሰው ፡ አላየሁም ።

67 በዚችም ፡ በዚያችም ፡ ትወጋጋኛለች ፤
—እስቲ ፡ ዋገምት ፡ አምጡ ፡ በደም ፡ ትወጣለች ።

ሠ ፡ በያለበት ፡ የምትወጋጋኝን ፡ በሽታ ፡ ከደም ፡ ጋራ ፡ ለማስወገድ ፡ እስቲ ፡ ዋገምት ፡ አምጥታችሁ ፡ አግሙኝ ።

ወ ፡ በፍቅር ፡ ካልሆነ ፤ በግድ ፡ በኀይል ፡ ደም ፡ እስከ ፡ ማፍሰስ ፡ ደርሼ ፡ አስወጣታለሁ ።

68 በዚያም ፡ በዚያም ፡ ቢሆን ፡ እኔ ፡ ካሳ ፡ አልበላ ፤
—ገንዘቤን ፡ ካገኘሁ ፡ አልፈልግም ፡ ሌላ ።

ሠ ፡ እንጡራ ፡ ገንዘቤን ፡ ንጹሕ ፡ ሀብቴን ፡ ካገኘሁ ፡ የኔ ፡ ያልሆነውን ፡ የሰው ፡ ገንዘብ ፡ አልሻም ፤ አልፈልግም ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ «ገንዘቤን» ፡ ካገኘሁ ፡ ሌላውን ፡ አልሻውም ፤ ካሳም ፡ አል ቀበል ።

69 በዚያ ፡ በበረሓ ፡ በዚያ ፡ በንዳድ ፡
—እረ ፡ ጥላ ፡ ጥላ ፡ ቊረጥልኝ ፡ ሆድ ።

ሠ ፡ ወዳጄ ፡ ሆይ ፡ ከፀሓይ ፡ የምከለልበት ፡ ጥላ ፡ የሚሆነኝ ፡ ቅጠል ፡ ቊረጥልኝ ፤ ቅጠፍልኝ ።

ወ ፡ ሆዴ ፡ የሷን ፡ ነገር ፡ ተወው ፤ ፍቅሯን ፡ ርሳው ፤ ትዝታዋን ፡ ዘን ጋው ፤ እንዠቴ ፡ የሷን ፡ ነገር ፡ ቊረጥልኝ ፤ ርግፍ ፡ አድርገህ ፡ ተወው ።

70 በገብስማ ፡ ዶሮ ፡ እየተመኻኘ ፡
በወሰራ ፡ ዶሮ ፡ እየተመኻኘ ፡
—የኔስ ፡ በሽታዬ ፡ ሰው ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ።

ሠ ፡ ሕመሜ ፡ ታወቀ ፤ ዐይነ ፡ ወግ ፡ መሆኑ ፡ ተረጋገጠ ፤ ለካ ፡ የሚያመኝ ፡ እጅ ፡ ሰብ ፡ (ቡዳ) ፡ ኖሯል ።

ወ ፡ ለካ ፡ የሚያስጨንቀኝ ፡ የሚያሠቃየኝ ፡ ሕመሜ ፡ የወዳጄ ፡ «የተገኘ» ፡ ፍቅር ፡ ኖሯል ፤ በሽታዬ ፡ ሰው ፡ መውደድ ፡ በፍቅር ፡ መውደቅ ፡ ሆኖ ፡ ተገኘ ።

71 በጨለማ ፡ ስሄድ ፡ ማነህ ፡ ይለኛል ፡ ሰው ፤
—ተልኬ ፡ አይደለም ፡ ወይ ፡ የምመላለሰው ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 38) ፡

ሠ ፡ የምወጣው ፡ የምወርደው ፡ እየተላክሁ ፡ ነው ፤ ወዲያ ፡ ወዲህ ፡ የምለውም ፡ መልክት ፡ ለማድረስ ፡ ነው ።

ወ ፡ ሁል ፡ ጊዜ ፡ የምሄደው ፡ ከወዳጄ ፡ ከልኬ ፡ ዘንድ ፡ ነው ፤ የምመላለስ ፡ እርሷ ፡ ቤት ፡ ነው ።

72 በጭራሽ ፡ አገርሽ ፡ ትሄጂ ፡ እንደሆን ፡
—አብረሽ ፡ እንዳትወስጂው ፡ ተይልኝ ፡ ስሜን ።

ሠ ፡ ሁለተኛ ፡ ስሜን ፡ እንዳታነሽ ፤ እገሌ ፡ ብለሽም ፡ አትጥራብኝ ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ ስሜን ፡ አትንኪብኝ ፤ ከሱ ፡ ጋራ ፡ ባየሁሽ ፡ ቀን ፡ መጣላታችን ፡ ነው ።

73 ቢሆንም ፡ ይሆናል ፡ ባይሆንም ፡ አይሆንም ፤
—ቢማር ፡ ቄስ ፡ ነው ፡ እንጂ ፡ ሰው ፡ መላክ ፡ አይሆንም ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ምንም ፡ ቢማር ፡ ሊቅ ፡ ቢሆን ፡ መልአክ ፡ መሆን ፡ አይችልም ።

ወ ፡ ሰው ፡ መላክ ፡ ይቅርብህ ፡ አንተ ፡ ራስህ ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ብለህ ፡ ና ።

74 ቢነግሩሽ ፡ አትሰሚ ፡ ቢጠቅሱሽ ፡ አታዪ ፤
—ዝግ ፡ ብለሽ ፡ ሂጂ ፡ ብር ፡ ብር ፡ አትበዪ ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 125) ፡

ሠ ፡ ረጋ ፡ ብለሽ ፡ ተራመጅ ፤ አትክለፍለፊ ፤ ጥላ ፡ ቢስ ፡ አትሁኝ ።

ወ ፡ ለገንዘብ ፡ ብለሽ ፡ ካልሆነ ፡ ሰው ፡ እጅ ፡ አትውደቂ ፤ አቻሽን ፡ ፈልገሽ ፡ አግቢ ።

75 ባይንሽ ፡ ጕድፍ ፡ ገባ ፡ ሁሉን ፡ አይ ፡ ብለሽ ፤
—ሳያምሽም ፡ አይቀር ፡ ሳይቈረቈርሽ ።

ሠ ፡ ዐይንሽ ፡ የገባው ፡ ጕድፍ ፡ ሳያምሽ ፡ ሳይቈረቈርሽ ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ ያንንም ፡ ያንንም ፡ አይ ፡ ብለሽ ፡ ያ ፡ የተውሽው ፡ ሁነኛ ፡ ወዳጅሽ ፡ እያደር ፡ ሳይቈጭሽ ፡ አይቀርም ፤ የርሱ ፡ ነገር ፡ ውሎ ፡ አድሮ ፡ የእግር ፡ እሳት ፡ ይሆንብሻል ።

76 ቤተ ፡ ክሲያን ፡ አትግቢ ፡ አላችኋት ፡ ምነው ፤
—ደማምነቷማ ፡ ተፈጥሮዋ ፡ እንጂ ፡ ነው ።

ሠ ፡ የሴቶች ፡ የወር ፡ ግዳጅ ፡ ( አበባ ) ፡ በተፈጥሮ ፡ ያለ ፡ ነው ፤ ከቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ መግባት ፡ የሚያስከለክላት ፡ ርኵሰት ፡ አይደለም ።

ወ ፡ ቈንጆ ፡ ደም ፡ ግባቷ ፡ የሚማርክ ፡ ነች ፤ ደማም ፡ ውብ ፡ በመሆኗ ፡ የሰውን ፡ ልብ ፡ የምታነኖልል ፡ ፍጡር ፡ ነች ።

77 ብርማ ፡ መቼ ፡ አጣሁ ፡ ባቍማዳዬ ፡ ሙሉ ፡
—አሁን ፡ አጠገቤ ፡ የሺ ፡ ወርቄን ፡ ጣሉ ። (ን ፡ ኀ ፡ መ) ፡

ሠ ፡ አሁን ፡ ባሁን ፡ አንድ ፡ ሺሕ ፡ ብር ፡ የሚያወጣ ፡ ወርቄን ፡ ጣሉብኝ ፤ ታላቅ ፡ ዋጋ ፡ ያለውን ፡ ዕቃ ፡ አሶሰዱብኝ ።

ወ ፡ ወዳጂን ፡ የሺ ፡ ወርቅን ፡ ካለችበት ፡ ፈልጋችሁ ፡ አምጡልኝ ።

78 ብዙ ፡ ሸቀጥ ፡ ነበር ፡ ቀድሞ ፡ ከቤትሽ ፤
—እንዴት ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ነው ፡ አንቺን ፡ የገዛሽ ።

ሠ ፡ ያን ፡ ሁሉ ፡ በቤትሽ ፡ የነበረውን ፡ ሸቀጥሽን ፡ የገዛሽ ፡ እንዴት ፡ ያለ፡ ሰው ፡ ነው ፤ ንግድሽን ፡ በሙሉ ፡ በጅምላ ፡ የወሰደልሽ ፡ ሰው ፡ ማነው ።

ወ ፡ አንችን ፡ በፍቅር ፡ ገዝቶ ፡ የሚያኖርሽ ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ነው ፤ እንዴት ፡ ያለ ፡ የታደለ ፡ ነው ።

79 ብዙ ፡ አድርገን ፡ አዘን ፡ ዝናሽን ፡ ብንሰማ ፤
—ማንን ፡ ደስ ፡ ይለዋል ፡ አንች ፡ ተከፋሽማ ።

ሠ ፡ አንች ፡ ሆድ ፡ ከባሰሽ ፡ በሆነ ፡ ባልሆነ ፡ ከተከፋሽ ፡ ባንች ፡ የሚደሰተው ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ ይሆናል ፤ ይጨነቅ ፡ ይቸገር ፡ የለምን ።

ወ ፡ ያንች ፡ ሆድ ፡ ከጨከነ ፡ ማዘን ፡ መራራቱን ፡ ከተወው ፡ ማን ፡ ይደስታል ።

80 ብነግርህ ፡ ብመክርህ ፡ ምነው ፡ አልሰማ ፡ አልህ ፤
—ሲመሽ ፡ አትምጣብኝ ፡ ከንግዲህ ፡ ወዲህ ።

ሠ ፡ የምነግርህን ፡ ስማ ፤ በምሽት ፡ አትምጣ ፤ የፈቀደው ፡ ቢሆን ፡ በጨለማ ፡ አትሂድ ፤ ከመሸ ፡ ወዲያ ፡ ከቤትህ ፡ አትውጣ ።

ወ ፡ ማታ ፡ ማታ ፡ በትዝታ ፡ እየመጣህ ፡ አታስጨንቀኝ ፤ ፍቅርህ ፡ እንቅልፍ ፡ አይንሣኝ ፤ መተኛት ፡ አይከልክለኝ ።

81 ብንጠይቅ ፡ ዝናዋን ፡ የመጡትን ፡ ሁሉ ፡
—ያነንም ፡ ቤት ፡ ከፍታ ፡ ትታ ፡ ዋለች ፡ አሉ ።

ሠ ፡ መቼም ፡ የከፈተችውን ፡ መዝጋት ፡ አይሆንላትም ፤ ደግሞ ፡ ያንንም ፡ ቤት ፡ ከፍታ ፡ ሳትዘጋው ፡ ሄዳለች ፡ አሉ ።

ወ ፡ ያንን ፡ ቤት ፡ በክፋቷ ፡ አውድማው ፡ አጥፍታው ፡ ባዶውን ፡ አስቀርታዋለች ፤ ዐይኑ ፡ ተዙላውን ፡ አሳጥታዋለች ።

82 ተላልኬ ፡ ነበር ፡ ግብር ፡ አምጡ ፡ ብዬ ፤
—መናኛው ፡ መጣና ፡ ማለፊያው ፡ ዘገ(የ)ዬ ።

ሠ ፡ ግብር ፡ እንዲሠራ ፡ ማእድ ፡ እንዲቀርብ ፡ አዝዤ ፡ ነበር ፤ ከገበታ ፡ ሥር ፡ የሚውለው ፡ መናኛው ፡ መጣና ፡ ጥሩ ፡ እንጀራ ፡ ሳይቀርብ ፡ ቀረ ፤ ወደ ፡ ኋላ ፡ ዘገየ ።

ወ ፡ ልቤ ፡ የማይፈቅደው ፡ መጣና ፤ አንዠቴ ፡ የሚዋልልለት ፡ ቀልጣፋው ፡ «ዘገየ» ፡ ቀረ ።

83 ተልኬ ፡ መጣሁኝ ፡ ያን ፡ ሁሉ ፡ መንገድ ፤
—አትስሙኝ ፡ ፈቅ ፡ በሉ ፡ ነግሪያት ፡ ልሂድ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡ (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 38 ፡ 71) ፡

ሠ ፡ ዘወር ፡ በሉ ፤ የምነግራት ፡ ምስጢር ፡ አለኝ ፤ አትስሙኝ ፡ ፈቅ ፡ በሉ ፤ አታዳምጡ ፤ ከርሷ ፡ ጋራ ፡ ቈይታ ፡ አለኝ ።

ወ ፡ ገለል ፡ በሉ ፤ ወዳጄ ፡ ልኬን ፡ ላነጋግርበት ፤ ብዙ ፡ ቀን ፡ ተለይታኝ ፡ የቈየች ፡ ነች ፤ መነፋፈቅ ፡ በልባችን ፡ አለና ፤ አትስሙኝ ።

84 ተናግሬ ፡ ነበር ፡ ሊመጣ ፡ ነው ፡ ብዬ ፤
—ዐውቄ ፡ እንኳ ፡ አይደለ ፡ እንዲያው ፡ መላ ፡ ጥዬ ።

ሠ ፡ ሳላውቅ ፡ በመላ ፡ ይመጣል ፡ ያልኩት ፡ ሰው ፡ መጣ ፤ አቦ ፡ ሰጡኝ ፤ የተናገርኩት ፡ ነገር ፡ እውነት ፡ ሆነ ።

ወ ፡ የማፈቅረው ፡ የምወደው ፡ የኔ ፡ መላጣ ፡ ይኸው ፡ እንደ ፡ ተናገርኩት ፡ መጣ ።

85 ተገዝቼ ፡ መጣሁ ፡ በሰባት ፡ አቡን ፤
—ሥራዬን ፡ ላልፈታ ፡ ቦዘኔ ፡ ላልሆን ።

ሠ ፡ ሰነፍ ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡ እንዳልሆን ፡ ጊዜዬን ፡ ያለሥራ ፡ እንዳላባክን ፡ ምዬ ፡ ተገዝቼ ፡ መጣሁ ፤ ለሰባት ፡ አቡን ፡ ቃሌን ፡ ሰጥቼ ፡ ተመለስኩ ።

ወ ፡ ሚስቴን ፡ «ሥራዬን» ፡ እንዳልፈታ ፡ ከባለቤቴ ፡ እንዳልለያይ ፡ ቃሌን ፡ ለቄስ ፡ ሰጥቼ ፡ መጣሁ ።

86 ታናሽ ፡ ታላቅ ፡ ሥጋ ፡ እያለ ፡ ከቤቴ ፡
—ሽኾና ፡ አስወደደኝ ፡ ምንድነው ፡ ብልኀቴ ። (አ ፡ ወ ፡ ጊ) ፡

ሠ ፡ ዐመሌ ፡ ግራ ፡ አገባኝ ፤ የማደርገው ፡ መላ ፡ ቅጡ ፡ ጠፋኝ ፤ ታላቅ ፡ ታናሽ ፡ እያለ ፡ ሽኾና ፡ የጥፍር ፡ ሥጋ ፡ ያሰኘኛል ።

ወ ፡ ስንት ፡ ወይዛዝሮች ፡ እያሉ ፡ እዚህ ፡ ግቢ ፡ የማይኗትን ፡ ገረድ ፡ ሽኾን ፡ አስወደደኝ ፤ በርሷ ፡ ላይ ፡ ፍቅር ፡ ጣለብኝ ።

87 ታጠቢ ፡ አትልም ፡ ወይ ፡ ከሆነስ ፡ እናት ፤
—እረ ፡ እድፉ ፡ ምንድነው ፡ ከዚያች ፡ ልጅ ፡ አንገት ።

ሠ ፡ ውሃ ፡ በመንደሩ ፡ የለም ፡ ወይ ፤ ለምን ፡ ልጅቷ ፡ አንገቷ ፡ ላይ ፡ ያለውን ፡ እድፍ ፡ አትታጠበውም ።

ወ ፡ በዚያች ፡ ልጅ ፡ አንገት ፡ ላይ ፡ የሚታየው ፡ እንደ ፡ ዕርከን ፡ ሆኖ ፡ ረድፍ ፡ ረድፍ ፡ ያበጀው ፡ ነገር ፡ ምንድነው ።

88 ትላንትና ፡ ማታ ፡ አሻሮ ፡ ሸቶኝ ፡
—እረ ፡ ጠላ ፡ ሆዴ ፡ ትዝም ፡ አትለኝ ።

ሠ ፡ ጠላ ፡ አያምረኝም ፤ ምንም ፡ የብቅልና ፡ የጌሾ ፡ ነገር ፡ ውል ፡ አይለኝም ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ አትናፍቀኝም ፤ ፍቅር ፡ በቅቶኛል ፤ ትዝታም ፡ ተረስቶኛል ፤ መኖር ፡ አለመኖሯ ፡ እንኳ ፡ አይታወሰኝም ።

89 ትላንትና ፡ ጠፋሽ ፡ ሰው ፡ ብልክብሽ ፤
—እንጫወትም ፡ ወይ ፡ አንድ ፡ እግር ፡ መጥተሽ ።

ሠ ፡ መላላኩ ፡ ቀርቶ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ብቅ ፡ ብለሽ ፡ እንጫወትም ፡ ወይ ።

ወ ፡ አንድ ፡ እግረ ፡ ቈራጢት ፡ መጥተሽ ፡ እንጫወትም ፡ ወይ ።

90 ትላንት ፡ ኮሶ ፡ ጠጣሁ ፡ ዛሬ ፡ መረረኝ ፤
—እስቲ ፡ አራዳ ፡ ልውጣ ፡ ብርቱካን ፡ ባገኝ ።

ሠ ፡ ለኮሶው ፡ ምሬት ፡ የምመጠው ፡ ብርቱካን ፡ ይገኝ ፡ እንደሆን ፡ አራዳ፡ ወጥቼ ፡ ልግዛ ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ ብርቱካንን ፡ ባገኝ ፡ እስቲ ፡ አራዳ ፡ ገበያ ፡ ወጥቼ ፡ ልፈልጋት ።

91 ትልቁን ፡ አሳዛ ፡ ሸጠችው ፡ ለብር ፤
—ትንሽ ፡ ለምድ ፡ አመጣች ፡ የሚቈረቍር ። (ብ ፡ ወ ፡ ሐ)፡

ሠ ፡ ቢተኙበት ፡ ሙቀት ፡ የሌለው ፡ ትንሽ ፡ ድብዳብ ፡ ደላጎ ፡ ቢጤ ፡ አምጥታ ፡ ሰጠችኝ ፤ ትልቁን ፡ አሳዛ ፡ ለካ ፡ ሸጣዋለች ።

ወ ፡ የሚከነክን ፡ ትዕግሥት ፡ የሚያስጨርስ ፡ ደግሞ ፡ መጥፎ ፡ ልማድ ፡ አመጣች ፤ ትልቁን ፡ ወዳጅዋን ፡ ትታ ፡ ትንሽ ፡ ሰው ፡ ለምዳ ፡ መጣች ።

92 ትመስሊኝ ፡ ነበረ ፡ የቡልጎች ፡ ወገን ፤
—እኔ ፡ መች ፡ ዐወቅሁት ፡ ጠሬ ፡ መሆንሽን ። (ኤልያስ ፡ ወልደ ፡ ጻድቅ)፡

ሠ ፡ እኔ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ ሳይሽ ፡ የቡልጋ ፡ ሴት ፡ ትመስሊኝ ፡ ነበር ፤ የጠራ ፡ ተወላጅ ፡ መሆንሽን ፡ አላውቅም ፡ ነበር ።

ወ ፡ የሮሮዬ ፡ ጠባቂ ፡ የኔ ፡ ወገን ፡ ትመስሊኝ ፡ ነበር ፤ ጠላቴ ፡ ፀሬ ፡ መሆንሽን ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ አልተረዳሁትም ፡ ነበር ።

93 ትመጫለሽ ፡ ብዬ ፡ አሻግሬ ፡ ሳይ ፡
—አንች ፡ ልጅ ፡ ማለፊያ ፡ መንገድ ፡ አጣሽ ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ከአሁን ፡ አሁን ፡ ትመጫለሽ ፡ ብዬ ፡ መንገድ ፡ መንገዱን ፡ ሳይ ፡ ቀረሽ ፤ የዘገየሽው ፡ በደኅናሽ ፡ ነውን ፤ ወይስ ፡ መሸጋገሪያ ፡ መተላለፊያ ፡ አጥተሽ ፡ ነውን ።

ወ ፡ አንቺ ፡ ይህ ፡ ቀረሽ ፡ የማትባይ ፡ ቈንጆ ፡ ልጅ ፡ ወደኔ ፡ ለመምጣት ፡ ሰበብ ፡ ምክንያት ፡ አጥተሽ ፡ ነው ፡ ወይ ፡ የቀረሽው ።

94 ትሰሙኝ ፡ እንደሆን ፡ ልንገራችሁ ፡ በውነት ፤
—በራሰው ፡ እንዝርት ፡ ነው ፡ መድኀኒት ፡ መጠጣት ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 220)፡

ሠ ፡ መድኀኒት ፡ ከመጠጣት ፡ በፊት ፡ ሆድን ፡ ማለስለስ ፡ እንዝርትን ፡ ማራስ ፡ ያስፈልጋል ።

ወ ፡ በእእምሮ ፡ የበሰለ ፡ ራስ ፡ በራ ፡ ሰው ፡ መውደድ ፡ መልካም ፡ ነው ፤ ትዝታው ፡ ማራኪ ፡ ነው ።

95 ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ሂጂ ፡ ወንበዴው ፡ ሳይጠና ፤
—ከዚህ ፡ ስፍራ ፡ ቀረሽ ፡ አትባይምና ።

ሠ ፡ ቶሎ ፡ ቶሎ ፡ ሄደሽ ፡ በጊዜ ፡ እቤትሽ ፡ ግቢ ፤ ወንበዴው ፡ ከፍቷል ፤ ይመሽብሽና ፡ ዐጕል ፡ ቦታ ፡ ወድቀሽ ፡ ትቀሪያለሽ ።

ወ ፡ እንከን ፡ የማይገኝብሽ ፡ ይህ ፡ ቀረሽ ፡ የማትባይ ፡ ነሽ ፤ ከቶ ፡ ምንም ፡ ጕድለት ፡ የለብሽም ፤ ውበትሽ ፡ ፍጹም ፡ ነው ።

96 ነድፌ ፡ ነድፌ ፡ ባልጋ ፡ ከምሪያለሁ ፤
—የዛሬ ፡ ቀን ፡ ከብዷል ፡ ባል ፡ አለ ፡ ብያለሁ ።

ሠ ፡ ዛሬ ፡ ቀን ፡ ይቀፋል ፤ እጅግ ፡ ይከብዳል ፤ በዓል ፡ ሳይኖርበት ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ ዛሬ ፡ ለጨዋታ ፡ አይመችም ፤ ባለቤቴ ፡ ከቤት ፡ ውሏል ።

97 ነጋዴ ፡ ነህ ፡ አሉ ፡ እኔስ ፡ አልነግድም ፤
—ወረቱ ፡ ካለቀ ፡ ሰው ፡ አይወደድም ።

ሠ ፡ መረጃ ፡ ገንዘብ ፡ የሌለው ፡ ቅርሱ ፡ ያለቀበት ፡ ሰው ፡ አይወደድም ።

ወ ፡ ፍቅሩ ፡ ካረጀ ፡ ወረቱ ፡ ካለቀ ፤ ሰው ፡ አይፈለግም ፤ መተሳሰብ ፡ አይኖርም ።

98 ና ፡ ብትይኝ ፡ መጣሁ ፡ ብመጣም ፡ አንች ፡ የለሽ ፤
—ያመት ፡ ባል ፡ ቤተ ፡ ክሲያን ፡ ሆኖ ፡ ቈየኝ ፡ ደጅሽ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡
(ዘለ ፡ ቍ ፡ 213) ፡

ሠ ፡ ልጠይቅሽ ፡ ብመጣ ፡ ደጅሽ ፡ ክብረ ፡ በዓል ፡ ያለበት ፡ ታቦት ፡ የሚነግሥበት ፡ የቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ማርገጃ ፡ ሆኖ ፡ አገኘሁት ፡ ብዙ ፡ ሰው ፡ በደጅሽ ፡ ነበር ።

ወ ፡ በደጅሽ ፡ የሚታዩ ፡ ፈላጊዎችሽ ፡ ብዙዎች ፡ ናቸው ፤ ላገኝሽም ፡ አልቻልኩም ።

99 አሁን ፡ ምን ፡ ቸገረሽ ፡ አብረን ፡ ብናመሽ ፤
—እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ነኝ ፡ አንቺ ፡ ብዙነሽ ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 187) ፡

ሠ ፡ እኔ ፡ የሚያነጋግረኝ ፡ አንድ ፡ ሰው ፡ እንኳ ፡ የለኝም ፤ አንቺ ፡ ብዙ ፡ አጫዋች ፡ አለሽ ፤ ብቻሽን ፡ አይደለሽም ፤ እባክሽ ፡ ነዪና ፡ አብረን ፡ እናምሽ ።

ወ ፡ ወዳጇ ፡ ብዙነሽ ፡ ዛሬ ፡ ብቻዬን ፡ ነኝና ፡ መጥተሽ ፡ አብረን ፡ እናምሽ ፤ ስንጫወት ፡ እንደር ።

100 አሁን ፡ ምን ፡ ያደርጋል ፡ ነገር ፡ መሊቃቀም ፤
—ባባቷ ፡ ያልሆነ ፡ ባያት ፡ ምን ፡ ልጠቀም ።

ሠ ፡ በቅርቡ ፡ ያባቷ ፡ ዝምድና ፡ ያልጠቀመኝ ፤ ባያቷ ፡ ብዛመድ ፡ ምን ፡ ይረባኛል ፤ አባቱን ፡ አያውቅ ፡ አያቱን ፡ ናፈቅ ፡ መሆን ፡ ነው ።

ወ ፡ የምወዳትን ፡ የምመኛትን ፡ ልጅ ፡ ካላገኘኋት ፤ ባያትና ፡ ብመለከታት ፡ ምን ፡ ይጠቅመኛል ።

101 አልሄድም ፡ ከቤቷ ፡ እኔ ፡ እፈራታለሁ ፤
—ዐይኗ ፡ ሰው ፡ ይወጋል ፡ ሲሉ ፡ ሰምቻለሁ ።

ሠ ፡ ጠይብ ፡ ናት ፡ ዐይኗ ፡ ሰውን ፡ ይተናኰላል ፡ ይዷታል ።
ወ ፡ ዐይን ፡ አገላለጧ ፡ ልብን ፡ ይማርካል ፤ ጕልበትን ፡ ያብረከርካል ።

102 አልፈልግም ፡ ሌላ ፡ ትበቂኛለሽ ፤
—ለቤቱ ፡ ጥበቃ ፡ በይ ፡ አንቺው ፡ አለሽ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 115) ፡

ሠ ፡ ቤቱን ፡ ለመጠበቅ ፡ አጥር ፡ ግቢውን ፡ ለመመልከት ፡ ሌላ ፡ ሰው ፡ አያሻም ፤ አንችው ፡ ትበቂያለሽ ።
ወ ፡ ሌላ ፡ ተጋባዥ ፡ አያስፈልግም ፤ የተሰናዳውን ፡ ለመብላት ፡ የተዘጋጀውን ፡ ለማባከን ፡ አንቺው ፡ በቂ ፡ ነሽ ።

103 አ(ዓ)ምና ፡ ወባ ፡ ጥሎት ፡ ሳስታምም ፡ ከርሜ ፡
—ባርያ ፡ ጣለው ፡ አሉ ፡ ምን ፡ ላርገው ፡ ደግሜ ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 177) ፡

ሠ ፡ ዓምና ፡ ወባ ፡ ጥሎት ፡ ሳስታምም ፡ ቈይቼ ፡ ዘንድሮ ፡ ደግሞ ፡ እያዞረ ፡ የሚጥል ፡ (ጋኔን) ፡ አደረበት ፤ በሽታ ፡ የማይለየው ፡ ሆነ ፤ ጣጣው ፡ በዛ ፤ ሕመሙ ፡ በረከተ ።
ወ ፡ አለ ፡ አለና ፡ ከባርያ ፡ ጋራ ፡ በፍቅር ፡ ወደቀ ፤ አቻውን ፡ የማያውቅ ፡ ሆነ ።

104 አ(ዐ)ሥራ ፡ ሁሉት ፡ ጥጃ ፡ ታስሮ ፡ ከደጅሽ ፣
—ወተት ፡ ብዬ ፡ ስሞት ፡ ምነዋ ፡ ጨከንሽ ።

ሠ ፡ አንቺ ፡ ቤት ፡ ዐሥራ ፡ ሁለት ፡ ጥገት ፡ ላሞች ፡ እያሉ ፡ እኔ ፡ በወተት ፡ እጦት ፡ ስሞት ፡ ምነው ፡ ጨከንሽ ፤ አንገሽትሽ ፡ እንዴት ፡ ቻለልሽ ።
ወ ፡ እኔ ፡ ባንቺ ፡ ናፍቆት ፡ ስዋትትና ፡ ስንገላታ ፡ አንቺ ፡ ለምን ፡ እንዲህ ፡ ትጨክኛለሽ ፤ ለምን ፡ ርኅራኄና ፡ አዘኔታ ፡ አይኖርሽም ።

105 አራዳ ፡ ለኪራይ ፡ ቤት ፡ የፈለጋችሁ ፡
—ዘማለች ፡ ምናልባት ፡ በውል ፡ እያያችሁ ። (አ ፡ በ) ፡ (ዘለ ፡ ቍ ፡ 194) ፡

ሠ ፡ የምትከራየዋ ፡ ቤት ፡ ወደ ፡ አንድ ፡ ወገን ፡ አዘንብላለች ፤ ልትወድቅ ፡ ጥቂት ፡ ቀርቷታል ፤ አጋድላለች ፤ ዘማለች ።
ወ ፡ ወደ ፡ አራዳ ፡ የምትወጡ ፡ ሁሉ ፡ እንዳትሳሳቱ ፡ ዘማዊት ፡ ሴት ፡ አለች ፤ ዐጓጕል ፡ እንዳትሆኑ ፡ ተጠንቀቁ ።

106 አሳጨደች ፡ አሉ ፡ አልማዝ ፡ ስንዴዋን ፤
—ትታልኝ ፡ አንድ ፡ እመም ፡ የማልችለውን ።

ሠ ፡ አልማዝ ፡ ድርሻ ፡ ፋንታዬን ፡ አንድ ፡ እመም ፡ አስቀርታልኝ ፡ የቀረውን ፡ እኽል ፡ አሳጨደች ።
ወ ፡ አልማዝ ፡ የሚያስጨንቅ ፡ የሚያስጠብብ ፡ የማይዘልቅ ፡ ፍቅር ፡ ትታልኝ ፡ ሄደች ።

107 አስቢያለሁና ፡ ልኖር ፡ አብሬህ ፡
ድንኳን ፡ አስተክዬ ፡ ተማሪ ፡ ቤትህ ፤
—አንተ ፡ ልጅ ፡ ሰሎሞን ፡ ተራዳ ፡ እባክህ ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ የድንኳን ፡ መትከያ ፡ ተራዳ ፡ እባክህ ፡ ስጠኝ ፡ አውሰኝ ።

ወ ፡ ሰሎሞን ፡ ባለ ፡ ዐቅምህ ፡ በሚቻል ፡ መንገድ ፡ ርዳኝ ፤ አግዘኝ ።

108 አሽከር ፡ የለውም ፡ ወይ ፡ ጭቃና ፡ ምስለኔ ፤
—ለስሜኝ ፡ እንግዳ ፡ ባዘዝኩለት ፡ እኔ ።

ሠ ፡ ስሜኝን ፡ የሚቀበለውና ፡ የሚያሳድረው ፡ ሰው ፡ ባዘዝኩለት ፡ ደግ ፡ ነበር ፤ የሚመራበት ፡ ቤት ፡ በሰጠሁት ፡ ነበር ።

ወ ፡ በስሜኝ ፡ እንግዳ ፡ ፍቅር ፡ ፈዘዝኩ ፤ ነኖለልሁ ፤ ቧዘዝሁ ፤ ተቅበዘበዝሁ ።

109 አቅላትን ፡ ወገምን ፡ ሁሉንም ፡ ታውቂያለሽ ፤
—እንዴት ፡ ጣሜ ፡ ጠፍቶሽ ፡ ታስጨንቂኛለሽ ።

ሠ ፡ «አቅላትና ፡ ወገም» ፡ የሚባሉትን ፡ አገሮች ፡ ስታውቂ ፡ እንዴት ፡ ጣሜ ፡ የሚባለው ፡ ቦታ ፡ ተሳተሽ ።

ወ ፡ አንቺ ፡ የኔ ፡ ነገር ፡ የማይጥምሽ ፡ ሆኖ ፡ ነውን ፡ እንዲህ ፡ የምታስጨንቂኝና ፡ የምታሳዝኚኝ ።

110 አበድሽ ፡ ብለውሻል ፡ እንግዲህ ፡ ጨምቺ ፤
—ተሙሉ ፡ አዳራሽ ፡ ሴት ፡ ትመቻለሽ ፡ አንቺ ።

ሠ ፡ አፍሽን ፡ አሳርፈሽ ፡ ምላስሽን ፡ ሰብስበሽ ፡ ተቀመጭ ፤ መክለፍለፍሽን ፡ ተዪ ፤ ኋላ ፡ ትመቻለሽ ።

ወ ፡ ከሴቶቹ ፡ ሁሉ ፡ ያንቺ ፡ ሰውነት ፡ ይመቻል ፤ ይደላል ።

111 አብረን ፡ ተቀምጠን ፡ መልካችን ፡ አንድ ፡ ነው ፤
—አሁን ፡ እኔና ፡ እሷን ፡ የሚለየን ፡ ማነው ።

ሠ ፡ በመልክ ፡ ተመሳሳይ ፡ ነን ፤ ኅብረ ፡ ገጻችን ፡ አንድ ፡ ነው ፤ እኔና ፡ እሷን ፡ ለይቶ ፡ ማወቅ ፡ የሚችል ፡ ማነው ።

ወ ፡ እኔና ፡ እሷን ፡ መለያየት ፡ የሚቻለው ፡ የለም ።

112 አብረን ፡ እንደ ፡ ከረምን ፡ በግንቦት ፡ በሰኔ ፤
—በበጋ ፡ እንሻገር ፡ ዋና ፡ አላውቅም ፡ እኔ ።

ሠ ፡ ክረምቱ ፡ ሲያልፍ ፡ ውሃ ፡ ሲጐድል ፡ በበጋ ፡ ወንዙን ፡ ተሻግረን ፡ እንሂድ ፤ እኔ ፡ መዋኘት ፡ አላውቅም ፤ የሞላ ፡ ወንዝ ፡ መሻገር ፡ አልችልም ።

ወ ፡ ተጠንቀቅ ፡ አያዋጣህምና ፤ ዋ ፡ ቶሎ ፡ ብትመጣ ፡ ይሻላል ፤ እንዳይቈጭህ ፡ ውርድ ፡ ከራሴ ፡ ነው ።

113 አትውሰጂው ፡ ሲሏት ፡ የሰው ፡ ዕቃ ፡ ወስዳ ፡
—ደግሞ ፡ ጥላ ፡ መጣች ፡ ልታገባን ፡ ዕዳ ።

ሠ ፡ የሰው ፡ ዕቃ ፡ ወስዳ ፡ ጥላ ፡ ደግሞ ፡ ዕዳ ፡ ልታገባን ፡ ገንዘብ ፡ ልታስ ገባን ፡ ተመልሳ ፡ መጣች ።

ወ ፡ አምባጓሮ ፡ አበቀለች ፤ ጥል ፡ ክርክር ፡ አመጣች ፤ ደግሞ ፡ በሷ ፡ የተ ነሣ ፡ ጣጣ ፡ ልንገባ ፡ ነው ።

114 አትወጅኝም ፡ ያልከው ፡ የጠላሁህ ፡ የታል ፤
—አንድ ፡ አንገት ፡ ነው ፡ ያለኝ ፡ ተኝተህበታል ።

ሠ ፡ በሆዴ ፡ ላይ ፡ ተኝተህበታል ፤ ሌላ ፡ ቦታ ፡ የለም ።

ወ ፡ በሙሉ ፡ ልቤ ፡ እወድሃለሁ ፤ አንገቴ ፡ ነህ ፤ አንተን ፡ የምጠላበት ፡ ነገር ፡ የለኝም ።

115 አንተም ፡ ሴት ፡ ይመስል ፡ ትፈራለህ ፡ ወይ ፤
—ሲመሽ ፡ በጨለማ ፡ አትመጣውም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ለምን ፡ ሲመሽ ፡ ሲጨልም ፡ ሰው ፡ ጭር ፡ ሲል ፡ ማታ ፡ አትመ ጣም ፤ ለምን ፡ ሴት ፡ ይመስል ፡ ትፈራለህ ።

ወ ፡ አውሬ ፡ የማይተናኰልህ ፡ ጠይብ ፡ ነህ ፤ በጨለማ ፡ መምጣት ፡ ምን ፡ ያስፈራሃል ።

116 አንተ ፡ ብትመጣ ፡ ምን ፡ ታደርጋለህ ፤
—ሐኪሙን ፡ ላክልኝ ፡ አድነው ፡ ብለህ ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ብትመጣ ፡ ባትመጣ ፡ ግድ ፡ የለም ፤ ሐኪሙን ፡ ግን ፡ እ ንደ ፡ ምንም ፡ ርዳው ፡ አድነው ፡ ብለህ ፡ ላክልኝ ።

ወ ፡ ወዳጄን ፡ አድነውን ፡ እንደ ፡ ምንም ፡ ብለህ ፡ ተቸግረህም ፡ ቢሆን ፡ ወደኔ ፡ ላክልኝ ፤ የሱ ፡ ነገር ፡ አይሆንልኝምና ።

117 አንተ ፡ የጓሮ ፡ ፍየል ፡ ብትስል ፡ ብታነጥስ ፡
—ዛሬ ፡ ባል ፡ ነውና ፡ ቅጠልም ፡ አልበጥስ ።

ሠ ፡ ዛሬ ፡ የፈሰሰ ፡ ውሃ ፡ እንኳ ፡ አላቀናም ፤ ዓመት ፡ በዓል ፡ ነው ፤ ሥራ ፡ አይሠራበትም ፤ ርጥብ ፡ ቅጠል ፡ እንኳ ፡ መበጠስ ፡ አይገ ባም ።

ወ ፡ ዛሬ ፡ ባሌ ፡ ከቤት ፡ ስላለ ፡ ላጫውትህ ፡ አልችልም ።

118 አንቺስ ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ ለምን ፡ ትደፍሪያለሽ ፤
—እንዴት ፡ በሰው ፡ ሸክላ ፡ እሳት ፡ ትጭሪያለሽ ።

ሠ ፡ ለምን ፡ በሰው ፡ ገል ፡ እሳት ፡ ትጭሪያለሽ ፤ የሰው ፡ ዕቃ ፡ ትነኪያ ለሽ ።

ወ ፡ የሰውን ፡ ገላ ፡ ለምን ፡ በበሽታሽ ፡ ታቃጥያለሽ ።

119 አንቺ ፡ አትሰፊውም ፡ ወይ ፡ አክርማ ፡ ቀጭተሽ ፤
—ስንት ፡ ቅል ፡ ቢኖር ፡ ነው ፡ ለጠብ ፡ የፈለግሽ ።

ሠ ፡ ብዙ ፡ ቅል ፡ ለጠብ ፡ ከምታደርጊ ፡ ለምን ፡ አክርማ ፡ ቀጭተሽ ፡ በሙሉ ፡ ራስሽ ፡ አትሰሪውም ።

ወ ፡ ለምን ፡ ጠብና ፡ ጭቅጭቅ ፡ ትፈልጊያለሽ ፤ ንዝንዝ ፡ ታበዢለሽ ።

120 አንቺ ፡ እበላ ፡ ባይ ፡ ሴት ፡ አንቺ ፡ ተግደርዳሪ ፡
—አላየሁም ፡ እንዳንች ፡ ከሴቶች ፡ ባልሻሪ ።

ሠ ፡ እንዳንች ፡ በዓልን ፡ የሚሽር ፡ ሰንበትን ፡ የማያከብር ፡ አላየሁም ።

ወ ፡ ባሏን ፡ በየጊዜው ፡ የምትፈታ ፡ ጋብቻዋን ፡ የምታፈርስ ፤ እንዳንች ፡ ያለች ፡ ሴት ፡ አላየሁም ።

121 አንቺን ፡ የለመዱ ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሳሉ ፡
—በቤት ፡ ሙሉ ፡ አዛኝሮሽ ፡ እንግዳ ፡ ነው ፡ አሉ ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 54) ፡

ሠ ፡ ቤትሽን ፡ በጣም ፡ የሚያውቁት ፤ ጓዳውንና ፡ ውስጡን ፡ የተረዱት ፡ የለመዱት ፡ ብዙ ፡ ሰዎች ፡ ሳሉ ፤ በቤትሽ ፡ ውስጥ ፡ አስተናባሪው ፡ እንግዳ ፡ ነው ፤ አዛዥሮሽ ፡ ባይተዋር ፡ ነው ።

ወ ፡ በሰውነትሽ ፡ የሚያዘው ፡ ወዳጅሽ ፡ እንግዳ ፡ ነው ፡ ይላሉ ፤ ከሱ ፡ በቀር ፡ ሌላ ፡ የምታምኝው ፡ የምታቀርቢው ፡ ሰው ፡ የለም ።

122 አንች ፡ አሽከር ፡ ነገርሽ ፡ ከኮሶ ፡ ባሰሳ ፤
—ያስቀምጠኝ ፡ ዥመር ፡ ሌሊት ፡ እያስነሣ ።

ሠ ፡ ሌሊት ፡ እያስነሣ ፡ ያስቀምጠኝ ፡ ዥመር ፤ በየጊዜው ፡ ያመላልሰኛል ፤ ተቅማጡ ፡ አስቸገረኝ ።

ወ ፡ ትዝታሽ ፡ አላስተኛም ፡ አለኝ ፤ በደረቅ ፡ ውድቅት ፡ እያስነሣ ፡ ቍጭ ፡ አድርጎ ፡ ያሳድረኛል ።

123 አንድ ፡ የሰው ፡ አሞራ ፡ አስቀምጬ ፡ እቤት ፡
—እጠብቃለሁኝ ፡ ቀንና ፡ ሌሊት ።

ሠ ፡ አንድ ፡ የሰው ፡ ለማዳ ፡ አሞራ ፡ እቤት ፡ አስቀምጬ ፡ ሌት ፡ ከቀን ፡ እንዳይጠፋ ፡ እጠብቃለሁ ።

ወ ፡ እንደ ፡ አሞራ ፡ ከተፎ ፡ የሆነው ፡ ወዳጄን ፡ እንዳይሄድብኝና ፡ ሌላ ፡ ወዳጅ ፡ እንዳያበጅብኝ ፡ ቀን ፡ ከሌት ፡ እጠብቀዋለሁ ፤ እከታተለዋለሁ ።

124 አንዠቴ ፡ ተቈርጦ ፡ ከሆዴ ፡ ከወጣ ፤
—እንግዲህ ፡ ወጌሻው ፡ ምን ፡ ሊቀጥል ፡ መጣ ።

ሠ ፡ ሆድ ፡ ዕቃዬ ፡ ከአካሌ ፡ ተለይቶ ፡ ከሄደ ፡ በኋላ ፡ ጅባት ፡ ከተባለ ፡ ወዲህ ፡ ሐኪሙ ፡ ምን ፡ ሊፈጥር ፡ መጣ ፤ ነፍስ ፡ መዝራት ፡ ይችላልን ።

ወ ፡ ሆዴ ፡ አንዠቴ ፡ የነበረውን ፡ ወዳጄን ፡ ርግፍ ፡ አድርጌ ፡ ከተውሁትና ፡ ልቤ ፡ ተቈረጠልኝ ፡ ወዲህ ፤ ያማላጁ ፡ ጋጋታ ፡ ምን ፡ ሊያሻሽል ፡ ነው ፤ ምን ፡ ፋይዳ ፡ ሊሞላ ፡ ነው ።

125 አንገት ፡ የለሽም ፡ ወይ ፡ አዙሮ ፡ የሚያይ ፤
—ሲመሽ ፡ ብር ፡ ብለሽ ፡ ትሄጃለሽ ፡ ወይ ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 74) ፡

ሠ ፡ ጀንበር ፡ መጥለቋን ፡ መምሸቷን ፡ እያየሽ ፡ እንዴት ፡ በጨለማ ፡ ብር ፡ ብዬ ፡ ልሂድ ፡ ትያለሽ ፤ መሮጥ ፡ ያለብሽ ፡ ፀሐይ ፡ ካለች ፡ ነበር ።

ወ ፡ ለገንዘብ ፡ ለብር ፡ ብለሽ ፡ በጨለማ ፡ መሄድ ፡ ይገባልን ።

126 አው ፡ ብትል ፡ ኸርቦ ፡ መች ፡ እፈራሃለሁ ፤
—እኔንም ፡ ና ፡ ብላኝ ፡ ከበሯ ፡ ቈሚያለሁ ።

ሠ ፡ አያ ፡ ኸርቦ ፡ እስቲ ፡ ና ፡ ብላኝ ፤ ከበር ፡ ቆሜልሃለሁ ፤ ጩኸትህን ፡ አልፈራም ፤ በደጅ ፡ ቆሜ ፡ እጠብቅሃለሁ ።

ወ ፡ እኔንም ፡ ጠርታኝ ፡ ቀጠሮ ፡ ሰጥታኝ ፡ ይኸውና ፡ በበር ፡ ተገትሬ ፡ እጠባበቃለሁ ፤ ደጅ ፡ እጠናለሁ ፤ ካሁን ፡ አሁን ፡ ከፈተችልኝ ፡ እ ያልሁ ፡ ምድራኽ ፡ ምድራኹን ፡ እመለከታለሁ ።

127 አውራ ፡ ዶሮ ፡ ጭሮ ፡ እኽልሽን ፡ ሲያፈሰው ፡
—እሽ ፡ አለማለትሽ ፡ የሚገርም ፡ እኮ ፡ ነው ።

ሠ ፡ ዶሮ ፡ እኽሉን ፡ ሲበላው ፡ ስጡን ፡ እየጫረ ፡ ሲያፈሰው ፡ አለመከል ከልሽ ፡ የሚገርም ፡ ነው ።

ወ ፡ ፈቃድሽ ፡ ቢሆን ፡ ብትለመኝ ፡ ምን ፡ አለበት ፤ መዥራትሽ ፡ ዕሺ ፡ ይሁን ፡ አለማለትሽ ፡ የሚደንቅ ፡ ነው ፡ እኮ ።

128 አየሁ ፡ አዝመራሽን ፡ አውሬ ፡ ሲጨርሰው ፤
—እንግዴህ ፡ ትቀሪ ፡ ይመስለዋል ፡ ለሰው ።

ሠ ፡ እንግዲህ ፡ ዝንጀሮ ፡ ዐሣማና ፡ እሪያ ፡ ለመጠበቅ ፡ አውሬ ፡ ለመከ ልከል ፡ ሰብል ፡ ለማየት ፡ የማትወጪ ፡ ይመስላል ።

ወ ፡ ሰው ፡ ይኽን ፡ ሲያይ ፡ ሁለተኛ ፡ የማትመጪ ፡ በዚያው ፡ የምትቀሪ ፡ ይመስለዋል ፤ ዳግመኛ ፡ መመለስሽን ፡ ይጠራጠራል ፤ አንቺ ፡ ግን ፡ እንዳትቀሪ ፡ አምናለሁ ።

129 አይደለ ፡ የመንፈቅ ፡ አይደለ ፡ የወር ፤
—እንደ ፡ ምን ፡ አለፍሽው ፡ ያመት ፡ ባልን ፡ ክብር ።

ሠ ፡ ዐውዳመቱን ፡ ክብረ ፡ በዓሉን ፡ እንዴት ፡ አሳለፍሽው ፤ በዓሉ ፡ በ መልካም ፡ አለፈ ፡ ወይ ፤ በሚገባ ፡ በደኅና ፡ እንግዳው ፡ ተሸኘልሽ ፡ ወይ ።

ወ ፡ ባልሽን ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ መናቅ ፡ አይገባሽም ፤ ክብሩን ፡ መብቱን ፡ መጠበቅ ፡ ይሻላል ፤ አትዳፈሪው ፤ አጕራ ፡ ዘለል ፡ አትሁኚ ።

130 አይገርማችሁም ፡ ወይ ፡ የዚያች ፡ የልጅ ፡ ነገር ፤
—እኔን ፡ አንከር ፡ ትታ ፡ እሷ ፡ ጐንደር ፡ ማደር ።

ሠ ፡ እኔን ፡ «አንከር» ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ጥላ ፡ ብቻዬን ፡ ትታ ፡ እሷ ፡ ጐንደር ፡ ማደሯ ፡ አይገርማችሁምን ።

ወ ፡ እኔን ፡ አንገላታ ፡ አንከራታ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ስታዋትተኝ ፡ ኖራ ፡ ጐንደር ፡ ሄዳ ፡ ተቀመጠች ፤ ድካሜ ፡ ሁሉ ፡ ገደል ፡ ገባ ፤ ያለዋጋ ፡ ቀረ ።

131 አገሩን ፡ አለመድሽ ፡ ያለሽ ፡ በንግድነት ፤
—ምነው ፡ ቢቀርብሽ ፡ ወጣ ፡ ወጣ ፡ ማለት ።

ሠ ፡ አገሩን ፡ ሳትለምጂው ፡ ሰው ፡ ሳታውቂ ፡ ለምን ፡ ብቅ ፡ ብቅ ፡ ትያ ለሽ ፤ ምነው ፡ ዐርፈሽ ፡ እቤትሽ ፡ ብትቀመጪ ፡ ቢያስችልሽ ፡ ደግ ፡ ነበር ።

ወ ፡ አለሁ ፡ አለሁ ፡ ደረስኩ ፡ ደረስኩ ፡ እታይ ፡ እታይ ፡ ማለቱ ፡ ይቅር
ብሽ ፤ ጭምት ፡ ደርባባ ፡ ሁኚ ።

132 አገሩ ፡ ደጋ ፡ ነው ፡ አያበቅልም ፡ ገብስ ፤
—እሷ ፡ በሶ ፡ አትበላ ፡ እሱም ፡ በሶ ፡ አይቀምስ ።

ሠ ፡ ሁለቱም ፡ በሶ ፡ አይመገቡም ፤ አሸር ፡ ባሸር ፡ የሆነ ፡ ምግብ ፡ አይበ
ሉም ።

ወ ፡ ሁለቱም ፡ ሕገ ፡ እግዚአብሔርን ፡ የሚጠብቁ ፡ ናቸው ፤ እሷ ፡ በሱ ፡
ላይ ፡ እሱም ፡ በሷ ፡ ላይ ፡ አይሄዱም ።

133 አጐንብሼ ፡ መሄድ ፡ አላውቅ ፡ ብዬ ፡ እንደ ፡ ሰው ፤
—እቀና ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ ቤቴ ፡ የፈረሰው ።

ሠ ፡ ጐንበስ ፡ ብዬ ፡ እንደ ፡ መሄድ ፡ ቀጥ ፡ ብዬ ፡ ሰገግ ፡ ሰገግ ፡ ስል ፡ የ
ቤቴን ፡ ጣራ ፡ አፈረስሁት ።

ወ ፡ ቤቴን ፡ ትዳሬን ፡ የፈታሁት ፡ በቅናት ፡ ነው ፤ መታገሥ ፡ አቅቶኝ
ነገር ፡ አላሳልፍ ፡ አላስችል ፡ ብሎኝ ፡ ነው ።

134 አጥር ፡ አልታጠረ ፡ አልጠፋ ፡ መንገድ ፤
—ምን ፡ ያደርግልሻል ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ መሄድ ።

ሠ ፡ መንገድ ፡ እያለ ፡ መተላለፊያ ፡ ሳይጠፋ ፡ ለምን ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ እየተ
ራመድሽ ፡ ትሄጃለሽ ።

ወ ፡ አንድ ፡ ይበቃሻል ፤ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ አታማርጪ ፤ በባልሽ ፡ ላይ ፡
አትሂጂ ፡ ባንድ ፡ ወንድ ፡ ርጊ ።

135 አፈኛ ፡ ይሏታል ፡ ባላወቁት ፡ ነገር ፤
—ውልውሉን ፡ ይዛ ፡ ነው ፡ እሷ ፡ እምትናገር ።

ሠ ፡ ሰው ፡ ግራ ፡ ያገባታል ፡ እንጂ ፡ እሷ ፡ የምትናገረው ፡ ሥር ፡ መሠረ
ቱን ፡ ውሉን ፡ ይዛ ፡ ነው ።

ወ ፡ እሷ ፡ እንዲህ ፡ የልብ ፡ ልብ ፡ የበቃት ፡ የተወለወለውን ፡ መልከ ፡
መልካሙን ፡ ይዛ ፡ ነው ።

136 አፏ ፡ ሳይናገር ፡ ሳይኖራት ፡ ክፋት ፡
—እረ ፡ ስለ ፡ ምን ፡ ነው ፡ ሰው ፡ አማሽ ፡ ያሏት ።

ሠ ፡ ከአንደበቷ ፡ ክፉና ፡ በጎ ፡ ሳይወጣት ፡ ለምንድነው ፡ ሰው ፡ ሐሜ
ተኛ ፡ የሚያደርጋት ፤ በሆነ ፡ ባልሆነ ፡ የሚወቅሣት ።
ወ ፡ ትንሽ ፡ ትልቁ ፡ በጥባጭ ፡ ነሽ ፡ ሰው ፡ ታምሻለሽ ፡ ይሉሻል ።

137 እንጀራና ፡ ወጡ ፡ መች ፡ ይበላልኛል ፤
—እንደ ፡ ሦስት ፡ ዓመት ፡ ልጅ ፡ ጡት ፡ ጡት ፡ ያሰኘኛል ።

(ቀኛ ፡ ም) ፡

ሠ ፡ እንጀራው ፡ ወጡ ፡ እፊቴ ፡ እያለ ፡ እንደ ፡ ልጅነቴ ፡ ጡት ፡ ያምረ
ኛል ።

ወ ፡ የያዘኝ ፡ አባዜ ፡ ጡታም ፡ ሴት ፡ ያስመለክተኛል ።

138 እመጣለሁ ፡ ብሎ ፡ ሰው ፡ እንዴት ፡ ይዋሻል ፤
—ማበል ፡ እንኳን ፡ አንቺን ፡ ምድር ፡ ያበላሻል ።

ሠ ፡ ማዕበል ፡ ስንኳን ፡ አንችን ፡ ምድርን ፡ እየጠራረገ ፡ ይወስዳል ፤ ከመሬት ፡ ፊት ፡ ዐፈሩን ፡ እያጋፈፈ ፡ ወደ ፡ ባሕር ፡ ያገባዋል ።

ወ ፡ ዋሾ ፡ ቃል ፡ አባይ ፡ መሆን ፡ ስንኳን ፡ አንችን ፡ ሌላውንም ፡ ሁሉ ፡ ከትልቅ ፡ ጕዳት ፡ ያደርሳል ፤ በውሸት ፡ በዕብለት ፡ ብዙ ፡ ዐደል ፡ ይሠራል ፡ የምድር ፡ ዳር ፡ ድንበር ፡ እንኳን ፡ ይገፋል ፡ ወሰን ፡ ይበላሻል ። ቅሌት ፡ ውርደትንም ፡ ያመጣል

139 እረኛው ፡ ነህ ፡ አሉ ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ ለዚያ ፡ ሰው ፤
—ባልመጣ ፡ በቀረ ፡ ብታገኝ ፡ መልሰው ።

ሠ ፡ ዛሬ ፡ ባይመጣ ፡ እቤቱ ፡ ቢውል ፡ ይሻላል ፤ ሲመጣ ፡ እመንገድ ፡ ያገኘኸው ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መልሰህ ፡ ይዘኸው ፡ ሂድ ።

ወ ፡ አቶ ፡ ባል ፡ መጥቷል ፤ ዛሬ ፡ ወዳጄ ፡ እንዳይመጣ ፡ አንተ ፡ ሰው ፡ እባክህ ፡ ንገረው ፤ ሲመጣ ፡ ብታገኘውም ፡ መልሰው ።

140 እራሱን ፡ (ራሱን) ፡ የቻለ ፡ ከፊደሉ ፡ ማነው ፤
—ከጠየቅከኝማ ፡ እኔ ፡ እማውቀው ፡ «ና» ፡ ነው ።

ሠ ፡ እኔ ፡ እንደማውቀው ፡ ከፊደል ፡ ዘር ፡ ራሱን ፡ የቻለ ፡ ና ፡ የሚባለውን ፡ ብቻ ፡ ነው ።

ወ ፡ እኔን ፡ ከለመንኸኝ ፡ መግደርደር ፡ መሽኰርመም ፡ አላውቅም ፤ የምለው ፡ ዕሺ ፡ ይሁን ፡ ና ፡ ነው ።

141 እስቲ ፡ ልነሣና ፡ ልክፈተው ፡ በሬን ፤
—አምጥቶልኝ ፡ እንደሁ ፡ ይህ ፡ አሽከር ፡ ብሬን ።

ሠ ፡ ያ ፡ ብላቴና ፡ ገንዘቤን ፡ ብሬን ፡ ይዞ ፡ መጥቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እስቲ ፡ ልነሣ ፡ በሩን ፡ ከፍቼ ፡ ልየው ።

ወ ፡ አሽከሬ ፡ ወዳጄ ፡ «ብሬን» ፡ ይዞልኝ ፡ መጥቶ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እስቲ ፡ መዝጊያውን ፡ ከፍቼ ፡ ላስገባው ።

142 እስቲ ፡ ዝምድናህን ፡ ቈጥረህ ፡ ንገረኝ ፤
—ከወንድም ፡ አንተ ፡ ነህ ፡ ትዝ ፡ የምትለኝ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 196) ፡

ሠ ፡ ከወንድሞቼ ፡ ሁሉ ፡ የምትናፍቀኝ ፡ አንተ ፡ ነህ ፤ ያንተ ፡ ነገር ፡ ይጸናብኛል ።

ወ ፡ ከወንዶች ፡ ሁሉ ፤ ሱሪ ፡ ካጠለቁት ፡ ከልቤ ፡ የማትጠፋው ፡ አንተ ፡ ብቻ ፡ ነህ ፤ ትዝታህ ፡ በኅሊናዬ ፡ ተሸንቅሮ ፡ ይኖራል ።

143 እስቲ ፡ ጓዳ ፡ ግቡ ፡ ያች ፡ ሌባ ፡ ገብታለች ፤
—ካላጣችው ፡ ሥጋ ፡ ልብ ፡ ይዛ ፡ ሄዳለች ።

ሠ ፡ ያች ፡ ሌባ ፤ ታናሽ ፡ ታላቅ ፡ እያለ ፡ ካላጣችው ፡ ሥጋ ፡ የበሬውን ፡ ልብ ፡ ይዛው ፡ ሄዳለች ።

ወ ፡ ያች ፡ ደመግቡ ፡ መልከ ፡ መልካም ፡ ልጅ ፡ ልቤን ፡ ማርካ ፡ ኅሊናዬን ፡ ወስዳዋለች ፤ ትዝታዋ ፡ ያነኋልለኛል ።

144 እስከ ፡ ዛሬ ፡ ድረስ ፡ መች ፡ ዐወቅሁ ፡ ዝናሽን ፤
—ገና ፡ ዛሬ ፡ ሰማሁ ፡ ሸንኰራ ፡ መሆንሽን ።

ሠ ፡ እስካሁን ፡ የት ፡ እንዳለሽ ፡ ሳላውቅ ፡ ቀርቼ ፡ ገና ፡ ዛሬ ፡ «ሸንኰራ»፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ መኖርሽን ፡ ሰማሁ ፤ አድራሻሽን ፡ ዐወቅሁት ።

ወ ፡ እጅግ ፡ ተወዳጅ ፡ ስመ ፡ ጥሩ ፡ መሆንሽን ፡ ገና ፡ ዛሬ ፡ ተረዳሁት ፤ እንደ ፡ ሸንኰራ ፡ አገዳ ፡ ፍቅርሽ ፡ ጣፋጭ ፡ ነው ።

145 እባካችሁ ፡ ሰዎች ፡ ያችን ፡ ልጅ ፡ ተቈጧት ፤
—አትጣላ ፡ ከኔ ፡ ርሷን ፡ ባላገባት ። (ዘ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ ለምን ፡ በማያገባት ፡ ነገር ፡ ከሰው ፡ ጋራ ፡ ተደርባ ፡ ጣልቃ ፡ ገብታ ፡ ከኔ ፡ ትጣላለች ፤ አምባጓሮ ፡ ታነሣለች ።

ወ ፡ ርሷ ፡ ባለባል ፡ ሆነች ፤ ትዳር ፡ ይዛለች ፤ እንግዲህ ፡ አላገኘኋትም ።

146 እባክህ ፡ ሸማኔ ፡ ሥራልኝ ፡ ብለው ፤
—ይኸን ፡ ያኽል ፡ ጥለት ፡ ጣለብኝ ፡ ምነው ።

ሠ ፡ ሸማኔው ፡ የሸማዬን ፡ ጥለት ፡ አበዛው ፤ አንቦገቦገው ፤ እንዳልሆነ ፡ አደረገው ።

ወ ፡ ፍቅር ፡ ጣለብኝ ፤ የማይቻል ፡ ትዝታ ፡ ወደቀብኝ ፤ የመውደዱ ፡ ሁናቴ ፡ እንዴት ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ መላ ፡ ቅጡ ፡ ጠፋኝ ።

147 እባክህ ፡ አሞራ ፡ ሂድ ፡ ተላከኝና ፤
ብታገኝም ፡ ይዘህ ፡ ብታጣም ፡ ቶሎ ፡ ና ፤
—«ዋ» ፡ ብሎ ፡ መሚለስ ፡ ባንተ ፡ ያምራልና ።

ሠ ፡ ጅባት ፡ ብሎ ፡ ቍርጡን ፡ ዐውቆ ፡ መመለሱ ፡ ባንተ ፡ ያምራል ፤ ጸጸቱን ፡ «ዋ» ፡ ብሎ ፡ ማዘኑን ፡ ታውቅበታለህ ።

ወ ፡ «ዋ» ፡ ብሎ ፡ ተገርሞ ፡ ተደንቆ ፡ መመለስ ፡ ባንተ ፡ ያምራል ።

148 እተከለከለው ፡ እጨፌ ፡ እየዋለች ፡
—አልታለብ ፡ ብላ ፡ ያቺስላም ፡ እንቢ ፡ አለች ።

ሠ ፡ ሣር ፡ እንደ ፡ ልቧ ፡ እያገኘች ፡ ከጨፌው ፡ እየዋለች ፡ ላሟ ፡ ወተት ፡ አልሰጥም ፡ አለች ፤ ነጠፈች ።

ወ ፡ ያች ፡ የእስላም ፡ ሴት ፡ አልለመንም ፡ አለች ፤ አሻፈረኝ ፡ አለች ።

149 እቴ ፡ የናቴ ፡ ልጅ ፡ ራሴን ፡ መታኝ ፤
—ካሳዬን ፡ አልተውም ፡ እበላለሁኝ ።

ሠ ፡ የእናቴም ፡ ልጅ ፡ ቢሆን ፡ ፈንክቶኝ ፡ እንዲሁ ፡ አለቀውም ፤ እካስዋለሁ ።

ወ ፡ ምንም ፡ ቢሆን ፡ «ከካሳ» ፡ ጋራ  አልለያይም ፤ እኔና ፡ እሱን ፡ የሚነጥል ፡ የለም ፤ እኔ ፡ እሱን ፡ እስከ ፡ ምን ፡ ጊዜውም ፡ አልተወውም ።

150 እናትና ፡ አባትሽ ፡ ሥጋ ፡ ነው ፡ እርማቸው ፤
—አንገሮት ፡ ትበያለሽ ፡ አንቺማ ፡ ልጃቸው ።

ሠ ፡ አባት ፡ እናትሽ ፡ ሥጋ ፡ እርማቸው ፡ ነው ፤ አንቺ ፡ ግን ፡ አንዠት ፡ ሳይቀር ፡ ትበያለሽ ።

ወ ፡ አንቺ ፡ ፍቅር ፡ ታውቂያለሽ ፤ ትዝታሽ ፡ ከሆድ ፡ አይጠፋም ፤ አን ዠት ፡ ይበላል ፤ ያብከነክናል ።

151 እናትና ፡ አባትሽ ፡ ዘመዶችሽ ፡ ሁሉ ፤
—ምነው ፡ በረገሙሽ ፡ ባነሣሽ ፡ እያሉ ።

ሠ ፡ አባት ፡ እናትሽ ፡ ያንሣሽ ፡ ብለው ፡ በረገሙሽ ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ ቆመሽ ፡ ከምትቀሪ ፡ ምነው ፡ አንዱ ፡ ጠልፎ ፡ በወሰደሽ ፡ እያሉ ፡ ዘመዶችሽ ፡ ይመኙልሻል ።

152 እኔም ፡ ለዚህ ፡ ብዬ ፡ ሥልጡን ፡ እወዳለሁ ፤
—ዛሬ ፡ ባል ፡ ነው ፡ ስትይ ፡ ምን ፡ እሻ ፡ እመጣለሁ ።

ሠ ፡ በዓል ፡ መሆኑን ፡ ሥራ ፡ የማይሠራበት ፡ ቀን ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ እያወቅሁ ፡ ሥራ ፡ አለ ፡ ብዬ ፡ አልመጣም ።

ወ ፡ ዛሬ ፡ በሠለጠነ ፡ አነጋገርሽ ፡ ባለቤቱ ፡ አለ ፡ አይመችኝም ፡ ስትዪ ፡ ምን ፡ ላደርግ ፡ እመጣለሁ ፤ የማይሆንልኝ ፡ መሆኑን ፡ እያወቅሁት ፡ ለምን ፡ በከንቱ ፡ እለፋለሁ ።

153 እኔ ፡ ሴቱ ፡ መስሎኝ ፡ ጥጡን ፡ የሚሠራ ፤
—ለካስ ፡ ያባዝታል ፡ ያሣሣል ፡ ደብተራ ።

ሠ ፡ ለካ ፡ እንደ ፡ ሴት ፡ ወንዱ ፡ ደብተራው ፡ ጥጥ ፡ ያባዝታል ፤ ያለሰል ሳል ።

ወ ፡ ለካ ፡ የደብተራ ፡ ፍቅር ፡ ጽኑ ፡ ነው ፤ ሰውነትን ፡ ያመነምናል ፤ ያከሳል ።

154 እኔስ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ ልጅ ፡ ያጠፋብሽ ፤
—ምን ፡ ያሳዝንሻል ፡ በይ ፡ አንቺው ፡ ከሆንሽ ።

ሠ ፡ አጥፊዋ ፡ አንቺው ፡ ራስሽ ፡ ከሆንሽ ፡ ምን ፡ ያስቈጭሻል ፤ ምን ፡ ያሳዝንሻል ፤ በገዛ ፡ ጥፋትሽ ፡ ምን ፡ ታረግጃለሽ ።

ወ ፡ እኔ ፡ እስከ ፡ ዛሬ ፡ እንጀራውን ፡ የሚቈርሱት ፡ ወጡን ፡ የሚጨልፉት ፡ ልጆች ፡ ይመስሉኝ ፡ ነበር ፤ ለካ ፡ በላተኛዋ ፡ አንቺው ፡ ራስሽ ፡ ኖረ ሻል ።

155 እኔስ ፡ መስሎኝ ፡ ነበር ፡ የተጐሳቈለ ፤
—ምን ፡ ጊዜ ፡ ታድሶ ፡ ይኸ ፡ ቤት ፡ ጸዳለ ።

ሠ ፡ መቼ ፡ ታደሰና ፡ ይኸ ፡ ቤት ፡ እንዲህ ፡ ጽዳት ፡ አገኘ ፤ እንዲህ ፡ አማረ ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ጸዳለ ፡ እዚህ ፡ ቤት ፡ ስላለች ፡ ደስ ፡ ይለኛል ፤ ዐሥር ፡ ጊዜ ፡ መውጣት ፡ መግባት ፡ እወዳለሁ ፤ ቤቱን ፡ ባልለየው ፡ እፈቅ ዳለሁ ።

156 እኔስ ፡ ይገርመኛል ፡ የዚህ ፡ አብነቱ ፤
—ባላልቦ ፡ ወለደች ፡ ልጃገረዲቱ ።

ሠ ፡ ዕድሜ ፡ ጉድ ፡ ያሳያል ፤ ሴትዮዋ ፡ ጌጥ ፡ ያላት ፡ የእግር ፡ አልቦ ፡ ያደረገች ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፤ ተሰምቶ ፡ ታይቶ ፡ የማይታወቅ ፡ ነገር ፡ ሆነ ። የሥነ ፡ ፍጥረት ፡ ሕግ ፡ ተፋለሰ ።

ወ ፡ ልጃገረዲቱ ፡ ሳታገባ ፡ ባል ፡ ሳይኖራት ፡ ልጅ ፡ ወለደች ፤ ዲቃላዋን ፡ ታቅፋ ፡ ቀረች ፤ ይገርማል ።

157 እኔ ፡ ባርያ ፡ ብሆን ፡ አንቺ ፡ ደበናንሣ ፤
—ያጥንታችን ፡ ነገር ፡ ይቅር ፡ አይነሣ ።

ሠ ፡ ዘር ፡ መቋጠሩ ፡ ይቅር ፤ ትውልዳችንን ፡ ሳናነሣ ፡ ገበናችን ፡ ሳይገለጥ፡ እንዲሁ ፡ በደፈናው ፡ እንጋባ ፤ ተሸፋፍነን ፡ እንኑር ።

ወ ፡ የጥንቱ ፡ ነገር ፡ አይነሣ ፤ ነበርን ፡ አታውሩ ፤ ላለፈ ፡ ክረምት ፡ ቤት ፡ አይሠራም ።

158 እኔ ፡ ተቀምጬ ፡ ከጐዳናው ፡ ላይ ፡
—ማለፊያ ፡ ስፍራውን ፡ አጥተሽው ፡ ነወይ ።

ሠ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ የምትለፊው ፡ የምትወጪው ፡ የምትወርጂው ፡ መንገዱ ፡ ጠፍቶሽ ፡ ማለፊያው ፡ ተስቶሽ ፡ ነው ፡ ወይ ።

ወ ፡ ወይዘሮ ፡ ማለፊያ ፡ እንዲህ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ የምትቅበዘበገርው ፡ የተቃጠርንበትን ፡ ስፍራ ፡ አጥተሽው ፡ ቦታውን ፡ ዘንግተሽው ፡ ነወይ ።

159 እኔንስ ፡ ለሌላ ፡ ለምን ፡ ታስማማለህ ፤
—አንተ ፡ ብቻ ፡ ግዛኝ ፡ ብዙ ፡ ዋጋ ፡ ያለህ ።

ሠ ፡ ብዙ ፡ ሀብት ፡ ያለህ ፡ ገንዘብ ፡ የተረፈህ ፡ አንተው ፡ ግዛኝ ፤ አሳልፈህ ፡ ለሌላ ፡ አትስጠኝ ።

ወ ፡ አንተ ፡ ክብርና ፡ ማዕርግ ፡ ያለህ ፡ ሰው ፡ አኑረኝ ፤ አስተዳድረኝ ።

160 እኔ ፡ እየተከተልኩ ፡ እሷ ፡ እየመራችኝ ፡
—ስማዳ ፡ ስማዳ ፡ ስማዳ ፡ አገባችኝ ።

ሠ ፡ እሷ ፡ ፊት ፡ ፊት ፡ ስትሄድ ፡ እኔ ፡ እኋላ ፡ እኋላዋ ፡ ስከተል ፡ «ስማዳ»፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ ይዛኝ ፡ ገባች ።

ወ ፡ ወደድኩህ ፡ እያለች ፡ እየሳሳመች ፡ ከዕዳ ፡ አገባችኝ ፤ ፍቅሯ ፡ የማይለቀኝ ፡ ሆነ ።

161 እኔ ፡ ወፍራም ፡ኩታ ፡ ለብሻለሁ ፡ ብዬ ፤
እኔ ፡ ወፍራም ፡ ጃኖ ፡ ለብሻለሁ ፡ ብዬ ፤
—በዚህም ፡ በዚህም ፡ አከላቴ ፡ ታ(የ)ዬ ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ልብስ ፡ ለብሻለሁ ፡ ብዬ ፡ ስዝናና ፡ ለካ ፡ መላ ፡ ሰውነቴ ፡ በያለበት ፡ ይታያል ፤ የተሸፈነ ፡ አካል ፡ የለኝም ፤ ዕራቍቴን ፡ ዕርቃን ፡ ሥጋዬን ፡ ነኝ ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ አካሌ ፡ ታየ ፡ በዚያም ፡ በዚህም ፡ በየሄድኩበት ፡ ሁሉ ፡ ይገጥመኛል ።

162 እኔ ፡ ዐይኔን ፡ አሞኛል ፡ ወይ ፡ አልሞት ፡ አልድን ፤
—እሷንም ፡ ጥሎባት ፡ እንደኔው ፡ ትሁን ።

ሠ ፡ የኔን ፡ ሕመም ፡ ይስጣት ፤ እሷንም ፡ ዐይኗ ፡ ላይ ፡ ይጣልባት ፤ ብርሃ
ኗን ፡ ይከልላት ።

ወ ፡ እሷም ፡ ፍቅር ፡ ደርሶባት ፡ እንደኔው ፡ ትሁን ፤ ትዝታን ፡ ጥሎባት ፡
ትንዠዋለል ።

163 እኔ ፡ የልጅዋ ፡ ልጅ ፡ እሷ ፡ የናቴ ፡ እናት ፤
—አኳኋኗ ፡ ሁሉ ፡ እንዳያት ፡ እንዳያት ። (ክ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ አዘኔታዋና ፡ ሁኔታዋ ፡ አሳቧ ፡ ሁሉ ፡ አያት ፡ እንደሚያደርገው ፡
ያለ ፡ ነው ፤ ውለታዋ ፡ ፍቅሯ ፡ ካያት ፡ የሚወዳደር ፡ ነው ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ የምትሆነው ፡ እኔ ፡ እንድመለከታት ፡ ነው ፤ ይህ ፡ አድራ
ጎት ፡ እኔን ፡ ለመሳብና ፡ ከኔ ፡ ለመጋባት ፡ በፍቅሯ ፡ ለማሰር ፡
ነው ።

164 እንካ ፡ ብላ ፡ አለችኝ ፡ ደረቁን ፡ እንጀራ ፤
—እሷ ፡ በነካካው ፡ በራሰው ፡ ልትበላ ።

ሠ ፡ እሷ ፡ መረቅ ፡ (ወጥ) ፡ ያለበትን ፡ የራሰውን ፡ ልትበላ ፡ ለኔ ፡ ደረ
ቁን ፡ እንጀራ ፡ ሰጠችኝ ፤ ያለመባያ ፡ አቀረበችልኝ ።

ወ ፡ እሷ ፡ ራስ ፡ በራ ፡ ሰው ፡ ወዳ ፡ መሄዷ ፡ ነው ፤ እኔን ፡ ባዶ ፡ ልታስቀ
ረኝ ፡ ነው ።

165 እንደ ፡ ምን ፡ አድርገሽ ፡ ትራመጃለሽ ፤
—የኛን ፡ አገር ፡ አልፈሽ ፡ ሳላይሽ ፡ ያደርሽ ።

ሠ ፡ የኛን ፡ አገር ፡ ዘለሽ ፡ ከመቼው ፡ «ሳላይሽ» ፡ ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ደረ
ስሽና ፡ አደርሽ ፤ መንገዱ ፡ እንዴት ፡ አፈጠነሽ ።

ወ ፡ ሳላይሽ ፡ ያደርኩት ፡ ሳላገኝሽ ፡ የቀረሁት ፡ የት ፡ ሄደሽ ፡ ነው ።

166 እንዳንች ፡ ያታለለኝ ፡ ያሞኘኝ ፡ ሰው ፡ ጠፋ ፤
—እንቢ ፡ አለ ፡ ሚዛኑ ፡ ወዳንች ፡ እየደፋ ።

ሠ ፡ እጅግ ፡ አታለልሽኝ ፤ በገበያ ፡ ዋጋ ፡ ጐዳሽኝ ፤ ሚዛኑ ፡ ወዳ[illegible] ፡
ያመዝናል ፤ ያጋድላል ።

ወ ፡ ያንቺ ፡ ነገር ፡ አልሆነልኝም ፤ ማንኛውም ፡ ፍቅርሽ ፡ ሁሉ ፡ [illegible] ፡
ሆነብኝ ፡ ትዝታሽ ፡ ከሁሉ ፡ ያመዝናል ።

167 እንግዲህ ፡ ጣይ ፡ በጣይ ፡ ከሆነ ፡ መንገዶ ፡
—እረ ፡ ጥላ ፡ ጥላ ፡ ቍረጥልኝ ፡ ሆዶ ።

ሠ ፡ ወዳጄ ፡ ሆዴ ፡ ከዋዕየ ፡ ፀሐይ ፡ የምከለልበት ፡ ጥላ ፡ ቍረጥልኝ ፡ የ
ዛፍ ፡ ቅጠል ፡ ቀጥፈህ ፡ አምጣልኝ ።

ወ ፡ ልቤ ፡ ሰው ፡ መውደድክን ፡ ርሳው ፤ ተስፋ ፡ ቍረጥ ፤ የሚጠጎህን ፡
ጥላው ።

168 እ(ዕ)ንጩቱን ፡ ለቃቅመን ፡ ታላቀረብንላት ፡
—ቤቱን ፡ አፈራርሳ ፡ የምታነደው ፡ ናት ።

ሠ ፡ ልጅቷ ፡ ደንታ ፡ የላትም ፤ የማገዶ ፡ ዕንጨት ፡ ካላገኘች ፡ ጣራውን ፡ እየመዘዘች ፡ ግድግዳውን ፡ እያፈረሰች ፡ መማገዷ ፡ አይቀርም ።

ወ ፡ ይህቺ ፡ ልጅ ፡ የባሏን ፡ ትዳሩን ፡ ንብረቱን ፡ አፈራርሳ ፡ ባለቤቷን ፡ ከብስጭትና ፡ ከንዴት ፡ ሳትጥለው ፡ የማትቀር ፡ ናት ፤ አያያዟና ፡ ሁኔታዋ ፡ ያስፈራል ።

169 እንጫወት ፡ ይላል ፡ ሥራ ፡ ፈት ፡ ሰው ፤
—እኔ ፡ ባል ፡ ደርሶብኝ ፡ ተጨንቄ ፡ ነው ።

ሠ ፡ መደዳውን ፡ ተከታትሎ ፡ በዓል ፡ ብቻ ፡ ሆኖብኝ ፡ የሥራ ፡ ቀን ፡ አጥቼ ፡ ተጨንቄያለሁ ፡ የሥራ ፡ ውዝፍ ፡ በዝቶብኛል ።

ወ ፡ ስቀብጥ ፡ ባለቤቴ ፡ ደርሶብኝ ፡ ዕጤ ፡ ዱብ ፡ ብሏል ፤ ግራ ፡ ገብቶኛል።

170 እንፍሌው ፡ ለምኔ ፡ መረቁ ፡ ለምኔ ፤
—ለምለም ፡ አንድ ፡ እንጀራ ፡ ትበቃለች ፡ ለኔ ።

ሠ ፡ ግፍልፍሉ ፡ መረቁ ፡ ለማነው ፤ ለኔ ፡ እንደሆን ፡ አንዲት ፡ ደረቅ ፡ ለስላሳ ፡ እንጀራ ፡ ትበቃኛለች ፤ ለሆዴ ፡ እምብዛም ፡ ይህን ፡ ያኽል ፡ አልጨነቅለትም ።

ወ ፡ ከወዳጄ ፡ ለምለም ፡ ወዲያ ፡ ሌላ ፡ ሴት ፡ አልፈልግም ።

171 እኛም ፡ እንወጣለን ፡ እተራራው ፡ ላይ ፤
—አንቺም ፡ በዚያው ፡ አርገሽ ፡ አመዳሚት ፡ ነይ ።

ሠ ፡ አንቺም ፡ እግረ ፡ መንገድሽን ፡ በዚያው ፡ በኩል ፡ «አመዳሚት» ፡ እስከሚባለው ፡ ቦታ ፡ ድረስ ፡ ነዪ ።

ወ ፡ አንቺ ፡ ነጫጭቢት ፡ አመዳሚት ፡ እተቃጠርንበት ፡ ቦታ ፡ ድረስ ፡ እንድትመጪ ፡ ቀጠሮውን ፡ እንድታከብሪ ።

172 እዘኑልኝ ፡ ለኔ ፡ ለምመነኵሰው ፤
—እሷስ ፡ ላሜን ፡ ይዛ ፡ ትጠጋለች ፡ ከሰው ።

ሠ ፡ እሷ ፡ ጥገት ፡ ላሜን ፡ ይዛ ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ ትጠጋለች ፤ ተዳብላ ፡ ትኖራለች ፤ በላሜ ፡ ትደገፋለች ።

ወ ፡ እሷ ፡ ምን ፡ ቸገራት ፤ እስላም ፡ ወዳጅዋን ፡ ተከትላ ፡ ወደ ፡ አንዱ ፡ አገር ፡ ትሄዳለች ።

173 እዩልኝ ፡ ስሙልኝ ፡ የኔ ፡ ዱቄት ፡ ልም ፡ ነው ፤
—ተገረዳደፈ ፡ የሚለኝ ፡ ሰው ፡ ማነው ።

ሠ ፡ ዱቄትህ ፡ አልደቀቀም ፤ ሽርክት ፡ ነው ፤ ልም ፡ አይደለም ፡ የሚለኝ ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ሰው ፡ ነው ።

ወ ፡ ከገረድ ፡ ተዋደቀ ፡ ክብሩን ፡ አዋረደ ፡ የሚለኝ ፡ ማነው ።

174 እያወቀው ፡ ሆዴ ፡ እንደ ፡ በደለችኝ ፡
---ሳማት ፡ መጣችና ፡ ምን ፡ አልኩህ ፡ አለችኝ ።

ሠ ፡ በሐሜት ፡ ስሻን ፡ ሳነሣ ፡ ደረሰችና ፡ ምን ፡ በደልኩህ ፡ ምን ፡ አደረግኩህ ፡ ስሜን ፡ ለምን ፡ ታጠፋለህ ፡ አለችኝ ።

ወ ፡ ስትጫወትና ፡ ስትሳሳም ፡ ውላ ፡ መጥታ ፡ ምን ፡ በደልኩህ ፡ አለችኝ ፣ የሠራችውን ፡ ሥራ ፡ እያወቀች ፡ ልታስተባብለኝ ፡ ፈለገች ።

175 ከሁሉ ፡ ተጣላሽ ፡ እያሙንሽ ፡ ሰባቂ ፣
—እንግዲህስ ፡ ወዲህ ፡ አንቺ ፡ ሴት ፡ ታረቂ ።

ሠ ፡ እንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ታገሽ ፣ አሉባልታ ፡ እየሰማሽ ፡ ከሰው ፡ አትጣዪ ፣ በሆነ ፡ ባልሆነው ፡ አትቀያየሚ ።

ወ ፡ ከዛሬ ፡ ዠምሮ ፡ ዐቅምሽን ፡ ዐውቀሽ ፡ እደሪ ፣ ልክ ፡ መግባት ፡ መቀጣት ፡ አለብሽ ፣ እንደ ፡ ልብ ፡ መንዘልዘሉ ፡ ይብቃሽ ።

176 ከሰው ፡ የበለጠ ፡ እበላለሁ ፡ ወይ ፣
ከሰው ፡ የበለጠ ፡ እጠጣለሁ ፡ ወይ ፣
—ቦጋለ ፡ አካላቴ ፡ አደባባይ ፡ ላይ ።

ሠ ፡ ሰውነቴ ፡ አማረበት ፣ ያባራ ፡ ዠመር ፣ ወዘናዬ ፡ ተመለሰ ፣ ደም ፡ ግባቴ ፡ ጠራ ።

ወ ፡ አካሌ ፡ ወዳጄ ፡ ቦጋለን ፡ ባደባባይ ፡ ላይ ፡ አየሁት ፣ ከሸንጎ ፡ ማኸል ፡ አገኘሁት ።

177 ከበሽታ ፡ ሁሉ ፡ ሕመም ፡ ነው ፡ ከሚሉት ፣
—ባርያ ፡ የጣለው ፡ ሰው ፡ የለውም ፡ መድኀኒት ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 103) ፡

ሠ ፡ ጋኔን ፡ የሚጥለው ፡ ሰው ፡ መዳኛ ፡ የለውም ፣ ከበሽታ ፡ ሁሉ ፡ የሚከፋ ፡ እሱ ፡ ነው ።

ወ ፡ በባርያ ፡ ፍቅር ፡ የተያዘ ፡ ሰው ፡ መቅኖ ፡ የለውም ፣ ውሎ ፡ አድሮ ፡ ውርደትና ፡ ቅሌት ፡ ሳያገኘው ፡ አይቀርም ።

178 ከበሽታ ፡ ሁሉ ፡ ፈንጣጣ ፡ ክፉ ፡ ነው ፣
—ክትባት ፡ እንዳንቺ ፡ የሚያምርበት ፡ ማነው ።

ሠ ፡ ከተከተቡ ፡ አይቀር ፡ እንዳንቺ ፡ ነው ፣ ፈንጣጣዋ ፡ በቀላሉ ፡ ወጣችልሽ ፣ በሰላም ፡ ሸልማሽ ፡ ሄደች ።

ወ ፡ ምን ፡ ቢሸፈኑ ፡ ተከተው ፡ ቢሰነብቱ ፡ እንዳንቺ ፡ የሚያምርበት ፡ የለም ፣ የባትሽ ፡ ቅርጽ ፡ ኀሊናን ፡ ይስባል ፣ ልብን ፡ ይማርካል ።

179 ከብት ፡ ጠፋት ፡ አሉ ፡ በኛ ፡ አደባባይ ፣
—እኔን ፡ መፈለጊያ ፡ ማድረጓ ፡ ነወይ ።

ሠ ፡ ከብትስ ፡ ቢጠፋት ፡ ለምንድነው ፡ በኔ ፡ ቀዬ ፡ የምትመላለሰው ፡ የኔን ፡ ደጅ ፡ የጠፋ ፡ ከብት ፡ መሰብሰቢያና ፡ ማጠያየቂያ ፡ ማድረጓ ፡ ነውን ።

ወ ፡ እኔን ፡ መፈለጊያ ፡ ማድረጓ ፡ ነውን ፣ ለካ ፡ አብራኝ ፡ ያለችው ፡ ለዘለቄታ ፡ አይደለም ፣ ለዕለት ፡ ነው ።

180 ከተነጋገርንስ ፡ እስኪ ፡ ልጠይቅሽ ፤
—መለመን ፡ አላውቅም ፡ እንዴት ፡ ነው ፡ እባክሽ ።

ሠ ፡ ነገሩንስ ፡ ካነሣነው ፡ እስኪ ፡ ልጠይቅሽ ፤ መለመን ፡ አፍራለሁ ፤ እንዴት ፡ እንደሚለመን ፡ አላውቅም ፤ ዘዴውን ፡ ንገሪኝ ።

ወ ፡ እንግዲህ ፡ ከተጨዋወትንና ፡ ከተነጋገርን ፡ መግባባት ፡ ከዠመርን ፡ ይቅርታ ፡ አድርጊልኝና ፡ ፈቃድሽ ፡ ይሁን ፤ ተለመኚኝ ።

181 ከንግዲህስ ፡ ወዲያ ፡ ሰው ፡ አልክባትም ፤
—እሷ ፡ ትመጣለች ፡ መቋሚያ ፡ የላትም ።

ሠ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ቤቴን ፡ ካየችው ፡ እሷ ፡ ራስዋ ፡ ትመጣለች ፤ ሰው ፡ መላክ ፡ አያሻም ፤ አመላላሽ ፡ አያስፈልግም ።

ወ ፡ እንግዲህ ፡ ሥራቱ ፡ ዘመናይነቱ ፡ ሁሉ ፡ ቀረ ፤ እግሯ ፤ ተቈረጠ ፤ አንካሳ ፡ ሆነች ።

182 ከወፍ ፡ አእላፍ ፡ አብላኝ ፡ እያለ ፡ ሲዘራ ፡
—ምን ፡ ያምር ፡ ገበሬ ፡ የኔ ፡ ባልንጀራ ።

ሠ ፡ ከሰው ፡ ሁሉ ፡ ከወፍ ፡ አእላፍ ፡ ያለውን ፡ ተካፍሎ ፡ የሚበላ ፡ የእንጀራ ፡ ጌታ ፡ የሆነው ፡ ገበሬ ፡ ደስ ፡ ያሰኘኛል ።

ወ ፡ ትዳሬ ፡ ንብረቴ ፡ ልብሴ ፡ ጕርሤ ፡ ባሌ ፡ ነው ።

183 ካንድ ፡ ለመታገል ፡ ሲያቅተው ፡ ሰው ፡ ሁሉ ፤
—አንቺ ፡ ሰው ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ትጥያለሽ ፡ አሉ ።

ሠ ፡ አንቺ ፡ ትግል ፡ ታውቂያለሽ ፤ አንዱን ፡ ባንዱ ፡ ላይ ፡ አደራርበሽ ፡ አነባብረሽ ፡ ትጥያለሽ ፡ አሉ ።

ወ ፡ አንቺ ፡ ካንድ ፡ ሰው ፡ አትረጊም ፤ በያዝሽው ፡ ሰው ፡ ላይ ፡ ትሄጃለሽ ፡ ቅብጠት ፡ ታበዣለሽ ።

184 ኮሶ ፡ መለሰባት ፡ ቢሉን ፡ ስናዝን ፡
—አሁን ፡ ግን ፡ ብንሰማ ፡ አዳናት ፡ አሉን ።

ሠ ፡ መላልሶ ፡ ታይቷት ፡ ነበር ፤ አሁን ፡ ግን ፡ የጠጣችው ፡ ኮሶ ፡ አድኗታል ፤ መድኀኒቱ ፡ ቀንቷታል ፤ ፈውሷታል ።

ወ ፡ ያለችበት ፡ ጠፍቶን ፡ ስናዝን ፡ ስንጨነቅ ፡ አሁን ፡ «አዳ» ፡ ከሚባል ፡ አገር ፡ ናት ፡ ብለው ፡ ነገሩን ።

185 ወረደ ፡ ይሉኛል ፡ መተማ ፡ ነጋዴ ፤
—ቀረጡት ፡ እያሉኝ ፡ ምር ፡ አዘነ ፡ ሆዴ ። (ቀኛ ፡ ም) ፡ (ዘፈ ፡ ( 222 ፡ 224 ፡ 242 ) ፡ ፡

ሠ ፡ የመተማን ፡ ነጋዴ ፡ ቀረጥ ፡ አስከፈሉት ፡ ቢሉኝ ፡ ሆዴ ፡ እጅግ ፡ አዝኗል ።

ወ ፡ አጕጠጕጤዋ ፡ ያልወደቀ ፡ ጡታም ፡ ሴት ፡ ባለማግኘቴ ፡ እጅግ ፡ አዘንኩ ።

186 ወሮ ፡ በላው ፡ በዛ ፡ በየወንዛወንዙ ፤
—እኔ ፡ ብቻዬን ፡ ነኝ ፡ ልጠጋ ፡ ከብዙ ።

ሠ ፡ ብቻዬን ፡ ከምሆን ፡ ሰው ፡ ከበዛበት ፡ ሕዝብ ፡ ከተሰበሰበበት ፡ ሄጄ ፡ ከወገን ፡ ልደባለቅ ።

ወ ፡ ብቻዬን ፡ ከምቀመጥ ፡ ከወዳጄ ፡ ከብዙ ፡ ጋራ ፡ ልዳበል ፤ የሷ ፡ ጥገኛ ፡ ሆኜ ፡ ልኑር ።

187 ወይ ፡ መካሪ ፡ የለው ፡ ጎረ ፡ ቤት ፡ ከደጅ ፤
—ያለማታ ፡ አይመጣም ፡ ይህ ፡ የኔ ፡ ወዳጅ ።

ሠ ፡ ወዳጄ ፡ በጊዜ ፡ አይገባም ፤ ካልመሸ ፡ ካልጨለመ ፡ ቤቱን ፡ አያስታውሰውም ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ ጠብ ፡ ጠብ ፡ ይለዋል ፤ ቄጣ ፡ ቄጣ ፡ ማለት ፡ ይቀናዋል ፤ አምባጓሮ ፡ ማንሣት ፡ ይወዳል ።

188 ወይፈኑ ፡ ቢታመም ፡ ጊደሯም ፡ ታመመች ፤
—እረ ፡ ለመሆኑ ፡ ያችስላም ፡ እንዴት ፡ ነች ።

ሠ ፡ ላሻ ፡ እንደ ፡ ምን ፡ ነች ፤ አልከሳችም ፡ ወይ ፤ የምትበላው ፡ የግጦሽ ፡ ሣር ፡ ይገኛል ፡ ወይ ።

ወ ፡ እስላሻ ፡ ወዳጄ ፡ ደኅና ፡ ነች ፡ ወይ ፤ ያለችው ፡ እዚያው ፡ እቦታዋ ፡ ነወይ ።

189 ወጣ ፡ ወጣ ፡ ስትል ፡ ክፉ ፡ ምች ፡ መቷት ፡
—ተቸግሪያለሁኝ ፡ ያችን ፡ ልጅ ፡ አሻት ። (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 6) ፡

ሠ ፡ ያች ፡ ልጅ ፡ ምች ፡ መቷት ፡ ታማብኛለች ፤ ያተኵሳታል ፤ ያቃዣታል ።

ወ ፡ ባልሠራችው ፡ ሥራ ፡ በማታውቀው ፡ ነገር ፡ ያችን ፡ ልጅ ፡ ያሻታል ፤ ይቦጭቃታል ፤ ጥሬ ፡ ሥጋዋን ፡ ይበሏታል ።

190 ውሃ ፡ ውሃ ፡ ይላል ፡ ጠጅ ፡ እያተኰሰው ፤
—አሁን ፡ ምን ፡ ያሻዋል ፡ ከጠላ ፡ ወዲያ ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ከጠላ ፡ ወዲያ ፡ ሌላ ፡ መጠጥ ፡ ምን ፡ ያስፈልጋል ፤ ሁሉን ፡ ዐይነት ፡ ቢጠጡ ፡ ከማስከር ፡ በቀር ፡ ምን ፡ ይጠቅማል ፤ ትርፉ ፡ ውርደት ፡ ነው ።

ወ ፡ ሰው ፡ ከተጠላና ፡ ቅርታ ፡ ከገባው ፡ ወዲያ ፡ ለምን ፡ በግብዝነት ፡ ይነጋገራል ፤ ካንገት ፡ በላይ ፡ ሲሆን ፡ ለሰው ፡ ይምሰል ፡ ለምን ፡ ይፋቀራል ።

191 ዋርዳና ፡ ግራጫ ፡ ዕቃዋ ፡ ደማቅ ፤
—እንዳንች ፡ ያለ ፡ በቅሎ ፡ አይቼም ፡ አላውቅ ።

ሠ ፡ ዕቃዋ ፡ የደመቀባት ፡ እንደዚች ፡ ያለ ፡ ሠጋር ፡ በቅሎ ፡ እኔ ፡ አይቼ ፡ አላውቅም ፤ መልካም ፡ ናት ፤ አትገኝም ።

ወ ፡ እንዳንች ፡ ያለ ፡ በውበትና ፡ በደምግባት ፡ ያሸበረቀች ፡ ሴት ፡ አልተወለደችም ፤ እጅግ ፡ ቈንጆ ፡ ነሽ ።

192 ወፍ ፡ እጠብቃለሁ ፡ ወጥቼ ፡ ከማማ ፤
—እንደኔ ፡ ማን ፡ አለ ፡ ሳይበላ ፡ የታማ ።

ሠ ፡ ከሸቱ ፡ ሳልበላ ፡ በከንቱ ፡ እንደኔ ፡ የታማ ፡ ማን ፡ አለ ።

ወ ፡ ከሰው ፡ ሴት ፡ ሳልደርስ ፡ በከንቱ ፡ የታማ ፡ የተጠረጠረ ፡ እንደኔ ፡ ማን ፡ አለ ።

193 ዕቃ ፡ ከመንገድ ፡ ላይ ፡ ለምን ፡ አኖራችሁ ፤
—ወጣ ፡ ወጣ ፡ ስትል ፡ ሰበረችላችሁ ።

ሠ ፡ ወጥ ፡ አወጣለሁ ፡ አሳልፋለሁ ፡ ብላ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ ስትመላለስ ፡ ዕቃውን ፡ ሰበረችው ፤ አደቀቀችው ።

ወ ፡ አላርፍ ፡ ብላ ፡ ስትወጣ ፡ ስትገባ ፡ ስትቅነዘነዝ ፡ ዕቃውን ፡ ፈጀችው ።

194 ዘማለች ፡ እያልን ፡ ምክር ፡ እየናቁ ፡
—ምን ፡ ይጠቀማሉ ፡ እየገቡ ፡ ቢያልቁ ። (አ ፡ በ) ፡ (ዘለ ፡ ቍ ፡ 105) ፡

ሠ ፡ ቤቷ ፡ መዝመሻን ፡ እየነገርናቸው ፡ ምክራችንን ፡ በመናቅና ፡ በማቃለል ፡ እየገቡ ፡ ጕዳት ፡ ቢደርስባቸው ፡ ምን ፡ ይጠቀማሉ ።

ወ ፡ ሴትዮዋ ፡ አመንዝራ ፡ መሆኗን ፡ እያወቁ ፡ ለምን ፡ ርስ ፡ በርሳቸው ፡ ይጣላሉ ፤ በማይረባ ፡ ነገር ፡ ይጋጫሉ ።

195 ዘግቼ ፡ ቈልፌ ፡ የተውኩትን ፡ እልፍኝ ፡
—ከፍተሽ ፡ መቈየትሽ ፡ በጣም ፡ አሳዘነኝ ።

ሠ ፡ የዘጋሁትን ፡ በር ፡ ከፍተሽ ፡ እንዳልሆነ ፡ አድርገሽ ፡ ቤቴን ፡ ለሌባ ፡ ሰጥተሽ ፡ መቈየትሽ ፡ እጅግ ፡ አሳዘነኝ ።

ወ ፡ ባሕሪሽ ፡ ተለዋውጦ ፡ የዱሮው ፡ መልካሙ ፡ ዐመልሽ ፡ ተቀያይሮ ፡ ክፉ ፡ ሆነሽ ፡ ስላገኘሁሽ ፡ ሐዘን ፡ ተሰማኝ ፤ የሰው ፡ ተፈጥሮ ፡ አስደነቀኝ ።

196 ዝምድናችን ፡ እንኳ ፡ በወግ ፡ አልታወቀ ፤
—እቴነሽ ፡ እያሉ ፡ አካላቴ ፡ አለቀ ። (ዘለ ፡ ቍ ፡ 142) ፡

ሠ ፡ ትውልድ ፡ ሳንቋጠር ፡ ዝምድናችን ፡ ሳይረጋገጥ ፡ እኅትሽ ፡ ናት ፡ እያሉኝ ፡ ሰውነቴ ፡ ባየሁሽ ፡ ቍጥር ፡ ይደነግጣል ፤ በጣም ፡ አዝንልሻለሁ ።

ወ ፡ አንቺን ፡ ወዳጄን ፡ እቴነሽ ፡ ብለው ፡ በተጣሩ ፡ ቍጥር ፡ ልቤ ፡ ትር ፡ ትር ፡ ይላል ፤ ጎሊናዬ ፡ ይሸበራል ።

197 የኅቴንስ ፡ ወሬ ፡ ሰማሁ ፡ ትላንት ፡ ማታ ፤
—እስላም ፡ አገር ፡ ቀረች ፡ አሉኝ ፡ ተነካክታ ።

ሠ ፡ እኅቴ ፡ እስላም ፡ አገር ፡ ሄዳ ፡ ገደል ፡ ገብታ ፡ ተሰብራለች ፡ ተንከታክታለች ፡ አሉኝ ።

ወ ፡ የኅቴን ፡ ሁኔታ ፡ ሰማሁ ፤ ከስላም ፡ ጋራ ፡ ተገናኝታ ፡ ዐንጕል ፡ ሆናለች ፡ አሉኝ ።

198 የለም ፡ ዛሬ ፡ አልቻልኩም ፡ እኔ ፡ አንተን ፡ ልረዳ ፤
—ተቸግሪያለሁኝ ፡ መጥቶብኝ ፡ እንግዳ ።

ሠ ፡ ዛሬ ፡ እኔ ፡ ለራሴ ፡ ትልቅ ፡ እንግዳ ፡ መጥቶብኝ ፡ የማደርገው ፡ ጠፍቶ ኛል ፤ ምንን ፡ ከምን ፡ አድርጌ ፡ እንደማስተናግደው ፡ አላውቅም ።

ወ ፡ የጥንት ፡ ወዳጄ ፡ እንግዳ ፡ መጥቶብኛልና ፤ ዛሬ ፡ አንተን ፡ ለማጫ ወት ፡ አልቻልኩም ፤ አትምጣ ።

199 የለችም ፡ ብትሉኝ ፡ ሙች ፡ አምናችኋለሁ ፤
—አሁን ፡ በቀደምለት ፡ ባይኔ ፡ አይቻታለሁ ።

ሠ ፡ በዚህ ፡ ሰሞን ፡ አግኝቻታለሁ ፤ በቅርብ ፡ ጊዜ ፡ አይቻታለሁ ።

ወ ፡ ዐይኔ ፡ ከሚባል ፡ አገር ፡ ትኖራለች ፤ እዚያ ፡ አይቻታለሁ ።

200 የማታውቂበትን ፡ አጠባ ፡ ወርደሽ ፡
—ጐንደር ፡ ተደነቀ ፡ ባጠማዘዝሽ ።

ሠ ፡ ልብስ ፡ አስተጣጠብሽና ፡ አጠማዘዝሽ ፡ ሕዝቡን ፡ አስደነቀው ፤ ጐን ደርን ፡ አስገረመው ።

ወ ፡ ሜረኛ ፡ መሆንሽና ፡ ነገር ፡ ማዞርሽ ፡ ሕዝቡን ፡ አስገረመው ።

201 የሰው ፡ ሁሉ ፡ ሸማ ፡ በሦስት ፡ ባራት ፡ መቶ ፤
—እኔን ፡ የገደለኝ ፡ ሺበሺ ፡ ተሠርቶ ።

ሠ ፡ የሰው ፡ ልብስ ፡ በ፫ ፡ ባ፬ ፡ መቶ ፡ ጥንድ ፡ ሲሠራ ፡ የኔ ፡ በሺ ፡ ጥንድ ፡ ተሠርቶ ፡ እጅግ ፡ በዛብኝ ፤ ክብደቱ ፡ ሊገድለኝ ፡ ነው ።

ወ ፡ እኔን ፡ የበደለኝና ፡ የጐዳኝ ፡ የሺበሺ ፡ ፍቅር ፡ ነው ።

203 የሰው ፡ መሬት ፡ አራሽ ፡ ገበሬ ፡ ነህ ፡ ኰሩ ፤
—ዎ ፡ ብለህ ፡ ተመለስ ፡ ይኸ ፡ ነው ፡ ድንበሩ ።

ሠ ፡ የፈሩ ፡ መዳረሻ ፡ ድንበሩ ፡ ይኸ ፡ ነው ፤ በሬህን ፡ እዚህ ፡ አድርስና ፡ መልሰው ።

ወ ፡ ባሌ ፡ ድንበሩ ፡ ይሉሃል ፡ ይህ ፡ ነው ፤ ጅባት ፡ ብለህ ፡ ተስፋ ፡ ቈር ጣህ ፡ ተመለስ ።

204 የሸንብራ ፡ እሸቱን ፡ የበላው ፡ ሌላ ፡ ነው ፤
—እኛ ፡ የታማነው ፡ በጥርጣሪው ፡ ነው ።

ሠ ፡ እሸቱን ፡ ሳንበላ ፡ እኛ ፡ የታማነው ፡ ፍልፋዩ ፡ ጥርጣሪው ፡ አጠገባ ችን ፡ ስለ ፡ ተገኘ ፡ ነው ።

ወ ፡ እኛ ፡ የተወቀሥነው ፡ በሰው ፡ አፍ ፡ የታማነው ፡ ባላደረግነው ፡ ባልሠ ራነው ፡ ሥራ ፡ ተጠርጥረን ፡ ነው ።

205 የሸቶ ፡ ፋብሪካ ፡ መኪናው ፡ የት ፡ ነው ፤
—እንዲህ ፡ ሁነሽ ፡ አንቺ ፡ የተቀባሽው ።

ሠ ፡ አንቺ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ጥሩ ፡ ሽቶ ፡ ያለልክ ፡ የተቀባሽው ፡ ፋብሪካው ፡ የት ፡ ቢሆን ፡ ነው ፤ ባቅራቢያሽ ፡ ነውን ።

ወ ፡ አንቺ ፡ እጅግ ፡ ያማርሽ ፡ ውበትን ፡ የተመላሽ ፡ ነሽ ፤ ቍንጅናሽ ፡ ደም ፡ ግባትሽ ፡ ከሁሉ ፡ የላቀ ፡ ነው ።

206 የተጣደ ፡ ምጣድ ፡ ከኋላዬ ፡ ኖሮ ፡
—ለካስ ፡ ጥላት ፡ ብቻ ፡ ሆኛለሁ ፡ ዘንድሮ ።

ሠ ፡ ለካ ፡ ልብሴ ፡ በምጣድ ፡ ጥላት ፡ ተለውሷል ፤ እድፍ ፡ ብቻ ፡ ሆኗል ።

ወ ፡ ዘንድሮ ፡ ለካስ ፡ ብዙ ፡ ጠላት ፡ ኖሮኛል ፤ በቤቴ ፡ ንዝንዝና ፡ አምባ ጓሮ ፡ ሞልቶበታል ።

207 የዚህ ፡ ዓለም ፡ ኑሮ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አይሞላ ፤
—ባሌን ፡ እያከበርሁ ፡ ዐርፋለሁ ፡ ከጥላ ።

ሠ ፡ የእግዚአብሔርን ፡ በዓል ፡ እያከበርኩ ፡ ሰንበትን ፡ ሳልሽር ፡ ሥራ ዬን ፡ እየሠራሁ ፡ እኖራለሁ ።

ወ ፡ ካልቀበጥሁ ፡ ባሌን ፡ ታከበርሁ ፡ በሱ ፡ ላይ ፡ ታልሄድሁ ፡ ከጠቡ ፡ እድናለሁ ፤ ጭቅጭቅና ፡ ንዝንዝ ፡ አይደርስብኝም ፤ ተከብሬ ፡ እኖራ ለሁ ።

208 የዚህ ፡ ጠላ ፡ ነገር ፡ ጠፋኝ ፡ መላ ፡ ቅጡ ፤
—አሮጊቷ ፡ ናቸው ፡ የሚበጠብጡ ።

ሠ ፡ ጠላውን ፡ የጠመቁት ፡ ውሃ ፡ የሞሉበት ፡ አሮጊቷ ፡ ናቸው ።

ወ ፡ ነገር ፡ እያመላለሱ ፡ ወዲያና ፡ ወዲህ ፡ እያዋሸኩ ፡ ትዳራችንን ፡ የሚ በጠብጡት ፡ አሮጊቷ ፡ ናቸው ።

209 የዚያ ፡ ማዶ ፡ ጐመን ፡ እኔንም ፡ ያምረኛል ፤
—ቀንጥሶ ፡ እሚያመጣ ፡ ምን ፡ ወዳጅ ፡ ይገኛል ።

ሠ ፡ እዚያ ፡ ማዶ ፡ የሚታየው ፡ ጐመን ፡ እኔንም ፡ አስጐመዠኝ ፤ አሁን ፡ ቀጥፎ ፡ የሚያመጣልኝ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ አገኛለሁ ።

ወ ፡ ያለፍርሀት ፡ ቀን ፡ በቀን ፡ የወንዶቹን ፡ ኀይል ፡ ጥሶ ፡ ወዳጄን ፡ ነ ጥቆ ፡ የሚያመጣልኝ ፡ እንዴት ፡ ያለ ፡ ጐበዝ ፡ ይገኛል ።

210 የገላ ፡ ሳሙና ፡ ይገዛል ፡ ባልሽ ፤
—ማነን ፡ ሊያጥብበት ፡ ነው ፤ አንቺ ፡ ጥሩ ፡ ነሽ ።

ሠ ፡ አካላትሽ ፡ የጠራ ፡ ነው ፤ እድፍ ፡ የለብሽም ፤ ባልሽ ፡ የገላ ፡ ሳሙና ፡ የገዛው ፡ ማንን ፡ ሊያጥብበት ፡ ነው ።

ወ ፡ «ጥሩነሽ» ፡ እጅግ ፡ ያማርሽ ፡ የተዋብሽ ፡ ነሽ ፤ ደም ፡ ግባትሽ ፡ ልብን ፡ ይማርካል ።

211 የጠጅህን ፡ ማማር ፡ ብርሌህ ፡ ነገረኝ ፤
—ከጠላህ ፡ አልደርስም ፡ ምንም ፡ ቢቸግረኝ ።

ሠ ፡ ጠጅህን ፡ እጋበዛለሁ ፤ ጠላህን ፡ ግን ፡ አልጠጣም ፤ ከንፈሬ ፡ አይነካ ውም ፤ ምንም ፡ ቢሆን ፡ አልቀምሰውም ።

ወ ፡ ከጠላኸኝ ፡ ሁለተኛ ፡ እቤትህ ፡ አልመጣም ፤ እደጅህ ፡ አልደርስም ፤ አጥር ፡ ግቢህን ፡ አልረግጠውም ።

212 የጤፉን ፡ ቀለቤን ፡ ገብስ ፡ ለውጡኝ ፤
—ተኙቼ ፡ ብነሣ ፡ በሶ ፡ አሳለመኝ ።

ሠ ፡ ሽልብ ፡ አድርጎኝ ፡ ብነቃ ፡ በሶ ፡ ስቅም ፡ በሕልሜ ፡ አየሁ ፤ አቃዠኝ ።

ወ ፡ በእንቅልፌ ፡ ሳለሁ ፡ በሕልሜ ፡ አየኋት ፤ በርሷ ፡ አሳለመኝ ፤ አንቀባዠረኝ ።

213 ያላወቃት ፡ ሁሉ ፡ ብቻዋን ፡ ናት ፡ ይላል ፤
—መንፈሴን ፡ ከሷ ፡ ጋር ፡ መሆኑን ፡ ማን ፡ ያውቃል ።

ሠ ፡ ውቃቤዬ ፡ ያልተለያት ፡ መንፈሴ ፡ አብሯት ፡ ያለ ፡ መሆኑን ፡ ሳያውቁ ፡ ሰዎቹ ፡ ብቻዋን ፡ ናት ፡ ይሏታል ።

ወ ፡ ብቻዋን ፡ አይደለችም ፤ ከኔ ፡ ጋራ ፡ ሽርሽር ፡ ታደርጋለች ፤ በፍቅር ፡ ትነፍሳለች ።

214 ያመት ፡ ባል ፡ ቤተ ፡ ክሲያን ፡ ሆኖ ፡ ቢቈይ ፡ ደጇ ፤
—ቆመህ ፡ አስቈርበህ ፡ ስመህ ፡ ሂድ ፡ ወዳጇ ። (ነ ፡ ተ ፡ እ)፡ (ዘለ ፡ ቍ ፡ 98) ፡

ሠ ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተሳልመህ ፡ አስቀድሰህ ፡ ሥጋ ፡ ወደሙ ፡ ተቀብለህ ፡ ሂድ ፤ ቸኵለህ ፡ አትመለስ ።

ወ ፡ ምንም ፡ ሰው ፡ ቢበዛ ፡ ለጊዜው ፡ ባይመች ፡ ቈይተህ ፡ ስመኸኝ ፡ ሂድ ፤ አትጣደፍ ፤ አትቸኵል ።

215 ያመኝ ፡ የነበረ ፡ እያለሳለሰ ፡
—ሰው ፡ መውደዶን ፡ ብተው ፡ ገላዬ ፡ መለሰ ።

ሠ ፡ ያመነምነኝ ፡ ያከሳኝ ፡ የነበረ ፡ ሕመሜ ፡ ፍቅሩን ፡ ትዝታውን ፡ ብተወው ፡ ሰው ፡ መውደዶን ፡ ብረሳው ፡ ተሻለኝ ።

ወ ፡ «ሰው ፡ መውደዶ» ፡ ከምትባለዋ ፡ ወዳጇ ፡ ፍቅሬን ፡ ባቋርጥ ፡ ሰውነቴ ፡ ተመለሰ ።

216 ያምሮቴ ፡ ጀንበሩ ፡ ታሻል ፡ አውራ ፡ ጣቱን ፤
—ተቸግሪያለሁኝ ፡ እኔም ፡ ታናሽቱን ።

ሠ ፡ እኔም ፡ ትንሿን ፡ ጣቴን ፡ ታምሚያለሁ ፤ እየነዘነዘች ፡ እየጠዘጠዘች ፡ ታሠቃየኛለች ።

ወ ፡ እኔም ፡ በበኩሌ ፡ ታናሽ ፡ እኅቱን ፡ ወድጃለሁ ፤ በፍቅሯ ፡ ወድቂያለሁ ።

217 ያባቴንም ፡ ሐዘን ፡ ተውኩት ፡ በኸምር ፤
የናቴንም ፡ ሐዘን ፡ ተውኩት ፡ በኸምር ፤
—ደስታ ፡ በሆዴ ፡ ይጕላላ ፡ ዠመር ።

ሠ ፡ ጤና ፡ ይሰማኝ ፡ ዠመር ፤ ልቤ ፡ በደስታና ፡ በተድላ ፡ ተመላ ፤ ሐዘኑን ፡ ረሳሁት ፤ ትካዜውን ፡ ተውኩት ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ ደስታ ፡ ከሆዴ ፡ አይጠፋም ፤ ሁል ፡ ጊዜ ፡ ይታወሰኛል ፤ ትዝ ፡ ትዝ ፡ ቅር ፡ ቅር ፡ ይለኛል ፤ ነጋ ፡ ጠባ ፡ ስሙን ፡ ባነሣው ፡ እወዳለሁ ።

218 ያባት ፡ ዕዳ ፡ ለልጅ ፡ ይባል ፡ ነበር ፡ ዱሮ ፤
—ባያት ፡ ዕዳ ፡ ገባሁ ፡ እኔማ ፡ ዘንድሮ ።

ሠ ፡ ያባቴን ፡ ሳይሆን ፡ አልፌ ፡ ተርፌ ፡ ያያት ፡ ዕዳ ፡ እከፍላለሁ ፤ የሰው ፡ ብድር ፡ እገፈግፋለሁ ።

ወ ፡ እንደ ፡ አጋጣሚ ፡ አንድ ፡ ልጅ ፡ አይቼ ፡ ዕዳ ፡ ገብቻለሁ ፤ ግራ ፡ ገብቶኝ ፡ የማደርገው ፡ ጠፍቶኝ ፡ ተጨንቂያለሁ ።

219 ያቺን ፡ ቀጭን ፡ ኩታ ፡ ያቺን ፡ ጥበብ ፡ ኩታ ፡ ሆዴ ፡ እየወደዳት ፡
—አላዋቂ ፡ ሰፊ ፡ ባላጨማደዳት ።

ሠ ፡ ያቺን ፡ የምታሳዝን ፡ ቀጭን ፡ ጥበብ ፡ ኩታ ፡ ልብስ ፡ ሰፊው ፡ በጥንቃቄ ፡ በሰፋት ፤ አጨማዶ ፡ የግብር ፡ ይውጣ ፡ እንዳልሆነ ፡ አድርጎ ፡ ባልሰፋት ።

ወ ፡ ያችን ፡ መሳይ ፡ ልጅ ፡ ይሉኝታ ፡ የሌለው ፡ ዐጕል ፡ ባል ፡ በኑሮዋ ፡ አጕሳቈላት ፤ ከሰው ፡ መልክ ፡ አወጣት ፤ የቁም ፡ ስቅሏን ፡ አሳያት ።

220 ያች ፡ ተንኰለኛ ፡ ሴት ፡ የማታንቀላፋ ፡
—ላታመለምለው ፡ ሁሉን ፡ ነድፋ ፡ ነድፋ ።

ሠ ፡ ያቺ ፡ ዕረፍት ፡ የሌላት ፡ ታታሪ ፡ ሴት ፡ ሳትፈትለው ፡ ጥጡን ፡ ነድፋ ፡ ነድፋ ፡ ትታዋለች ።

ወ ፡ ያቺ ፡ ቀበጥ ፡ ዘማዊት ፡ ከሁሉ ፡ ጋራ ፡ ተነካክታለች ፤ እንደ ፡ እብድ ፡ ውሻ ፡ ያንንም ፡ ያንንም ፡ ለካክፋለች ፤ የቀራት ፡ ሰው ፡ የለም ።

221 ያቺን ፡ ጠይም ፡ አሽከር ፡ ልቤ ፡ እንዲያ ፡ ሲወዳት ፡
—ትላንት ፡ በዘነበው ፡ በራሰው ፡ ወሰዳት ።    (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 94) ፡

ሠ ፡ ያቺን ፡ ልጅ ፡ እንዲያ ፡ ስወዳት ፡ ስንጠበጠብላት ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፍርጃ ፡ ቀነ ፡ ጕደሎ ፡ ሆኖ ፡ ኀይለኛ ፡ ዝናብ ፡ ሳይጥል ፡ በትናንቱ ፡ ካፊያ ፡ የሞላው ፡ የወንዝ ፡ ውሃ ፡ ወሰዳት ።

ወ ፡ ያቺን ፡ የምወዳትን ፡ ልጅ ፡ አንድ ፡ ራስ ፡ በራ ፡ ሰው ፡ ነጠቀኝ ፤ ጠልፎ ፡ ወሰዳት ።

222 ያን ፡ ማዶ ፡ በረሓ ፡ ስፈራው ፡ ዱሩን ፡
—መልካም ፡ ገላለጡት ፡ ትሄዱ ፡ እንደሆን ።  (ቀኛ ፡ ም) ፡ (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 185 ፡ 224 ፡ 242) ፡

ሠ ፡ ዕንጨቱን ፡ ቈርጠው ፡ ዱሩን ፡ ጫካውን ፡ መንጥረው ፡ መንገድ ፡ አወጡለት ፤ መሄጃ ፡ ከፈቱለት ፤ የምትሄዱ ፡ ይህን ፡ ጊዜ ፡ ተጓዙ ።

ወ ፡ መጫወት ፡ የወደዳችሁ ፡ ሰውነቷ ፡ ገላዋ ፡ ያማረ ፡ ወይዘሮ ፡ አለች ፤ እዚያ ፡ ሂዱ ።

223 ያንት ፡ አዝመራ ፡ ስንዴ ፡ የኔ ፡ ማሽላ ፡ ነው ፤
—አንተ ፡ ዐጭድህ ፡ ስትከምር ፡ እኔ ፡ አልቄርጥ ፡ ምነው ።

ሠ ፡ አንተ ፡ ስንዴህን ፡ ስታጭድ ፡ እኔስ ፡ ለምን ፡ ማሽላዬን ፡ አልቄር ጥም ፤ አንተ ፡ መከርህን ፡ ስትሰበስብ ፡ እኔ ፡ ሥራ ፡ ፈትቼ ፡ ቦዘኔ ፡ ሆኜ ፡ ለምን ፡ እቀመጣለሁ ።

ወ ፡ አንተ ፡ ማፍቀሩን ፡ ስትተወው ፡ ካንዣትህ ፡ ስትጠላኝ ፡ እኔ ፡ ለምን ፡ ከልቤ ፡ ተስፋ ፡ አልቄርጥም ።

224 ያገሬን ፡ ነጋዴ ፡ አስያዙና ፡ አስመጡት ፤
—ባሳለፉት ፡ እንጂ ፡ ምነው ፡ ባልቀረጡት ። (ቀኛ ፡ ም) ፡ (ዘፈ ፡ ቍ ፡ ( 185 ፡ 222 ፡ 242 ) ፡

ሠ ፡ ያገሬን ፡ ነጋዴ ፡ ምነው ፡ በነጻ ፡ በለቀቁት ፤ ቀረጥ ፡ ባላስከፈሉት ፤ የዛሬን ፡ በማሩት ።

ወ ፡ ከሚወዷትና ፡ ከሚያፈቅሯት ፡ ጡታም ፡ ሴት ፡ ጋራ ፡ መጫወት ፡ ምነው ፡ ባልቀረ ።

225 ይህች ፡ ልጅ ፡ ሳትበድል ፡ ምንም ፡ ሳታጠፋ ፡
—አሁን ፡ በምን ፡ ነገር ፡ አደረች ፡ ተገፋ ። (ን ፡ ጎ ፡ መ) ፡ ( ዘፈ ፡ ቍ ፡ 54 ) ፡

ሠ ፡ ይህች ፡ ልጅ ፡ ምን ፡ አጥፍታ ፡ ነው ፡ የሌሊት ፡ ልብሷን ፡ ተነጥቃ ፡ ቀሚሷን ፡ ተገፋ ፡ ዕራቍቷን ፡ ያደረችው ።

ወ ፡ ሰው ፡ ሳይጠፋ ፡ እኩያ ፡ ሳይታጣ ፡ ክብሯን ፡ አዋርዳ ፡ ገፋ ፡ ክሚባ ለው ፡ አሽከር ፡ ጋራ ፡ ማደሯ ፡ በምን ፡ ነገር ፡ ነው ።

226 ይኸው ፡ ደረትሽ ፡ ነው ፡ ያጣላው ፡ ሰውን ፤
—እስቲ ፡ ሽፈን ፡ አርጊው ፡ ያጡት ፡ እንደሆን ።

ሠ ፡ ምናልባት ፡ ቢሰወራቸው ፡ ደረትሽን ፡ ሽፈን ፡ አድርጊው ፤ አትግለ ጪው ፡ ሸሽጊው ።

ወ ፡ ያ ፡ የሚታየው ፡ ከልብስሽ ፡ ውጭ ፡ ያለው ፡ ጡትሽ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡ ሸፍኚው ፤ ከሰው ፡ ዐይን ፡ ከልዪው ፡ ወደ ፡ ውስጥ ፡ አድርጊው ።

227 ደኅና ፡ ተቀምጠን ፡ ካመመው ፡ ሆዱን ፤
—እናጠጣዋለን ፡ ያምቦውሃ ፡ ባልሽን ። (ነ ፡ ተ ፡ እ) ፡

ሠ ፡ አሁን ፡ ባሁን ፡ ሆዱን ፡ ከጐረበጠው ፡ ጤና ፡ ከነሣው ፡ ባልሽን ፡ ያም፡፡ ፡ ውሃ ፡ እናጠጣዋለን ፤ ፡ሕገረ ፡ ሕይወትን ፡ ጠበል ፡ እናቀምሰ ዋለን ።

ወ ፡ ተተቈጨና ፡ ሆዱን ፡ ከከፋው ፡ ታግመነመነው ፤ ያንን ፡ ቡሐና ፡ መ ላጣ ፡ ባልሽን ፡ እናዋርደዋለን ፤ እስቲበቃው ፡ እልኩ ፡ ድረስ ፡ እንን ግረዋለን ።

228 ደረቴን ፡ ብዳብስ ፡ አጣሁት ፡ ልቤን ፤
—ወዳንተ ፡ መጥቶ ፡ እንደሁ ፡ አበጀ ፡ ይሁን ።

ሠ ፡ የጠፋው ፡ ዕቃዬ ፡ አንተ ፡ ዘንድ ፡ መጥቶ ፡ እንደሆን ፡ ደግ ፡ አደረገ ፤ መልካም ፡ ሠራ ፤ ዘመድ ፡ ዐወቀ ።

ወ ፡ ወዳጄ ፡ አፀጀ ፡ ልቤ ፡ ካንተ ፡ ነው ፤ ኀሊናዬ ፡ ምን ፡ ጊዜም ፡ አይረ
ሳህ ፡ በሐሳብ ፡ አትለየኝም ፤ ከአእምሮዬ ፡ አትጠፋም ።

229 ዳዊቱን ፡ አውርደህ ፡ ድገመው ፡ አንተ ፡ ልጅ ፤
—ምናልባት ፡ ቢመጣ ፡ ይወቅሠናል ፡ ወዳጅ ።

ሠ ፡ የሰው ፡ ያትርሱኝ ፡ ዳዊት ፡ አምጥተን ፡ ሰቅለን ፡ አንድ ፡ ቀን ፡ እ
ንኳ ፡ ሳንደግምበት ፡ ያየ ፡ ወዳጃችን ፡ ዘመድ ፡ አዝማዳችን ፡ ምን ፡
ይለን ፤ እንዴት ፡ ይታዘበን ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ ስንቀብጥ ፡ እንዳልሆነ ፡ ስንሆን ፡ ወዳጄ ፡ የመጣ ፡ እንደ ፡ ሆነ ፡
መጥፎ ፡ አስተያየት ፡ ይወስድብናል ፤ ከግምት ፡ በታች ፡ ያውለናል ።

230 ገበያ ፡ ለመዋል ፡ ስንሄድ ፡ በጧት ፤
—ሳንደርስ ፡ እኮ ፡ ነው ፡ የኛ ፡ መታማት ።

ሠ ፡ አራዳ ፡ ሳንወጣ ፡ እገበያ ፡ ውለዋል ፡ ተብለን ፡ ታማን ፤ ሳንደርስ ፡
ደረሳችሁ ፡ ተባልን ፤ በከንቱ ፡ ባልሠራነው ፡ ሥራ ፡ ስማችን ፡ ተነሣ ።

ወ ፡ ሳንፋቀር ፡ ተፋቀሩ ፡ ሳንቀብጥ ፡ ቀበጡ ፡ ተብለን ፡ ታማን ፤ ባላደረግ
ነው ፡ ባልሠራነው ፡ ነገር ፡ ሐሜት ፡ ደረሰብን ፤ ስማችን ፡ ጠፋ ።

231 ገና ፡ ስትወለድ ፡ ምን ፡ አጠነከራት ፤
መንደርደር ፡ ዠመረች ፡ ሁለት ፡ ወር ፡ ሳይሞላት ፤
—ድኻ ፡ አታውቅም ፡ እሷ ፡ እግዜር ፡ ከፈጠራት ።

ሠ ፡ ከተወለደች ፡ ዠምሮ ፡ በመሬት ፡ ተንፏቃ ፡ ባራት ፡ እግሯ ፡ ሄዳ ፡
አታውቅም ፤ አትድኽም ፤ በምድር ፡ ላይ ፡ እየተጐተተች ፡ አትሄ
ድም ።

ወ ፡ እሷ ፡ ለድኻ ፡ አትለመንም ፡ ሀብት ፡ ገንዘብ ፡ ለሌለው ፡ ፊት ፡ አትሰ
ጥም ፤ እንደ ፡ ሌሎች ፡ ሴቶች ፡ በቀላሉ ፡ አትበገርም ።

232 ግባ ፡ በይው ፡ እንጂ ፡ ምነው ፡ ወደ ፡ ደጅ ፤
—ከጨለመ ፡ ወዲያ ፡ የት ፡ ይሂድ ፡ ወዳጅ ።

ሠ ፡ ከብት ፡ ከገባ ፡ ጀንበር ፡ ከጠለቀ ፡ ወዲያ ፡ እኛን ፡ ብሎ ፡ የመጣ ፡
ወዳጅ ፡ በጨለማ ፡ ወዴት ፡ ይሄዳል ፤ ሲመሽ ፡ እያየን ፡ የት ፡ እንሰደ
ዋለን ።

ወ ፡ ወዳጅ ፡ ከጨለመ ፡ ወዲያ ፡ ከመጣ ፡ መሄድ ፡ የለበትም ፤ ማደር ፡
ይገባዋል ።

233 ጐዣምና ፡ ጐንደር ፡ ምን ፡ ያደርግልኛል ፤
—ለኔ ፡ ለኑሮዬ ፡ ባሌ ፡ ይሻለኛል ። (ከ ፡ ር ፡ ዘ) ፡

ሠ ፡ ከሁሉም ፡ ቦታ ፡ «ባሌ» ፡ የሚባለው ፡ አገር ፡ ይመቸኛል ፤ ለጤናዬ ፡
ይስማማኛል ።

ወ ፡ ባልን ፡ የመሰለ ፡ የለም ፤ ማንኛውም ፡ ነገር ፡ በሱ ፡ ያምራል ፤ ለኑሮ ፡
እንደ ፡ ባል ፡ የሚመች ፡ አይገኝም ።

234 ጠላቴ ፡ ነህ ፡ እንጂ ፡ መች ፡ ወዳጄ ፡ ነህ ፤
—አትድረስ ፡ ከደጄ ፡ አንተን ፡ አልይህ ።

ሠ ፡ እቤቴ ፡ አትምጣ ፤ አጥር ፡ ግቢዬ ፡ አትድረስ ፤ እፊቴ ፡ አትቅረብ ፤ እኔ ፡ ባለሁበት ፡ ቀበሌ ፡ እንዳላይህ ።

ወ ፡ እባክህ ፡ መጥተህ ፡ አንድ ፡ ጊዜ ፡ ልይህ ፤ መልክህን ፡ ልመልከተው ፤ ፊትህን ፡ አይቼ ፡ ልጥገበው ።

235 ጠጁን ፡ ብንጋብዘው ፡ ከቤት ፡ ያለንን ፡
—እሱ ፡ ጠላን ፡ ወዶ ፡ አቀለለብን ።

ሠ ፡ ጠጅ ፡ ብንሰጠው ፡ ጠላ ፡ ካልሆነ ፡ ብሎ ፡ ግብዣችንን ፡ አቃለለብን ፤ ናቀብን ፤ ከምንም ፡ ሳይቈጥረው ፡ ቀረ ።

ወ ፡ ያን ፡ ያኸል ፡ ይወደን ፡ የነበረው ፡ ሰው ፡ ጠላን ፤ እቤታችን ፡ መድረስን ፡ ተወው ፤ ተንገፈገፈ ።

236 ጠጅ ፡ ልኬልሻለሁ ፡ ውስኪ ፡ ላኪልኝ ፤
—ጠላ ፡ ቀረ ፡ ብለሽ ፡ አትቀየሚኝ ።

ሠ ፡ የጠላ ፡ መጠጥ ፡ ሳይደርሰኝ ፡ ቀረ ፡ ብለሽ ፡ አትከፊ ፤ ሆድ ፡ አይባስሽ ፤ ቅርታ ፡ አይግባሽ ።

ወ ፡ ጠልቶኝ ፡ ቀረ ፡ ንቆ ፡ ተወኝ ፡ ብለሽ ፡ አትዘኚ ፤ አትቀየሚ ።

237 ጠጅ ፡ እጠጣ ፡ ነበር ፡ ማለቱ ፡ አይቀርም ፡ ወይ ፤
—እንዲያው ፡ የጠላ ፡ ሰው ፡ ያስታውቅ ፡ የለም ፡ ወይ ።

ሠ ፡ ጠላ ፡ የሚወድ ፡ ሰው ፡ በሁኔታው ፡ ባኳኋኑ ፡ ያስታውቃል ፤ በፊቱ ፡ ያስረዳል ።

ወ ፡ ጥላቻ ፡ ያለበትና ፡ በልቡ ፡ የተቀየመ ፡ ሰው ፡ እንዲሁ ፡ ያስታውቃል ፤ ሁኔታው ፡ ያስረዳል ።

238 ጤፉን ፡ ዳዋ ፡ በላው ፡ ቀለባችንን ፤
—አንቺ ፡ ሰው ፡ አርሚ ፡ እንጣላለን ።

ሠ ፡ እባክሽ ፡ ጤፋችንን ፡ አርሚው ፤ ዳዋ ፡ በላው ፤ አራሙቻ ፡ ዋጠው ፤ እንደ ፡ ዋለ ፡ ሊቀር ፡ ነው ።

ወ ፡ አንቺ ፡ ሴት ፡ ሌላውን ፡ ሰው ፡ እርም ፡ ብለሽ ፡ ተዪ ፤ ኋላ ፡ እንጣላለን ፤ ከክፉ ፡ ነገር ፡ እንደርሳለን ።

239 ጤፍማ ፡ ብበላ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ በቻለኝ ፤
ስንዴማ ፡ ብበላ ፡ ምን ፡ ሰው ፡ በቻለኝ ፤
—ገብስ ፡ ነው ፡ እራቴ ፡ በሶ ፡ አደከመኝ ።

ሠ ፡ በሶ ፡ እየቃምሁ ፡ ሰውነቴ ፡ ደከመ ፤ ዐቅም ፡ አነሰኝ ፤ ጕልበቴ ፡ አለቀ ።

ወ ፡ በሷ ፡ ፍቅር ፡ ሰውነቴ ፡ ደከመ ፤ ሁለመናዬ ፡ ዛለ ።

240　ጥንቱን ፡ የቀበጥሁት ፡ እኔ ፡ አይደለሁም ፡ ወይ ፤
—ባትርሱኝ ፡ የመጣ ፡ ዝናም ፡ ይቻላል ፡ ወይ ።

ሠ ፡ በብዙ ፡ ጸሎት ፡ በምሕላና ፡ በእግዚኦታ ፡ የሚዘንብ ፡ ዝናብ ፡ ከባድ ፡ ነው ፤ ዶፍ ፡ በረዶ ፡ ይሆናል ።

ወ ፡ ባማላጅ ፡ የመጣው ፡ አቶ ፡ ዝናቡ ፡ ተጫነኝ ፤ ኀይለኛ ፡ ሆነብኝ ፤ አላስቆም ፡ አላስቀምጥ ፡ አለኝ ።

241　ጥጡን ፡ ነድፈሽ ፡ ነድፈሽ ፡ ባልጋ ፡ ቈልለሻል ፤
—ይኸን ፡ አመልምለሽ ፡ ብተይ ፡ ይሻልሻል ።

ሠ ፡ የነደፍሽውን ፡ አምልማሎ ፡ አድርገሽ ፡ ብታርፊ ፡ ይሻላል ።

ወ ፡ ይኸን ፡ መጥፎ ፡ ዐመልሽን ፡ ምለሽ ፡ ርግፍ ፡ አድርገሽ ፡ ብትተዪው ፡ ይጠቅማል ።

242　ፈርማውን ፡ ከያዘ ፡ የሹሙን ፡ ምልክት ፤
—ባሳለፉት ፡ እንጂ ፡ ምነው ፡ ባልቀረጡት ።　(ቀኛ ፡ ም) ፡ (ዘፈ ፡ ቍ ፡ 185 ፡ 222 ፡ 224) ፡

ሠ ፡ ነጋዴውን ፡ በነጻ ፡ በለቀቁት ፤ ቀረጥ ፡ ባላስከፈሉት ፤ የዛሬን ፡ ባሳለፉት ።

ወ ፡ ባለአጐጠጐጤ ፡ ጡታም ፡ የሆኑት ፡ ሴቶች ፡ ምነው ፡ እንደ ፡ ልብ ፡ በተገኙ ፤ ባልጠፉና ፡ ባልታጡ ።

243　ፋሲካ ፡ ለመድረስ ፡ ትንሽ ፡ ሲቀረው ፡
—እንዴት ፡ በመጋቢት ፡ ይሞታል ፡ ሰው ።

ሠ ፡ እንዴት ፡ ሰው ፡ ጾሞ ፡ ጾሞ ፡ ወደ ፡ ፋሲካው ፡ ሲቃረብ ፡ እትንሣኤ ፡ ሲደርስ ፡ በመጋቢት ፡ ወር ፡ ይሞታል ፤ ባጕል ፡ ሰዓት ፡ ያርፋል ።

ወ ፡ ካልጠፋ ፡ ሴት ፡ እንዴት ፡ ሰው ፡ በገረድ ፡ ፍቅር ፡ ይሞታል ።



# በመዲና ፡ ምስጋና ፤ ሐዘን ፤ ትካዜ ።

1 መች ፡ ይቸግራል ፡ ስንዴ ፡ ዘር ፤
—ካለማ እግዚአብሔር ።

ሠ ፡ እግዚአብሔር ፡ ቡቃያውን ፡ ካለማው ፡ ለፍሬ ፡ ካበቃው ፡ ስንዴ ፡ አይቸግርም ።

ወ ፡ የእግዚአብሔር ፡ ፈቃድ ፡ ከሆነ ፡ ሁሉ ፡ ነገር ፡ ይፈጸማል ፡ እሱ ፡ ያለው ፡ ይሆናል ፡ ያለ ፡ አምላክ ፡ ትእዛዝ ፡ የሚደረግ ፡ ነገር ፡ የለም ።

2 በከንቱ ፡ ያሙታል ፡ ባሰት ፤
—ሰው ፡ በላ ፡ ብለው፡ መሬት ።

ሠ ፡ ሰውን ፡ መሬት ፡ አፈር ፡ ትቢያ ፡ ይበላል ፡ እያሉ ፡ ያሙታል ።

ወ ፡ መሬት ፡ የሰውን ፡ ልጅ ፡ በላው ፡ በመቃብር ፡ ጨረሰው ፡ አፈር ፡ አደረገው ።

3 ባስብ ፡ ብሠራ ፡ ብመኝ ፤
መቼም ፡ ዘንድሮ ፡ አልሆነኝ ፡
አዘነ ፡ ሆዴ ፡ ተናደደ ፡
—ምነው ፡ ይዞኝ ፡ በሄደ ።

ሠ ፡ አሁን ፡ አብሬው ፡ ብሄድ ፡ ምን ፡ ቸገረው ፡ ለምን ፡ ትቶኝ ፡ ሄደ ፡ ቢያስከትለኝ ፡ ምን ፡ ነበር ።

ወ ፡ እንዲህ ፡ ከምጐሳቆል ፡ ምነው ፡ ብሞትስ ፡ የቁም ፡ ስቃይ ፡ ከማይ ፡ ምን ፡ ቸገረው ፡ ሞት ፡ ይዞኝ ፡ ቢሄድ ።

4 አልሰማም ፡ አለ ፡ ብነግረው ፤
—ድፍን ፡ የሸዋ ፡ ሰው ። (1)

ሠ ፡ የሸዋ ፡ ሰው ፡ በሙሉ ፡ ነገሩ ፡ አልገባውም ፡

ወ ፡ የሸዋ ፡ ሰው ፡ የተነገረው ፡ ምሥጢር ፡ አይገባውም ፡ ቃሌን ፡ አቃለለው ፡ የውሃ ፡ ጨኸት ፡ አደረገው ።

5 አምላክ ፡ ብጠራህ ፡ ዝም ፡ አልህ ፤
—ምነው ፡ እያለህ ፡ እንዴለህ ።

ሠ ፡ ምነው ፡ ሲያብል ፡ የተኛን ፡ ሆንክ ፡ እያለህ ፡ እንደሌለህ ፡ ሁሉ ፡ እየሰማህ ፡ ዝም ፡ አልህ ።

ወ ፡ ሀ) እግዚአብሔር ፡ ሆይ ፡ መስጠት ፡ መንሳት ፡ ገንዘብህ ፡ ሆኖ ፡ ሳለ ፡ ምነው ፡ ዝም ፡ አልኸኝ ፡ ምነው ፡ ስቸገር ፡ ጨከንክብኝ ።

(ለ) ምነው ፡ ምሉዕ ፡ በኩላሄ ፡ ስትሆን ፡ በግዛትህ ፡ እንዲህ ፡ ያለ ፡ ግፍ ፡ ሲሠራብኝ ፡ ዝም ፡ ትላለህ ።

---

(1) አንድ ፡ አቅራሪ ፡ ጦር ፡ መምጣቱን ፡ ተረድቶ ፡ ከብት ፡ ለመግዛት ፡ እንደሚፈልግ ፡ ሁሉ፡ በሸዋ ፡ ጦር ፡ ሠፈር ፡ እየዞረ ፡ በፈሊጥ ፡ እጅህን ፡ አውጣ ፡ አምልጥ ፡ ለማለት ፡ "ፈረስ ፡ ያለህ ፡ ብር ፡" እያለ ፡ ቢለፍም ፡ ምሥጢሩ ፡ የሚገባው ፡ ጠፍቶ ፡ አደጋው ፡ ስላልቀረ ፡ ሠራዊቱን ፡ ለመውቀስ ፡ ሲል ፡ የገጠመው ።

6 አዝመራ : ዛሬ : ተከተተ :
—አባቴ : እሽቴ : ሞተ ። ( ነ. ተ. እ.)

ሠ : አባባ : ሰብሌ : አልተረፈም : ዘማች : አደባየው : በእሽትነቱ : አጠፋው ።
ወ : አባቴ "እሽቴ :" አረፈ : ከዚህ ዓለም : በሞት : ተለየ : ያባት : ነገር : እ
ንግዲህ : በቃ : ተከተተ ።

7 አይቼ : መጣሁ : ብዙ : ጉድ ፤
—የሰው : አዝመራ : ሲታጨድ ። (1)

ሠ : የዚያ : የሀብታም : ሰፊ : አዝመራ : ልክ : በሌለው : ሰው : ሲታጨድ :
ሲሰበሰብ : አየሁ ።
ወ : በፋሽስት : ጊዜ : የሰው : ልጅ : እንደ : አዝመራ : ሲታጨድ : እንደ:
እህል : ሲወቃ : አየሁ ።

8 አጤ : ምኒልክ : ተጉዘው :
ከቤቴ : በላይ : ሰፍረው ፤
ሳያዙ : አይቀሩም : መጥን :
—እንጀራ : ጠላ : እኔን ።

ሠ : እንጀራና : ጠላ : አምጣ : መጥን : አግባ : ብለው : ጭቃ : ሹሞቹ : ሳያ
ዙኝ : አይቀሩም : እሰጋለሁ ።
ወ : ኑሮ : አልሆነልኝም : እንጀራ : አጣሁ ፤ ማግኘት : አቃተኝ ።

9 እስካሁን : ድረስ : ያልመጣነው :
—ጊዜው : ጣይ : ኖሆብን : ነው ።

ሠ : ቀኑ : ዋዕየ ፀሐይ : የበዛበት : በመሆኑ : ነው : የዘገየነው ።
ወ : ጊዜው : ቢያርሱ : ቢነግዱ : ቢወጡ : ቢወርዱ : ቢደክሙ ውጤት : የማ
ይሰጥ : ሆኗል ።

10 እየተጠራሁ : ሳጥር :
—ምነው : ዝም : አለኝ : እግዚአብሔር ።

ሠ : ይህን : ያህል : ስጣራ : ምነው : አለመስማቱ : ጥሪዬን : አለመቀበሉ ።
ወ : እንደዚህ : ስጨነቅ : ሳጣጥር : ፈጣሪዬ : ለምን : አልሰማም : አለኝ : ለቅ
ሶዬን : አልቀበል : አለኝ ።

11 እጅ : እግር : የለው : ቆማጣ ፤
—የሚመርቀን : መጣ ። (የኔታ : ፋንታ) (2)

ሠ : ብንሰጠው : እግዚአብሔር : ይስጥልኝ : ብሎ : የሚመርቀን : በሽተኛ :
መጣ ።
ወ : መራር : ስቃይ : የምናይበት : ብርቱ : ግፍ : የምንቀበልበት : ክፉ : ቀን :
መጣ : የጭንቀትና : የጥበት : ዘመን : ደረሰ ።

---

(1) ጠላት : በአገራችን : በወራሪነት : ገብቶ : በነበረ : ጊዜ : ይልቁንም : በየካቲት : ፲፪ :
፲፱፻፳፱ : ዓ. ም : ሕዝቡን : በጭካኔ : መፍጀቱን : ለመግለጥ : የተገጠመ ።

(2) የኔታ : ፋንታ : የሚባሉ : የቤተ : ክህነት : ሰው : የፋሽስትን : ግፈኛነትና : ጭካኔ : ጠ
ላት : ከመምጣቱ : በፊት : የተነበዩበት ።

12 ካልጋ ፡ መቀመጥ ፡ ከጠፋር ፡
ይመስለን ፡ ነበር ፡ የሚያምር ፡
አባቶቻችንን ፡ ብናያቸው ፡
—ሁሉም ፡ እመሬት ፡ ናቸው ።

ሠ ፡ ሽማግሌዎች ፡ በሙሉ ፡ የተቀመጡት ፡ እመሬት ፡ ላይ ፡ ነው ።
ወ ፡ አባቶቻችን ፡ በሞት ፡ አልቀዋል ፡ ሁሉም ፡ መሬት ፡ ሆነዋል ።

13 ወዳጇ ፡ ገዛ ፡ ከብት ፡
—ላቀው ፡ ወንድና ፡ ሴት ። ( ቀኛ. ቦረና ፡)[1] ( መጺ. ቍ. 19 )

ሠ ፡ ላቀው ፡ ወዳጇ ፡ ከብት ፡ ማርባት ፡ ፈልጐ ፡ ላምና ፡ በሬ ፡ ጊደርና ፡ ወይፈን፡ ገዛ ።
ወ ፡ ላቀው ፡ የወንድና ፡ የሴት ፡ ባሕርይ ፡ የተቀላቀለበት ፡ ሰው ፡ ነው ፡ የፋናፋንት ፡ ተፈጥሮ ፡ አለበት ።

14 የሞላሁትን ፡ ወተት ፡
ከንስራው ፡ ጐድሎ ፡ አየሁት ፡
እንግዲህ ፡ ምን ፡ አረጋለሁ ፡
—የተረፈውን ፡ እገፋለሁ ።

ሠ ፡ ምን ፡ ይበጃል ፡ ምንስ ፡ ማድረግ ፡ ይቻላል ።
ወ ፡ የወተቱ ፡ ጋን ፡ ጐደሎ ፡ ከሆነ ፡ ምኑን ፡ አርግቼ ፡ ቅቤ ፡ አወጣለሁ ።
ሠ ፡ ከንስራው ፡ ውስጥ ፡ የቀረውን ፡ እንጣለሁ ።
ወ ፡ ተረፈ ፡ ዘመኔን ፡ እንደምንም ፡ አድርጌ ፡ እገፋዋለሁ ፡ በትዕግስት ፡ እፈጽርሰዋለሁ ።

15 የሸምበቆ ፡ ቤት ፡ መሥራት ፡
ተጠንቅቆ ፡ ነው ፡ በብልሀት ፡
ገና ፡ ሲያመጣው ፡ ከሜዳ ፡
—ሲቀልሰው ፡ ተጐዳ ።

ሠ ፡ ገና ፡ ቆርጦ ፡ አምጥቶ ፡ ጫፉን ፡ ሲመልሰው ፡ በመሰበሩ ፡ ተጐዳ ።
ወ ፡ ሰው ፡ በቅሌታምነቱ ፡ ይጐዳል ፡ በባለጌነቱም ፡ የኋላ ፡ ኋላ ፡ ይዋረዳል ፡ ያፍራል ።

16 ያስቀመጥሁትን ፡ ለራት ፡
መሶቡን ፡ ብከፍት ፡ አጣሁት ፡
እስኪ ፡ አፈላልጉኝ ፡ በሙብራት ፡
—ሰውን ፡ በላው ፡ መሬት ።

---

(1) ቀኛ ፡ ቦረና ፡ የሚባሉ ፡ ቧልተኛ ፡ ሰው ፡ ላቀው ፡ የሚባለውን ፡ ወንዳገረድ ፡ በአማርኛ ፡ ዘይቤ ፡ የዘለፉበት ።

ሠ ፡ እራቱ ፡ የት ፡ ደረሰ ፡ ማን ፡ በላው ፡ እመሬት ፡ ገባ ፡ ሰው ፡ ወሰደው ፡ የት ፡ ጠፋ ?

ወ ፡ አ ፡ አዳም ፡ መሬት ፡ አንተ ፡ ወትገብዕ ፡ ውስተ ፡ መሬት ፡" በተባለው ፡ ቃል ፡ የሰው ፡ ልጅ ፡ ወደ ፡ መሬት ፡ እየገባ ፡ አለቀ ፡ በሞት ፡ ተጠነፈፈ ።

17 ይኸንን ፡ ሁሉ ፡ አቋርጬ ፡
እንደምን ፡ ልለፍ ፡ አፍጥሬኝ ፡
የዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ የማየው ፡
ዓይኑ ፡ ተፈሪ ፡ ነው ። ( ኤልያስ ፡ ወ. ጸ. )

ሠ ፡ በዚህ ፡ ሁሉ ፡ ሰው ፡ ማህል ፡ እንደምን ፡ አልፌ ፡ ልምጣ ፡ የሕዝቡ ፡ ዓይን፡ ያስፈራል ።

ወ ፡ ዓይናችን ፡ ብርሃናችን ፡ ንጉሥ ፡ ተፈሪ ፡ (ቀ. ኃ. ሥ.) ነው ፡ ተድላ ፡ ደስታ ፡ የምናየው ፡ በጃንሆይ ፡ ነው ።

18 ጃንሆይ ፡ ምድረ ፡ ርስት ፡ አንሷቸው ፡
ወሰን ፡ ሲገፉ ፡ በግራቸው ፡
ተላይ ፡ ተሰማ ፡ ታላቅ ፡ ቃል ፡
አስፋው ፡ ደግ ፡ ነው ፡ የሚል ። ( ኤልያስ ፡ ወ. ጸ. )

ሠ ፡ መልካም ፡ አርገሃል ፡ ወሰንህን ፡ አስፋ ፡ ዳር ፡ ድንበሩን ፡ አስተካክል ፡ የሚል ፡ ቃል ፡ ከላይ ፡ ተሰማ ።

ወ ፡ አስፋ ፡ ወሰን ፡ ኃ. ሥ. ደግ ፡ ቸር ፡ ልበ ፡ ርኅሩህ ፡ ነው ።

19 ጌታ ፡ ይወዳል ፡ ጠላቱን ፡
ዓርብ የሰቀለውን ። (1) ( መዲ. ቍ. 13 )

ሠ ፡ ጌታችን ፡ ኢየሱስ ፡ ክርስቶስ ፡ በዕለተ ፡ ዓርብ ፡ የሰቀለውን ፡ ጠላቱን ፡ እንኳን ፡ አልተበቀለም ፡ "ይቅር ፡ በላቸው ፡ አባቴ ፡ ሆይ ፡ የሚሠሩትን ፡ አያውቁምና ፡" ብሎ ፡ ጸለየ ፡ እንጂ ።

ወ ፡ አርብ - ሰቀል ፡ የሆነውን ፡ ሽማኔ ፡ ቀኛ ፡ ቦረናን ፡ ጌታው ፡ ወደደው ፡ ባለሟል ፡ አደረገው ።

---

(1) ላቀው ፡ ፍናፍንት ፡ ብለው ፡ የሰደቡትን ፡ ቀኛ ፡ ቦረናን ፡ አንተም ፡ ሽማኔ ፡ ነበርህ ፡ ብሎ፡ መልስ ፡ የሰጠበት ።

## ፱ ለ ሰ ኛ ።

1 ሀብቴ ፡ በመጥፋቱ ፡ ሳለቅስ ፡ ሳዝን ፡
—ደሞ ፡ ዓይኔን ፡ አጠፋት ፡ እንዳላይ ፡ ብርሃን ።

ሠ ፡ ዓይኔን ፡ በጥፊ ፡ መተው ፡ ብርሃኔ ፡ ታወከ ፡ ታወርኩ ።

ወ ፡ እንደ ፡ ልጄ ፡ ሀብቴ ፡ ዓይኔ ፡ የሚባለውንም ፡ ወንድሙን ፡ ገደሉብኝ ፡ ጧሪ ቀባሪ ፡ አሳጡኝ ፡ የወላድ ፡ መካን ፡ አረጉኝ ።

2 ለትንሽ ፡ ወንድሜ ፡ ሠራሁለት ፡ ቤት ፡
—እኔ ፡ ውሀ ፡ ሆኜ ፡ እናቴ ፡ መሬት ።

ሠ ፡ እኔ ፡ ውሀ ፡ በማመላለስ ፡ እናቴ ፡ አፈር ፡ በመሸከም ፡ ተረዳድተን ፡ ለትንሽ ፡ ወንድሜ ፡ ቤት ፡ ሠራንለት ።

ወ ፡ በእናቴና ፡ በትንሽ ፡ ወንድሜ ፡ ሞት ፡ ኀዘን ፡ ጸናብኝ ፡ ውሀ ፡ ሆንኩ ፡ ብዙ ፡ አለቀስኩ ።

3 ለንጉሥ ፡ ጥሬ ፡ ቅቤ ፡ ምንም ፡ አይፈውሰው ፡
—አንጥር ፡ አትልም ፡ ወይ ፡ ያመጣልህን ፡ ሰው ።

ሠ ፡ ጥሬ ፡ ቅቤ ፡ ሲመጣልህ ፡ ለምን ፡ አንጉፋት ፡ ወይም ፡ አንጥሩት ፡ አትልም፡

ወ ፡ ያልተጣራ ፡ ወሬ ፡ ሲመጣልህ ፡ ውሳኔ ፡ ከመስጠት ፡ በፊት ፡ ለምን ፡ ይጣራ ይመርመር ፡ አትልም ።

4 ምነው ፡ ገንዘብ ፡ አልሰጥ ፡ ምነው ፡ አላበድር ፡
—ይኸን ፡ ሁሉ ፡ መሬት ፡ ተመርቼ ፡ ሳድር ።

ሠ ፡ ይህን ፡ ያህል ፡ መሬት ፡ እያለኝ ፡ ለምን ፡ እንዳጣ ፡ ሰው ፡ ለሌለው ፡ አላበድርም ፡ አልቸርም ?

ወ ፡ ይህነን ፡ ሁሉ ፡ አገር ፡ የምሄደው ፡ እየተመራሁ ፡ ነው ፡ ማየት ፡ አልችልም ፡ ዓይነ ፡ ስውር ፡ ነኝ ።

5 ራቁቴን ፡ ሄድሁኝ ፡ በሰው ፡ ፊት ፡ ብደፍር ፡
—ራሴን ፡ ታዘብሁት ፡ ወዮው ፡ ዓለማፈር ።

ሠ ፡ ሐፍረተ ፡ ቢስ ፡ ደፋር ፡ መሆኔን ፡ እኔኑ ፡ አስደነቀኝ ፡ ራሴን ፡ ታዘብሁት ።

ወ ፡ ወዲያልኝ ፡ ወዲያ ፡ ዓለም ፡ ከንቱ ፡ ነው ፡ እንደ ፡ ትቢያ ፡ በኖ ፡ ጠፊ ፡ ነው።

6 ሸማ ፡ ሳይታጣ ፡ ልብስ ፡ ሳይቸግር ፡
—እንደምን ፡ የኔ ፡ እህት ፡ ተገፋ ፡ ትዳር ።

ሠ ፡ ሸማ ፡ እያለ ፡ ልብስ ፡ ሳይጠፋ ፡ ለምን ፡ የኔ ፡ እህት ፡ እንደዚሁ ፡ ዕራቁቷን ፡ አደረች ፡ ብርድ ፡ መታት ።

ወ ፡ እንዴት ፡ የኔ ፡ እህት ፡ ገፋ ፡ ከሚባለው ፡ አሽከር ፡ ጋር ፡ ስትዋደቅ ፡ ዝም ፡ አላችሁ ፡ ለምን ፡ አልነገራችሁኝም ።

7 በቀጭን ፡ አጃኖ ፡ ላይ ፡ የምትደርበው ፡
—ያለምድህ ፡ አለቀ ፡ ያከባከብከው ።

ሠ ፡ ያ ፡ በጃኖህ ፡ ላይ ፡ የምትደርበው ፡ የምታከባክበው ፡ ለምድህ ፡ ሎፊሳህ ፡ አረጀ ? አለቀ ? የት ፡ ደረሰ ?

ወ ፡ (ሀ) ያ ፡ ባንተ ፡ ጊዜ ፡ ይደላደል ፡ ይቀማጠል ፡ የነበረው ፡ ድኻ ፡ (ሕዝብ ፡)
ዛሬ ፡ አንተ ፡ ብትሞት ፡ ተጕሳቆለ ፡ የሚገባበት ፡ አጣ ፡ ግራ ፡ ገባው ።
(ለ) ያ ፡ ደግ ፡ ልማድህ ፡ ቀረ ፡ በጐ ፡ ሥራህ ፡ ተረሳ ፡ ተዘነጋ ።

8 **በተክለሃይማኖት ፡ ጐትነሽ ፡ ስትኖሪ ፡**
**—በይ ፡ መንገሻ ፡ መጣ ፡ እንግዲ ፡ ተሡሪ ።**

ሠ ፡ መንገሻ ፡ ወዳጅሽ ፡ መጣ ፡ በይ ፡ ጠጕርሽን ፡ ተሡሪ ፡ ሰውነትሽን ፡ አሳምሪ፡
ወ ፡ አጅሬ ፡ መንገሻ ፡ መጣ ፡ ወታደሩን ፡ በባላገሩ ፡ ላይ ፡ ሊሡራው ፡ ነው ፡ ድካ
ውን ፡ ሊያስወርረው ፡ ነው ።

9 **በወታደር ፡ ሥራ ፡ አልሰለጠንኩኝ ፡**
**—አሁን ፡ ለምንድነው ፡ ተጦር ፡ ሂድ ፡ ያሉኝ ።** ( ብ. ገ. ሕ. በለጠ ፡)

ሠ ፡ የጦር ፡ ትምህርት ፡ ሳይኖረኝ ፡ ለምን ፡ ወደ ፡ ዘመቻ ፡ ይሰዱኛል ፡ ያተኳኮ
ሱን ፡ ዘዴ ፡ ሳላውቀው ፡ ከጦር ፡ ሜዳ ፡ ብሄድ ፡ ምን ፡ እፈይዳለሁ ፡ ምንስ ፡
ሞያ ፡ እሡራለሁ ።
ወ ፡ አሁንም ፡ ማገልገል ፡ ስችል ፡ ሥራ ፡ ሳውቅ ፡ ለምንድነው ፡ ወደ ፡ ጡረታ ፡
የሚወስዱኝ ፡ እንደ ፡ ደካማ ፡ የሚቆጥሩኝ ።

10 **በጣም ፡ ያስደንቃል ፡ የኔስ ፡ አኳኋን ፡**
**—የወለድሁት ፡ ልጄ ፡ አጠፋው ፡ ዓይኔን ።**

ሠ ፡ የገዛ ፡ ልጄ ፡ ዓይኔን ፡ አፈሰሰው ፡ አካሌን ፡ አጐደለው ።
ወ ፡ በልጄ ፡ ሞት ፡ ለቅሶ ፡ ዓይኔ ፡ ጠፋ ።

11 **ቤታችን ፡ ተሡርቶ ፡ በመንታ ፡ መንገድ ፡**
**—እናያለን ፡ ሁሉን ፡ ሲወጣ ፡ ሲወርድ ።** ( ሰሎሞን ፡ የኔ ፡ ነህ ።)

ሠ ፡ ቤታችን ፡ አማካይ ፡ ቦታ ፡ ላይ ፡ በመሆኑ ፡ አላፊ ፡ አግዳሚውን ፡ ሲወጣ ፡
ሲወርድ ፡ እናያለን ።
ወ ፡ (1) መቆየት ፡ ደግ ፡ ነው ፡ መሾም ፡ መሻር ፡ መክበር ፡ መደኸየት ፡ ማግ
ኘት ፡ ማጣት ፡ በሰው ፡ ልጅ ፡ ላይ ፡ ሲፈራረቁ ፡ እናያለን ።
(2) የአዳም ፡ ልጅ ፡ ሲወለዱና ፡ ሲሞቱ ፡ እንመለከታለን ።

12 **ኃይለኛ ፡ ደብድቦን ፡ አግብቶን ፡ ከማጥ ፡**
**—እኔ ፡ ብቻ ፡ ቀረሁ ፡ ክንፍ ፡ ያለው ፡ ሲያመልጥ ።** ( 1) ( ነ. ተ. እ.)

ሠ ፡ ክንፍ ፡ ያለው ፡ በሮ ፡ ሲያመልጥ ፡ ክንፍ ፡ ያጣሁት ፡ መብረር ፡ የማልች
ለው ፡ እኔ ፡ ብቻ ፡ ቀረሁ ።
ወ ፡ ዘመድ ፡ ያለው ፡ ክንፌ ፡ ሲለቀቅ ፡ እኔ ፡ ወገን ፡ ያጣሁት ፡ ታስሬ ፡ ቀረሁ ፡
የሚያማልድ ፡ ዘመድ ፡ ባለማግኘት ፡ ተጉላላሁ ።

13 **አላልቅልኝ ፡ ብሎ ፡ የተጀመረው ፡ ቤት ፡**
**—በቀን ፡ ሳጥር ፡ ውዬ ፡ ደሞ ፡ አድራለሁ ፡ ሌሊት ።**

ሠ ፡ ቀን ፡ የሡራሁት ፡ አልበቃ ፡ ብሎ ፡ ሌሊት ፡ ደግሞ ፡ አጥራለሁ ፡ አጋም ፡
ስሸመጥጥ ፡ አድራለሁ ።

---

(1) ነጋድራስ ፡ ተሰማ ፡ እሸቴና ፡ ፊታ ፡ ክንፌ ፡ባንድነት ፡ ታስረው ፡ ሳላ ፡ ጓደኛቸው ፡ ፊታ፡
ክንፌ ፡ በዘመድ ፡ ኃይል ፡ ስለተፈቱ ፡ ነጋድራስ ፡ ተሰማ ፡ ወገን ፡ ማጣታቸውን ፡ የገለ
ጡበት ።

ወ ፡ ቀኑን ፡ በጨንቅ ፡ ውዬ ፡ ሌሊቱን ፡ በችግር ፡ አሳልፈዋለሁ ። ጠሚን ፡ ውዬ፡ እንዲሁ ፡ ምናምን ፡ ሳልቀምስ ፡ ባዶ ፡ አንጀቴን ፡ ተቆራምጄ ፡ አድራለሁ።

14 **አዋዜው ፡ በዛና ፡ ምላስክን ፡ ተኰሰው ፡**
**—አነካክቶ ፡ መብላት ፡ አታውቅም ፡ እንደሰው ።**

ሠ ፡ ቀባብቶ ፡ በመጠኑ ፡ ጠቅሶና ፡ አርምዶ ፡ መብላት ፡ አታውቅም ።
ወ ፡ አሾክሹኮ ፡ ነገር ፡ ሠርቶ ፡ ሰውን ፡ አጣልቶ ፡ መኖር ፡ አታውቅም ።

15 **እንዴት ፡ አደርክ ፡ በሉኝ ፡ ቆሜ ፡ ከተገኘሁ ፡**
**—ከነጋማ ፡ ወዲያ ፡ እረግ ፡ እኔም ፡ የለሁ ።** (1) ( ቀኛ . ሰውነቴ ፡)

ሠ ፡ ዛሬውኑ ፡ እንጨዋወት ፡ እንወያይ ፡ እንጂ ፡ ነገማ ፡ እኔ ፡ የለሁም ፡ አልገኝም ።
ወ ፡ ከነገ ፡ ጀምሮ ፡ በዚህ ፡ ዓለም ፡ አልኖርም ፡ ጢት ፡ ሚች ፡ ነኝ ፡ የምታዩኝ ፡ ዛሬ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

16 **እንግዲህ ፡ አላዝንም ፡ ለሰማይ ፡ አሞራ ፡**
**—የገዛ ፡ ሥጋውን ፡ ክንፉን ፡ ለሚበላ ።** (2)

ሠ ፡ አሞራ ፡ እርም ፡ አያውቅም ፡ የገዛ ፡ ክንፉን ፡ ይበላል ፡ አካሉን ፡ ይመገባል።
ወ ፡ አቶ ፡ ክንፉን ፡ በጦር ፡ ሜዳ ፡ ወድቆ ፡ አሞራ ፡ በላው ፡ የሰማይ ፡ አዕዋፍ ፡ ተናጠቀው ።

17 **እንግዲህ ፡ ሰውዬው ፡ ሰብሰብ ፡ ብለህ ፡ ተኛ ፡**
**—ማን ፡ በነገረልን ፡ እንዳለ ፡ ቀበኛ ።**

ሠ ፡ ልብስ ፡ የሚበላ ፡ መኖሩን ፡ ማን ፡ በነገረልን ፡ ቀበኛ ፡ እንዳለ ፡ ተረድተህ ፡ ተጠንቀቅ ።
ወ ፡ የኛ ፡ ነገር ፡ መፈጸሙን ፡ ማን ፡ ባስረዳልን ፡ ዘመድ ፡ ወገን ፡ የሌለን ፡ አሳዛኝ ፡ ፍጥረቶች ፡ ሁነን ፡ ቀርተናል ።

18 **እንግዲህስ ፡ በቃን ፡ አንሰበሰብም ፡ ባፈርሳታ ፡ ሜዳ ፡**
**—በጢት ፡ ቆላ ፡ ሲወርድ ፡ የገደለው ፡ ናዳ ።** (3)

ሠ ፡ የሞተው ፡ በናዳ ፡ ነው ፡ ሰው ፡ አልገደለውም ፡ ደመኛ ፡ የለውም ።
ወ ፡ የገደለው ፡ "ናዳ" የሚባል ፡ ሰው ፡ ነው ፡ ሌላ ፡ ጠላት ፡ የለውም ፡ ባላጋራው ፡ ደመኛው ፡ እሱ ፡ ብቻ ፡ ነው ።

---

(1) በኢጣልያ ፡ ጊዜ ፡ ትገደላለህ ፡ ተብሎ ፡ ተነግሯቸው ፡ ዘመዶቻቸው ፡ ለቅሶ ፡ ሲያደርጉ ፡ ራሳቸው ፡ ያወረዱት ፡ ሙሾ ።

(2) ክንፉ ፡ የሚባለው ፡ በዘመቻ ፡ ላይ ፡ ሞቶ ፡ ሬሳውን ፡ አሞራ ፡ ስለበላው ።

(3) ናዳ ፡ ገደለው ፡ የተባለው ፡ ድንጋይ ፡ ሳይሆን ፡ ሰው ፡ ለማለት ፡ ነው ።
ባገራችን ፡ ባፍርሳታ ፡ አጥፊው ፡ ሲገለጥ ፡ ዎፍ ፡ ነገረች ፡ ይባላል ፡ አንዳንድ ፡ ጊዜም ፡ በፈሊጥ ፡ በዘይቤ ፡ ስሙ ፡ ይጠራል ፡ በምሳሌ ፡ - ባገራችን ፡ ሌባው ፡ ለማ ፡ ቢ.ተው ፡ ይ.ተው ፡ ጀምበር ፡ በሰረቀ ፡ ቍጥር ፡ ስንታመስ ፡ አንኖርም ፡ ተብሏል ፡ በዚህም ፡ አነጋገር ፡ ለማ ፡ ቢ.ተው ፡ ጀምበር ፡ አጥፊዎች ፡ ወይም ፡ ሌቦች ፡ ናቸው ፡ ማለት ፡ ነው ።

19 እስከ ፡ ሐሙስ ፡ ድረስ ፡ ቀን ፡ ቍጥር ፡ አውቃለሁ ፡
ዓርብ ፡ ቀን ፡ ጠፍቶብኝ ፡ ተቸግሬአለሁ ።

ሠ ፡ ከሰኞ ፡ እስከ ፡ ሐሙስ ፡ ያሉትን ፡ ቀናት ፡ ስም ፡ አውቃለሁ ፡ ከዚያ ፡ ቀጥሎ ያለውን ፡ ግን ፡ አላውቀውም ፡

ወ ፡ የልብስ ፡ መሥሪያ ፡ አርቤን ፡ ቀን ፡ በቀን ፡ ሌባ ፡ ሰርቆኝ ፡ ተቸግሬአለሁ ።

ወ ፡ በዓርብ ፡ የፍስክ ፡ መብል ፡ በመብላቴ ፡ አዝናለሁ ፡ እጸጸታለሁ ።

20 እሱን ፡ ሞት ፡ ሲጠራው ፡ በሩቁ ፡ ሰምቼ ፡
እኔም ፡ ወይ ፡ አላልኩም ፡ ለራሴ ፡ ፈርቼ ።

ሠ ፡ ሲጠራ ፡ እየሰማሁ ፡ አቤት ፡ ሳልለው ፡ ቀረሁ ፡ የሚቆጣ ፡ መስሎኝ ፡ ወይ ፡ አላልሁትም ።

ወ ፡ እሱ ፡ ሲሞት ፡ አልረዳሁትም ፡ ዋይ ፡ እንኳ ፡ አላልሁም ፡ ለራሴ ፡ ፈርቼ ፡ ሸሽሁ ።

21 ከእንግዲህስ ፡ ወዲህ ፡ ማንም ፡ ማን ፡ አይረዳን ፡
ከጥንት ፡ አብሮ ፡ አደጌ ፡ ጥላዬ ፡ ሲከዳኝ ።

ሠ ፡ ነባር ፡ ጓደኛዬ ፡ ጥላዬ ፡ ከጠገቤ ፡ ሲጠፋ ፡ ወደፊት ፡ ማን ፡ ጓደኛ ፡ ይሆነኛል ፡ ብዬ ፡ አምናለሁ ።

ወ ፡ አብሮ ፡ አደግ ፡ ወዳጄ ፡ "ጥላዬ" በሞት ፡ ተለየኝ ፡ የሱ ፡ ነገር ፡ አለቀ ፡ በቃ ፡ ተከተተ ።

22 ወይዘሮ ፡ ዓለሚቱ ፡ ድግስ ፡ ደግሰሽ ፡ (ሰሎሞን ፡ የኔ ፡ ነህ ።)
ሁሉም ፡ ማለፊያ ፡ ነው ፡ መናኛም ፡ የለሽ ።

ሠ ፡ ለድግስሽ ፡ የተጋገረው ፡ እንጀራ ፡ ሁሉ ፡ ነጭ ፡ ጤፍ ፡ ነው ፡ ቅይጥ ፡ አልነበረም ።

ወ ፡ በተፈጥሮሽ ፡ እንከን ፡ የሌለሽ ፡ ደስ ፡ የምታሰኝ ፡ ነሽ ።

ወ ፡ ይህ ፡ ዓለም ፡ ኀላፊ ፡ ጠፊ ፡ ነው ፡ የጊዜ ፡ ማስተላለፊያ ፡ እንጂ ፡ ቀዋሚነት ፡ የለውም ፡ ሁሉም ፡ ከንቱ ፡ ነው ።

23 ዓይኔ ፡ ነበር ፡ እንጂ ፡ ኑሮዬ ፡ ያልኩት ፡
እስከዚያ ፡ አንድ ፡ ነው ፡ የምሰነብት ። ( ትልቁ ፡ ራስ ፡ ኀይሉ ፡)

ሠ ፡ ዓይኔ ፡ ከሚባለው ፡ አገር ፡ እስክሄድ ፡ ድረስ ፡ "ነድ" ከሚባለው ፡ ቦታ ፡ እቆያለሁ ፡ ከዚያ ፡ እሰነብታለሁ ።

ወ ፡ (1) ኑሮ ፡ በብርሃን ፡ በዓይን ፡ ነበር ፡ የሚያምረው ።
(2) የኔ ፡ ሕይወት ፡ መቆየት ፡ ለንዶት ፡ ለብስጭት ፡ ነው ፡ ለደስታ ፡ አይደለም ።

24 የትም ፡ እሄዳለሁ ፡ አልቀርም ፡ ዘንድሮ ፡
መልኬ ፡ ከጠፋብኝ ፡ አልፈልግም ፡ ኑሮ ።

ሠ ፡ ሰውነቱ ፡ ከተጐዳ ፡ መልኬ ፡ ከጠፋና ፡ ከተጐሳቆለ ፡ ባገር ፡ አልኖርም ።

ወ ፡ ልጄ ፡ መልኬ ፡ ከሞተብኝ ፡ ዓለምም ፡ አልፈልግ ፡ መንኜ ፡ እሄዳለሁ ።

25 የጐጃሙ ፡ ዶቄት ፡ ኩርኩሮ ፡ ሆነ ፡ አሉ ፡
የዳሞቱ ፡ ዶቄት ፡ ኩርኩር ፡ ሆነ ፡ አሉ ፡
—ራስ ፡ ዓሊ ፡ መጡ ፡ አስልመው ፡ ሊበሉ ። (1)

ሠ ፡ የተገረዳደፈውን ፡ የተከረተሰውን ፡ ዱቄት ፡ አሰልቀው ፡ አስደቁሰው ፡
አስልመው ፡ ለመብላት ፡ ራስ ፡ ዓሊ ፡ መጡ ።

ወ ፡ ራስ ፡ ዓሊ ፡ ጐጃምን ፡ እስላም ፡ አርገው ፡ ለመግዛት ፡ መጡ ፡ ሃይማኖት ፡
ሊያስለውጡ ፡ ነው ።

26 ያብርሃምን ፡ ሱሪ ፡ ሰፊ ፡ አበላሽቶበት ፡
—አባተ ፡ አባይትረፍ ፡ ጉልበቱን ፡ አየበት ። (2)

ሠ ፡ አባተ ፡ የአብርሃምን ፡ ጉልበት ፡ ሱሪው ፡ በማጠሩ ፡ ለማየት ፡ ቻለ ።

ወ ፡ አባተ ፡ አባይትረፍ ፡ (ራስ ፡ አባተ ፡ ቧያለው ፡) ለአብርሃም ፡ ኃይሉን ፡ አሳ
የው ፡ ማንነቱን ፡ አሳወቀው ።

27 ይህን ፡ ወተት ፡ በጋን ፡ ያስቀመጡትን ፡
—ግፋው ፡ ግፋው ፡ አሉኝ ፡ የማልችለውን ።

ሠ ፡ ጋን ፡ ሙሉ ፡ ወተት ፡ ናጥ ፡ እያሉ ፡ የማልችለውን ፡ ያስገድዱኛል ።

ወ ፡ የማልችለውን ፡ ባላጋራ ፡ ተቋቋመው ፡ ታገለው ፡ ይሉኛል ።

28 ደብረ ፡ ሊባኖስን ፡ ማን ፡ ዳኛ ፡ አድርጐታል ፡
—መኳንንቱ ፡ ሁሉ ፡ ይፈጠምበታል ።

ሠ ፡ በርሱ ፡ ዳኝነት ፡ ሰማንያ ፡ ይከነዳሉ ፡ ቀጠሮ ፡ ይወስዳሉ ፡ በስሙ ፡ ይፈጣ
ጠማሉ ።

ወ ፡ መኳንንቱ ፡ ሁሉ ፡ በሞት ፡ አለቁ ፡ በደብረ ፡ ሊባኖስ ፡ የሚቀበሩት ፡ ቁጥ
ራቸው ፡ በረከተ ፡ በጣም ፡ በዙ ።

29 ጃንሆይ ፡ ቢጠይቁህ ፡ ያለ ፡ መስኋቸው ፡
—ቦታውን ፡ ሊፈልግ ፡ ሄደ ፡ በላቸው ። (3) (ነ. ተ. እ. )

ሠ ፡ ቦታውን ፡ መሬቱን ፡ ርስቱን ፡ ለመመርመር ፡ ሄደ ፡ ብለህ ፡ ንገራቸው ።

ወ ፡ በላቸው ፡ ከቀድሞ ፡ ጌታው ፡ ሊቀላቀል ፡ ሄደ ፡ ብለህ ፡ ግለጥላቸው ።

30 ጐጃምና ፡ ዳሞት ፡ አታብዙት ፡ ኩራቱን ፡
—መድኀኒ ፡ ዓለም ፡ ዘምቶ ፡ አላዳነም ፡ ቤቴን ። (4)

---

(1) ትልቁ ፡ ራስ ፡ ዓሊ ፡ ጐጃምን ፡ ሲወሩ ፡ ስማቸው ፡ በተለመደው ፡ በእስላም ፡ ስም ፡ በዓሊ
በመጠራቱ ፡ የተገጠመ ።

(2) ራስ ፡ አባተ ፡ ቧያለው ፡ ከደጃዝማች ፡ አብርሃ ፡ ጋር ፡ አሸንጌ ፡ ላይ ፡ ተዋግተው ፡ ባለጋ
ራቸውን ፡ ድል ፡ ስላደረጉ ፡ የተገጠመ ።

(3) ነጋድራስ ፡ ተሰማ ፡ እሸቴ ፡ ቦታቸው ፡ በላቸው ፡ እርገጤ ፡ ለሚባል ፡ ሰው ፡ ተሰጥቶባ
ቸው ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ በርሱ ፡ መክዳት ፡ ምክንያት ፡ ርስታቸው ፡ እንዲለቀቅላቸው ፡ ያሳ
ሰቡበት ።

(4) ካጼ ፡ ዮሐንስ ፡ ጋራ ፡ የዘመተው ፡ የመድኃኔ ፡ ዓለም ፡ ታቦት ፡ የነበረበት ፡ ቤተ ፡ ክርስ
ቲያን ፡ ስለተቃጠለ ፡ የተገጠመ ።

ሠ ፡ የዘማቹ ፡ ቤት ፡ ተዘረፈ ፡ ተበዘበዘ ፡ ከቀማኛ ፡ አልዳነም ።
ወ ፡ ከንጉሡ ፡ ጋር ፡ የዘመተው ፡ የመድኃኔ ፡ ዓለም ፡ ታቦት ፡ ያለበት ፡ ቤተ ፡ ክርስቲያን ፡ ተቃጠለ ።

31 ጐጃም ፡ ተቃጠለ ፡ ዓባይ ፡ እስከ ፡ ዓባይ ፡
—ትግሬ ፡ ቅጠል ፡ ይዞ ፡ ሊያጠፋው ፡ ነወይ ። (1)

ሠ ፡ ጐጃም ፡ በእሳት ፡ ሲቃጠል ፡ ትግሬ ፡ ቅጠል ፡ ይዞ ፡ ለማዳን ፡ ይችላልን ።
ወ ፡ ትግሬ ፡ የጐጃምን ፡ አዝመራ ፡ በቡቃያነቱ ፡ ደርሶበት ፡ ሊያጠፋው ፡ ነው ። ለበቅሎ ፡ ለፈረሱ ፡ ምግብ ፡ ሊያደርገው ፡ ነው ፡ ሕዝቡን ፡ ምግብ ፡ አሳጥቶ ፡ ሊጐዳው ፡ ነው ።

32 ጓደኛ ፡ ሳይኖረኝ ፡ የማጫወተው ፡
—ምሥጢሬ ፡ ተሰማ ፡ እሆዴ ፡ ያለው ።

ሠ ፡ ለሰው ፡ ሳላካፍለው ፡ ለጓደኛ ፡ ሳልነግረው ፡ እሆዴ ፡ ያለውን ፡ ምሥጢር ፡ እውጭ ፡ ሰማሁት ፡ ከሰው ፡ አፍ ፡ አገኘሁት ።
ወ ፡ ምሥጢር ፡ ቻይው ፡ ቁም ፡ ነገረኛው ፡ ወዳጄ ፡ ተሰማ ፡ ነው ።

33 ጠላት ፡ እርስዎንስ ፡ ምንም ፡ አይደፍርዎ ፡
—የሚያስፈራው ፡ ሠይፉ ፡ እያለ ፡ በጅዎ ። (ጌታቸው ፡ አወቀ ፡)

ሠ ፡ እርስዎን ፡ ጠላቶ አይደፍርዎትም ፡ ባላጋራ ፡ አያስጋዎትም ፡ በጅዎ ፡ ሠይፍ ፡ ይዘዋል ፡ መከላከያ ፡ አለዎት ።
ወ ፡ "ሠይፉን" የመሰለ ፡ የበቃ ፡ የነቃ ፡ የሚያኰራ ፡ ልጅ ፡ አለዎ ፡ ምንም ፡ አይፈሩም ።

34 ጨጓራና ፡ ጉበት ፡ አትጠይቁን ፡
—በግም ፡ አላረድን ፡ ድሎትም ፡ የለን ።

ሠ ፡ በግ ፡ አልታረደም ፡ ጨጓራና ፡ ጉበት ፡ የለንም ፡ ድሎት ፡ አልተዘጋጀም ።
ወ ፡ ወንጀል ፡ አልሠራንም ፡ ሴራ ፡ አላደረግንም ፡ አልዶለትንም ።

35 ፈጥነህ ፡ አትኸድም ፡ ወይ ፡ ጌታህ ፡ ሲጠራህ ፡
—እንደነ ፡ ራስ ፡ ወሌ ፡ ነጋሪት ፡ የለህ ።

ሠ ፡ እንደባለ ፡ ነጋሪቶቹ ፡ እንደነራስ ፡ ወሌ ፡ እየተጀነንህ ፡ እየተንጓደድህ ፡ መሄዱን ፡ ትተህ ፡ ጌታህ ፡ ሲጠሩህ ፡ አትሮጥም ።
ወ ፡ አንተ ፡ እንደነ ፡ ራስ ፡ ወሌ ፡ ለንጉሡ ፡ የሚያስታውስ ፡ እቴጌ ፡ እህት ፡ የለህም ፡ ሥራህን ፡ ለበላይ ፡ የሚነግርልህ ፡ ዘመድ ፡ ያጣህ ፡ ነህ ።

---

(1) አጼ ፡ ዮሐንስ ፡ ጐጃምን ፡ የወረሩት ፡ በክረምት ፡ ወር ፡ ስለ ፡ ነበረ ፡ ሠራዊቱ ፡ ቡቃያውን ፡ ስላጠፋው ፡ የተገጠመ ።

# የፍቅር ፡ ዘፈን ።

1 ለምን ፡ ትሄጃለሽ ፡ ሁልጊዜ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡
ሁለት ፡ ዓይን ፡ ሳለሽ ፡ ጐዳናውን ፡ የሚያይ ።

ሠ ፡ እያየሽ ፡ አትሄጅምን ፡ ለምን ፡ መንገድ ፡ እያለ ፡ በሰው ፡ ላይ ፡ ትራመጃ ለሽ ፡ አትመለከችምን ።

ወ ፡ ከባልሽ ፡ በቀር ፡ ሁልጊዜ ፡ ሌላ ፡ ለምን ፡ ትፈልጊአለሽ ፡ ባንድ ፡ ወንድ ፡ ተወስነሽ ፡ አትኖሪምን ።

2 ሌላ ፡ ጉዳይ ፡ ኖሮኝ ፡ አልመጣሁም ፡ ከሰው ፡
ዋጋየን ፡ ብዬ ፡ ነው ፡ የምመላለሰው ።

ሠ ፡ እኔ ፡ አሁንም ፡ አሁንም ፡ የምመጣው ፡ ዕቃ ፡ የሸጥሁበትን ፡ ዋጋ ፡ ለመ ቀበል ፡ ነው ፡ ሰው ፡ ፍለጋ ፡ አይደለም ፡ ሌላም ፡ ጉዳይ ፡ የለኝም ።

ወ ፡ እኔ ፡ እግሬ ፡ እስኪቀጥን ፡ እንደዚህ ፡ የምመላለሰው ፡ ወዳጄን ፡ ወይዘሮ ፡ "ዋጋዬን" ለማግኘትና ፡ ለመነጋገር ፡ ነው ።

3 መልኩን ፡ አላውቀውም ፡ ስለምን ፡ ነው ፡ ያልሽው ፡
ዝንጀሮው ፡ በፊትሽ ፡ ተቀምጦ ፡ እያየሽው ።

ሠ ፡ ዝንጀሮ ፡ የሚባለው ፡ አውሬ ፡ ይኸ ፡ ከፊትሽ ፡ ያለው ፡ ነው ፡ ይህ ፡ የምታ ይው ፡ እንስሳ ፡ ዝንጀሮ ፡ የሚባለው ፡ ነው ።

ወ ፡ የዝንጀሮ ፡ መልክ ፡ ካንቺ ፡ ፊት ፡ በምንም ፡ ነገር ፡ አያሳስትም ፡ አንድ ፡ ናችሁ ፡ አንቺ ፡ ራስሽ ፡ ዝንጀሮ ፡ ነሽ ፡ አንችን ፡ ያየ ፡ ዝንጀሮ ፡ አይጠፋ ውም ።

4 በጧት ፡ ተነስቼ ፡ እወርዳለሁ ፡ ከሰም ፡
ያሳማት ፡ ያሳማት ፡ ያሳማት ፡ እያሉኝ ፡ ነድጃለሁ ፡ በጣም ።

ሠ ፡ በከሰም ፡ ወንዝ ፡ ዓሣ ፡ በብዛት ፡ ይገኛል ፡ ሞልቷል ፡ ተርፏል ፡ ብለውኝ ፡ ወርጄ ፡ ለማጥመድ ፡ ቸኩያለሁ ።

ወ ፡ ያ ፡ ሰው ፡ ለምዷታል ፡ ወዷታል ፡ አብሯት ፡ ይውላል ፡ ብለው ፡ ነድጃለሁ

5 ባልበላውም ፡ እንኳ ፡ እንዲያው ፡ በዓይኔ ፡ ልየው ፡
ይምጣልኝ ፡ እሸቱ ፡ መዳኒቴ ፡ እሱ ፡ ነው ።

ሠ ፡ እሸት ፡ አምጡልኝ ፡ በጣም ፡ አምሮኛል ፡ እሱን ፡ ባገኝ ፡ የምድን ፡ ይመስ ለኛል ።

ወ ፡ ከየትም ፡ ፈልጋችሁ ፡ አቶ ፡ "እሸቱን" አምጡልኝ ፡ ቀልቤ ፡ አርፎበታል፡ ወድጀዋለሁ ፡ ይናፍቀኛል ።

6 ብዙ ፡ የተዋበው ፡ እያለ ፡ እልፍኝሽ ፡
በምን ፡ ምክንያት ፡ ነው ፡ አዳራሽ ፡ የሆንሽ ።

ሠ ፡ እልፍኝሽ ፡ እያለ ፡ ለምን ፡ አደራሽ ፡ ተቀመጥሽ ? ለምን ፡ ከሰው ፡ ፊት ፡ ሰግደድ ፡ አላልሽም ፡ ሁሉ ፡ ካለበት ፡ ከአዳራሽ ፡ ሆንሽ ።

ወ ፡ በዘር ፡ በልደት ፡ ትልቅ ፡ ስትሆኚ ፡ ለምን ፡ ከአልባሌ ፡ ሰው ፡ ጋር ፡ ትው ያለሽ ፡ ከትንሽ ፡ ከትልቁ ፡ ላይ ፡ ትንጠለጠያለሽ ፡ ክብርሽን ፡ አትጠብ ቂም ?

7　አልሜሽ ፡ ሰልቄሽ ፡ ጥንጣን ፡ አድርጌሽ ፡
—እንዴት ፡ ያል ፡ መካሪ ፡ አከረተፈሽ ።

ሠ ፡ መክሬ ፡ ካገረምሁሽ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ ነካሽና ፡ እንደገና ፡ ጥሬ ፡ ሆንሽ ? ከበ ረድሽ ፡ በኋላ ፡ ምን ፡ አስቆጣሽ ።

ወ ፡ እየረገጥሁ ፡ ካሰለጠንኩሽ ፡ በኋላ ፡ አንድ ፡ ብለሽ ፡ የደነቆርሽው ፡ ባህር ይሽ ፡ የተለወጠው ፡ ከቶ ፡ ምን ፡ አግኝቶሽ ፡ ምንስ ፡ ተጠግቶሽ ፡ ይሆን ?

8　ነጠላ ፡ ነው ፡ ልብሴ ፡ አገር ፡ ጠይቁብኝ ፡
—ይበርደዋል ፡ ብለሽ ፡ እንዳትደርቢብኝ ።

ሠ ፡ ነጠላም ፡ ብለብስ ፡ አይበርደኝምና ፡ መደረቢያ ፡ አልሻም ፡ እንዳታክይ ብኝ ፡ የለበስሁት ፡ ይበቃል ።

ወ ፡ በኔ ፡ ላይ ፡ ሌላ ፡ ወዳጅ ፡ እንዳትይዢ ፡ አስጠነቅቅሻለሁ ፡ ፍቅርሽን ፡ እንዳ ታጋሪብኝ ፡ አደራ ።

# ማረሚያ

በገጽ፡ 234 ዘለሰኛ፡ ቁጥር. 858 - ስለንጉሥ፡ ተክለ፡ ሃይማኖት፡ የተደረሰው፡ ሲተረጐም - ለአርባ፡ አንድ፡ በቀረው፡ በ39 ዓመታቸው፡ ሞቱ፡ የተባለው፡ የግጥሙን፡ ስሜት፡ በመመልከት፡ ብቻ፡ ነው። ያረፉት ግን፡ በ55 ዓመታቸው፡ እንደሆነ፡ ሊታወቅ፡ ተችሏል።

ከባላምባራስ ፡ ማኅተመ ፡ ሥላሴ ፡ ወልደ ፡ መስቀል ፡
የተዘጋጁ ፡ መጽሐፎች ።

፩ ፡ ዝክረ ፡ ነገር ፡

፪ ፡ ዕጹብ ፡ ድንቅ ፡

፫ ፡ ያባቶች ፡ ቅርስ ፡
(አንደኛ ፡ እትም ፡
(ሁለተኛ ፡ እትም ፡

፬ ፡ ጥበበ ፡ ገራህት ፡

፭ ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡
(አንደኛ ፡ እትም ፡
(ሁለተኛ ፡ እትም ፡
(ሦስተኛ ፡ እትም ፡

፮ ፡ እንቅልፍ ፡ ለምኔ ፡
(አንደኛ ፡ እትም ፡
(ሁለተኛ ፡ እትም ፡

፯ ፡ ስለ ፡ ኢትዮጵያ ፡ የመሬት ፡ ሥሪት ፡ አስተዳደር ፡ ግብር ፡

፰ ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ከነመፍቻው ፡

፱ ፡ አማርኛ ፡ ቅኔ ፡ ከነመፍቻው ፡ ተሻሽሎ ፡ የወጣ ፡

፲ ፡ ስም ፡ ከመቃብር ፡ በላይ ፡

፲፩ ፡ የእኛም ፡ አሉ ፡ እንወቃቸው ።

፲፪ ፡ ብዕለ ፡ ገራህት ፡ (በመዘጋጀት ፡ ላይ ፡ ያለ)

በብርሃንና ሰላም ማተሚያ ቤት ታተመ